ዛሬ ያለው ውጊያ እምነቱን ባልያዘው ትንሽ እውቀት ላይ ባደረገ ውል ባጣ መሰረቱን በማያውቅ፣ ቢያውቅም በናቀ፣ ከነጭ የተቀበለውን ባህል፣ እምነት፣ የቁስ እድገት፣ እውቀት፣ እንደ አምላክ የሚያይና የሚያመልክ የጠፋ ትውልድ ጋር የሚካሄድ ትግል ሆኖአል፡፡

ዲያብሎስ ይህንን የጨለመበት ትውልድ በአመራርም በሃብትም በኃይልም እንዲደራጅ ጥሯል፡፡ መንግስት በራሱ የዲያብሎስ መሳሪያ ሆኖ ይህን የጠፋ ትውልድ ፍፁም እንዲጠፋ ያደርጋል፡፡ እያደረገም ይገኛል፡፡ በኢትዮጵያ ተዋህዶ እምነት ላይ ያለው ውጊያ በመልእክት 2 እንደተጠቀሰው እምነት አለን በሚሉ ብቻ የሚሰነዘር አይደለም ፤ እምነቱ በሌላቸው በመንግስት፣ በውጪ መንግስታት፣ አለም አቀፍ ድርጅቶች፣ ባለሃብቶች ጭምር እንጂ፡፡ ሁሉም ይህቺን እምነት ለማጥፋት እስከ አሁን ይሰራሉ፡፡ እየሰሩም ይገኛሉ፡፡ ሁሉን ለመዘርዘር ሰፊ ቦታ ይፈጃል፡ ፡ በጠቅላላ በእምነት ውጊያው ካቶሊክ፣ ፕሮቴስታነት፣ እስላም፣ ጀቫ፣ ሌሎችም ሁሉ በቅንብር በተዋህዶ ኦርቶዶክስ እምነት ላይ የዘመቱ ናቸው፡፡ ሁሉም ዘማቾች ከውጭ በሚደረግላቸው ቀጥታ የገንዘብና የስልት የቁሳቁስ ድጋፍ የታጠቁ ናቸው፡፡ በመሆኑም ፍርዳቸው ቀድሞ ወጣ፡፡ አሁን ስለ አፈፃፀሙ በጽሑፍ መጨረሻ እናየዋለን ፡፡

በኢኮኖሚ፣ በባህል የተደረገ ውግያ ከራሱ ከእምነቱ የማያንስ ነው፡፡ ድሃ እንድንሆን እንድንራብ እንድንበታተን ከራስ ባህል ይልቅ በምንዝርና፣ በውሸት በእርስ በእርስ መፈጀት እንድናልቅ፣ በሽታ እንድንረግፍ፣ ባለን ሃብት እንዳንጠቀም፣ በማድረግ ልማታችን ወደ ጥፋት በማዞር እስከ አሁን ሲሰራበት ኖሯል፡፡ በኢትጵያ ላይ በተደረገ ዘረፋ ብዙ ዘመቻ በጥቂት ግንባር ቀደም የምዕራብ፣ የአረብ፣ አገሮች በመመራት ሁሉም አለም የየበኩሉን ድንጋይ አቀብሏል፣ ወርውሯል ዛሬ ይከፍልበታል፡፡

እንደ መንግስት ማዳከም መንግስትን የራስ ጥገኛ ማድረግ፣ በተዋህዶ እምነታችን መሐል ተኩላ በውስጧ በመሰግሰግ ማዳከም፣ መበተን የተደረገ፤ እየተደረገ ያለ ግልፅ ተግባር ነው፡፡

ወገኖቼ በብርሃን ስለምንተያይ በሰፊው ያኔ እንነጋገርበትለን፡፡ በኢትዮጵያ አፈፃፀሙ ምን ይሆናል፡፡ በዚች አገር ያሉ ሁሉ ደግም ደጋግሞ እንዲያስተውል ተመክሯል ተዘክሯል፡፡

አሁን የወቀሳ፣ የመምከሪያ፣ የማስጠንቀቂያ ጊዜ ተጠናቋል፡፡ ፍርዱ ወደ ፍፃሜ ተሸጋግሯል፡፡ ስለዚህ በልዑል ያልተመዘገበ ፣ ለምህረት ያልተጻፈ፣ ከነ ድንጋይ ልቡ እያፌዘ ያለ፣ በዚህ አፈፃፀም ፍፁም ይጠረጋል እንጂ አያመልጥም፡፡

በምንዝርና የተነከረ፣ ከንስሐ ያልደረሰ፣ በትእቢት የጸና በጠመንጃው፣ በሃብቱ፣ በጉልበቱ የሚመካ፣ ውጪ ባለ ወገኑ የተኩራራ፣ በድሃ ያላገጠ፣ የድሃ ንብረት፣ሚስት የቀማ፣ ጓደኛውን የካደ፣ በውሸት የበለፀገ፣ አገርን የካደ ፣ ተዋህዶን ለማጥፋት የደከመ፣ ንብረቷን የዘረፈ፣ ምእመኑን ለተኩላ የበተነ፣ ለበእድ እምነትና መንግስት የሰለለ ዋጋም የተቀበለ፣ ምንዝርናን ስራው ያደረገ፣ ንጹሃንን ያሰገደለ፣ የገደለ፣ የእግዚአብሄር አገልጋዮችን የተዋህዶ ኦርቶዶክስ እምነት አገልጋዮችን ያሳደደ፣ ያሰረ፣ ያሰቃየ፣ በኢትዮጵያ ምድር የምህረትን ዘመን ያለ ቅጣት ያለ ዋጋ መክፈል ፈጽሞ አያይም፡፡ የሚያየውም ንስሃ የገባውና የተጸጸተው በመጠነኛ ቅጣት የታለፈው ብቻ ይሆናል፡፡ በኢትዮጵያ ምድር ምንዝርናን በማስፋፋት ሴቶች እጅግ ከፍተዋል፣ ሱሪ ለባሽ ገላዋን ገላጭ፣ በፍጹም የማትመለስ ነውረኛ ሴት ሁሉ በላያቸው ላይ የሚጠርጋቸው እሳት ወጥቷል፡፡

በኢትዮጵያ ከአንዲቷ ከተዋህዶ እምነት ውጪ ሌላ አይረግጥም፣ አይኖርባትም፣ አይጠለልባትም፡፡ ከዚህ አፈጻፀም መውጣት በኋላ በኢትዮጵያ በግልም፣ በመንግስትም፣ በኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤ/ክርስቲያንም ፣ በመንግስት ተቋማትም ስለሚወሰዱት አቋምና እርምጃዎች በቀጣዮች የድርጊት መመሪያዎች ይገለጻሉ፡፡

መላው አገሬ የኢትዮጵያ ልጆች፣ የተዋህዶ እምነት ልጆች፣ የድንግል ልጆች፣ የገብርኤል የሚካኤል አንበሶች፣ የኡራኤል፣ የሩፋኤል አርበኞች፣ ባጠቃላይ ቅን የዋህ የሆንከው ኢትዮጵያዊ በሙሉ፣ ባለህበት ፀንተህ ቁም ! ቅድስናህን ጠብቅ ! አትደንግጥ፣ አትፍራ እራስህን ለፈጣሪ ስጥ፣ ለታላቅ አገልግሎት እራስህን አዘጋጅ ! እስከዛሬ ከሰራኸው ጥፋት በምህረቱ ሽሮ በቸርነቱ ያሰራህን፣ የኢትዮጵያ አምላክ አስብ፣ አመስግን፡፡ ዝርዝር መመሪያዎችን በጥንቃቄ አንብብ፣ አስተውለህም አድርግ፡፡ እግዚአብሄር ለክብሩ መር ጦሃልና እራስህን በቅድስናና በትህትና አንጽ፣ ከክፋትም ሁሉ ራቅ፡፡

**14-1 ደቡብ አፍሪካ፡-**

ይህ ክልል ደቡብ አፍሪካን፣ ናሚቢያን፣ ዚምባብዌን፣ ሞዛንቢክ፣ ማደጋስካር፣ ሌሴቶ፣ ማላዊ፣ ቦትስዋና፣ ሞሪሺየስ፣ ኮሞሮስን ይይዛል፡፡ ይህ ክልል እጅግ የተጎዳ የቅኝ ተገዢ ነው፡፡ በተለይ በዚህ አገዛዟ መጥፎነት የምትታወቀው እንግሊዝ እስከዛሬ የምትጫነው ክልል ነው፡፡

ሕዝቡ የጌቶቹን እምነት የወረሰ ነው፡፡ በደቡብ አፍሪካ፣ በሞዛምቢክ፣ በዚምባብዌ፣ በናሚብያ ዛሬም ጥቁሩን እየገዙ እየዘረፉ ያሉት ነጮች እዚያው እንደሰፈሩ ናቸው፡፡ ስለዚህ ይህ ክልል እንደ አውሮፓዎች የሚመዘን ነው፡ ፡ በዚህ ክልል ምንዝርናው እጅግ የከፋ ነው፡፡ ብዙ እምነቶች አሉ፡- ካቶሊክ፣ አንጀሊካን፣ ፕሮቴስታንት፣ ሙስሊም፣ በስብጥረ ያለበት ነው፡፡

የተሰባጠረ ቅጣት ይጠብቃቸዋል፡፡ በእሳትም ይፈተሻሉ የማያቋርጥ እሳት ይበረብራቸዋል፡፡ ለሁሉም ዓለም እንደሚሆነው እነዚህም ጥቂት የሚተርፍ ስለሚኖራቸው፤ በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ስር ሲጠለሉ በኢትዮጵያ የሚሰፍነውን ብርሃናዊ አገዛዝ ሲቀበሉ ብቻ ሰላማቸው ይመለስላቸዋል፡፡ ከዚህ ውጪ የመፈጠር መፍትሄም ሆነ ዘዴ አያገኙም፡፡ አይኖርምም፡፡

አሞፅ 2 ፡ 14 - 16

በውስጥ ገፅ የተዘረዘሩት የመካከለኛው ምስራቅ አገሮች ሸክም እጅግ ከባድ ከብዙ ጥፋትና ውድመት በኋላ ነው ለተዋህዶ ኦርቶዶክስ /ለኢትዮጵያ/ አገዛዝ እጃቸውን የሚሰጡት መሰረታቸው ፍፁም ዲያቢሎሳዊ በመሆኑ እሳቱ እየወረደባቸው ጥቂት እስከሚቀሩ የማይመለሱ ናቸው፡፡

15 አውሮፓ፡- ይህ አህጉር አውሮፓ ሲሆን በዋናነት እነ እንግሊዝ፣ ጀርመንን፣ ፈረንሳይን፣ ስፔንን፣ ዴንማርክን፣ ጣሊያንን፣ ፖርቱጋልንና ሆላንድን ያቀፈ ሲሆን በቅርቡ ከራሽያ ተገንጥለው ወደሱ የገቡት እንደ ፖላንድ፣ ቼክ፣ ላቲቪያ፣ እስቶኒያ፣ ክሮሽያ፣ ቡልጋሪያ፣ ሩማንያ፣ ሃንጋሪን፣ የሰበሰበ የአውሮፓ ህብረት የሚባል ድርጅት ያለ ሲሆን ኔቶ ከአሜሪካ ጋራ ተጣምሮ አለምን ለመግዛት የሚጥሩና እየገዙም ናቸው፡፡

ጀርመን፣ ፈረንሳይ፣ ስፔይን፣ ኦስትርያ፣ እንግሊዝ፣ ሆላንድ፣ ጣሊያንና ፖርቹጋል እነዚህ አገሮች ፍጹም የጥፋት አገሮች ናቸው፡፡ በውስጣቸው ሁሉም የእምነት አይነት አለ፣ ከተዋህዶ እምነት በስተቀር፣ የምንዝርና ቁንጮ ናቸው፣ የክህደት አገር ነው፡፡ በኑሮአቸው ምቾት፣ ባላቸው የኢንዱስትሪና የፍልስፍና አካሄድ እጅግ የሚመጻደቁ ናቸው፡፡ ከእንግሊዝ ቀጥሎ አለምን በቅኝ በመግዛት በሰው ዘር ደም የተጨማለቁ ናቸው፡፡ ሰውን አሽከራቸው ሃብቱን ንብረታቸው አድርገው ዘምተው ለረጅም አመቶች ደሃን የፈጁ ናቸው፡፡ በእነሱ ውስጥ ያሉት ካቶሊክ አንጀሊካንና ፕሮቴስታንት እምነቶች ከመንግስታቸው ጋር እኩል ለሰው ጥፋት የዘመቱ ናቸው፡፡ ከእንግሊዝ አንገሊካን እንደ መንግስት ሆና የመራችም ነች፡፡

አውሮፓ ፍጹም የአለም የጥፋቷ ቁንጮ ነው፡፡ በአውሮፓ ተፈልጎ የሚገኝ አንድም ለምህረት የሚበቃ ነገር የለም፤ በሓዋርያት ደም የታጠበች፣ በብዙ ክርስቲያኖች ሕይወት ያላገጠች የዲያቢሎስ የጥንት ማዘዣ የዛሬው ከአሜሪካን ቀጥሎ ሁለተኛ ማዘዣ ጣቢያ ናት፡፡

የሚጠብቃት፡-

- አውሮፓ እንደ አህጉርም ሆነ በውስጧ እንዳቀፈቻቸው አገሮች በሙሉ በአንድ ሚዛን ትሰፈራለች
- በዚህ ክልል የአውሮፓ ህብረት አባል የሆኑ 28 የሚጠጉ አገሮች በሙሉ በልዑል የእሳት ማዕበል የሚጠረጉ ናቸው፡፡
- ከዚህ ክልል የሚተርፉ ቢኖሩ እጅግ ጥቂት ናቸው እንደ አገር ቀርቶ እንደ መንደር መቆም የማይችሉ ናቸው፡፡
- የሰበሰቡት መሳሪያ የራሳቸው መጥፊያ ይሆናል፡፡
- የአውሬ መርቢያ ይሆናል፡፡ ዛሬ እንረዳለን ባዮች ነገ እርዱን የሚሉ ይሆናሉ ከነዚህም የሚተርፍ የታደለ ነው፡፡ ከሚመጣውና ከሚፈሰው የልዑል ቁጣ ከተረፉት መዳን የሚቻለው በአንድ መንገድ ብቻ ነው፡፡ ለኢ. ተ. ኦርቶዶክስ እጅ መስጠት በእምነቱ በአስተዳደሩ እንደ መንግስትም እንደ ቡድንም እንደ ግለሰብም በኢትዮጵያ ለሚቆመው ብርሃናዊ መንፈሳዊ የልዑል አገዛዝ ፍጹም እጅ መስጠት ብቻ ነው፡፡ እጅም ቢሰጡ ከልዑል ሲጸናና መታዘዙ ከልብ መሆኑ በልዑል ሲረጋገጥ ነው፡፡
  ከውስጣችሁ ለሰው የሚጠቅም ሲቀር ማናቸውም ለጥፋት ሌላውን ለመግዛት ተፈጥሮን ለመጉዳት ለስግብግብነት ባጠቃላይ ለሰው ዘር ሰላምና ጤና ለምድሪቱም ጤና እንቅፋት የሆነው ሥራችሁ ሁሉ ከመሰረቱ ተጠርጎ ይጠፋል፡፡

የዳዊት መዝሙር፡ 13 / 14 / 2 – 8

**15-1 እንግሊዝ፡-**

ይህች ሃገር የአውሮፓ ቀዳሚ መሪ ናት የዚች አገር ወንጀል እና የሃጥያት ጥፋት ከአሜሪካ በምንም መልኩ የማይለይና በማናቸውም ታሪኳም ሆነ ስራዋ ከባቢሎን የምትመሳሰልና ጠበቃ በመሆኗ ከዚህ በተጨማሪ የክህደት ፈላስፎች የፈለቁባት የእምነታችን ጠላቶች በትልቅ ደረጃ የተሰፋፉባት ለአሜሪካ ልጆቿ እዚህ መድረስ ዋናዋ እሷ ናት፡፡ እንግሊዝ አለምን በቅኝ የገዛች የጥፋትን ስራ በሁሉም መልኩ ለአለም ያስተማረችና የመራች መሰረት ያስጨበጠች ናት፡፡ የዚች አገር እጣ ፈንታ በምንም መልኩ ከአሜሪካ እጣ ፈንታ አይለይም፡፡

**15-2 ፈረንሳይ፡-**

ይህች አገር ከእንግሊዝ ጋር ተመሳሳይ ታሪክ ያላት በአለም ቅኝ ገዥነት ከእንግሊዝ ጋር እኩል ትራመድ የነበረች ናት፡፡ ከአምስቱ ሃያላን አንዷ ናት፡፡ የኔቶ ቁልፍ አባል፣ የአውሮፓ ህብረት መስራች ናት፡፡ ፈረንሳይ በአገሬ ጉዳይ ጣልቃ የገባች ናት፡፡ አገሬን ወደብ አልባ ካደረጉ አገሮች የቅርቡ ተጨባጭ ጠላት ናት፡፡ ጅቡቲን የጦር ስፍራና መናኸሪያ ያደረገችም ናት፡፡

ለሷ የሚደርሰው ጥፋት እጅግ ብርቱ ነው፡፡ የሰበሰበችው ሃብት ይጠፋል፡፡ ያከማቸችው የጦር መሳሪያ ኒዩክለር፣ ኬሚካል፣ ባዮሎጂካል፣ ሚሳየል፣ ጀት፣ የጦር መርከብ፣ ሰበ መሪን ሁሉም እንደ ጢስ ይተናል፡፡ ዜጎቿ በሙሉ በእሳት ይበጠራሉ፡፡ አጥቶ መንከራተትን መራብን ያዩታል፡፡ ለነዚህ መንግስት ብርቱ ቅጣት ሳያቋርጥ ይወርድበታል፡፡ እናንተ በኢትዮጵያ ዛሬም እየሰራችሁት ላላችሁት በደል ለፍርድ ትቀርባላችሁ ቶሎ ምህረት ስለጠየቃችሁም አታገኙም፡፡

ሚኪያስ 2 ፡ 1 – 3

ጣሊያን ትናንት ቅኝ ሊገዛ መጣ ዛሬ የለም፡፡ እናንተ ግን ጉልበተኞች ብዙም ሳይርቅ ጅቡቲን ከእናት ምድር ነጥላችሁ ነፃ ናት አላችሁ፡፡ ጦር ሰፈር አደረጃችሁ፡፡ መቀበሪያችሁ ትሆናለች፡፡ አገራችሁ የሰውን አገር እንደበተነች ትበታተናለች፡፡ እናንተ በኢትዮጵያ ፊት አለፍርድ አትታለፉም ትቢያ ትለብሳላችሁ፡፡ በአውሮፓ ላሉ አገሮች የከፋ የጥፋት ምሳሌ ትሆናላችሁ፡፡

በመላው አለም ላለህ የሰው ዘር በሙሉ ልብ ብለህ አድምጥ ልትወስደው የሚገባህ እርምጃ ምንድን ነው፡፡

በዚህ የልዑል ውሳኔ ውስጥ የሁሉንም መልእክቶች በሚገባ የተረዳህ ከሆንክ ከዚህ በታች ያሉትን እንደመጀመሪያው ሁሉ ከዚህም በኋላ ያሉትን የአፈጻጸም ውሳኔዎች አስተውለህ ተረዳ አድርግም፡፡
ይህ መልእክት መላውን አለም የምታይበት የእምነት መነጽርህ ነው፡፡ ከራስህ አትለየው የሚፈጸመውን የልዑል ውሳኔ አስፈጻሚዎች ሲያከናውኑት ልብ ብለህ አስተውል፡፡ በምድር ሆነ በህዋ፣ በባህርም ውስጥ ሁሉ ሁኑ ይህ የልዑል መልእክት የማይዳኘው አለም የለምና ፍርዱን እዩ፡፡ ሁሉም የአለም መሪ፣ ሁሉም የአለም ህዝብ፣ ሁሉም ባለጸጋ፣ ሁሉም ድሃ በብርሃናዊ ፍርድ ይዳኛልና፡፡ ልብ ብለህ አድምጥ፡፡ እምነት የሌለህ ጠማማ ትውልድ እስከምትጠረግ ጠብቅ፡፡

**16 የምትወስደው እርምጃ እንደ ግለሰብ** መዝ ዳዊት 18 / 19 / 8 – 9

*ሀ/ ማንኛውም የሰው ዘር ይህንን መልእክት 1ኛውን 2ኛውን መልእክት ይህንንም 3ኛ የአፈጻጸም ውሳኔ ማንበብ መረዳት፣ ማስረዳት እንደ ወሳኝ መመሪያ መጨበጥ ለሌላውም ማስጨበጥ ከፈጣሪ የተሰጠን ግዴታ ነው፡፡*
*ለ/ ማንኛውም ሰው በኢትዮጵያ ተ/ ኦርቶዶክስ እምነት እንዲጸና እንዲጠለል አምኖ ተጠምቆ እንዲሰበሰብ በፈጣሪ ታዟልና፡፡ አንተም ይህን አድርግ ያመንክ ቀድሞውንም በእምነቱ ካለህ ማናቸውንም የፈጣሪ ትእዛዝ ጠብቅ ከቅድስናህ አትጉደል !!*
*ሐ/ ከኢትዮጵያ ውጪ ያለህ ማንኛውም በልብህ ያመንክ በህሊናህ የተለወጥክ ሰው በሙሉ ባለህበት የትኛውም የአለም ማዕዘን በጎጆህ /በቤትህ/ ሆነህ ወደ ፈጣሪ መመለስህን፣ መጸጸትህን፣ በእውነት ለተዋህዶ እምነት መቆምህን ለፈጣሪ በጾም በጸሎት ንገር፡፡ ቀጥሎም ማናቸውንም ኢትዮጵያዊ የእምነቱ ሰው ለማግኘት ጣር፡፡*
ዳዊት መዝ 23 / 24 / 3 – 5

በተዘረጉ የመረጃ መረቦች ለማግኘት ሞክር፣ በአገርህ ካለው የኢትዮጵያ ኤምባሲም መረጃ ጠይቅ ከዚህ ከኢትዮጵያ የሚያገናኝህን አድራሻም ጠይቀህ ሁሉንም አግኝተህ ተመለስ፡፡ በነጠላ ቢያቅትህ በህብረት አቅምህን አስተባብረህ መምጣትና የእምነቱን ስርአት ፈጽመህ ሕጉን አውቀህ መመሪያ ተቀብለህ መሄድ ትችላለህ፡፡ በልቡ ለተለወጠ ሰው መንገዱ ክፍት ነውና፡፡
*መ/ ማንኛውም ኢትዮጵያዊ በየትኛውም አለም ያለ ሁሉ መልእክቱን ለማግኘት የሚፈልጉ ሰዎችን መርዳት ግዴታው ነው፡፡ ከብርቱ ቅጣት መፍሰስ ጀምሮ ሰዎች ለመዳን ይጥራሉና ! ማምለጫውን ማሳየት ግዴታው ነው፡፡ በዚህም ለመነገድ የሚሞክር ይቀጣበታልና አገልግሎቱን በነጻ ይስጥ፡፡*
*ውሳኔው ወደ አፈጻጸም ተሻግሯልና ያልጠበቅናቸው አገሮች ሕዝቦች የሚጠፉ ሲጠፉ የሚተርፉ ምህረት ሲሹና ማምለጫ ሲፈልጉ በየትም ያለ የተዋህዶ ኦርቶዶክስ ልጅ በትህትና፣ በቅንነት፣ ራስን ዝቅ በማድረግ፣ መርዳት ዋናው ተግባርና ግዴታው ነው፡፡*
› በትምክህት የሚናገር የሚያደርግ የሚመጻደቅ ብርቱ ቅጣት ይጠብቀዋልና ከዚህ አጸያፊ ስራ ይቆጠብ፡፡
› አንዳንድ መንግስታቶች ቡድኖች ድርጅቶች ይጠቅመናል ባሉት ድርጅቶች የመከለሻ ዘዴ ተጠቅመው ሊገልጹት ይችላሉና በጥንቃቄ ከያዛችሁት ኦርጅናል መልእክት ጋር አመሳክሩት፡፡
› *ማንኛውም የሃገር መሪ፣ የእምነት ድርጅት መሪ፣ የጦር መሪ፣ የደህንነት ሃላፊ፣ የምክር ቤት አባላት፣ የመወሰኛ ምክር ቤት አባላት፣ የአለም አቀፍ ድርጅት መሪዎች፣ የእርዳታ ድርጅት መሪዎች፣ አለም አቀፍ የሙያ ማህበሮች ሃላፊነት ያለበት የህዝብ አመራር የያዘ በሙሉ ይህን ትእዛዝ ያስተውል፡፡*
*ሀ/ ባለው የወልም ሆነ የግልም ሃላፊነት ትልቅነትና ትንሽነት በዚህ መልእክት መሠረት ስለሚመዘን፣ መረጃን ለሕዝቡ መግለጽ፣ ሕዝቡን ወደ እውነት መመለስና ማስረዳት ግዴታው ነው፡፡ ይህን የማያደርግ እንደ ግለሰብም እንደ መሪነቱም ይጠየቃልና፡፡ እንደ ትእዛዙ የሚፈጽም ከሆነ ሸክሙ ይቀላል፡፡*

ለ/ በተለይ የአገር መሪዎች የአገሪቱ ህግ አውጪዎች በሕዝብ ተመርጠናል የሚሉ የስርና የበላይ ም/ቤቶች፣ ይህንን መልእክት በግልጽ ማሳወቅ፣ ማስረዳት፣ ወደኢትዮጵያ መጥተው ለመረዳት ለሚሹ ማገዝ መርዳት፣ መስጠት፣ ከኢትዮጵያ ካሉት ጋር ማገናኘት ግዴታቸው ነው፡፡

መፅሐፈ መቃብያን ቀዳማዊ 22 ፡ 5

ሐ/ በየትኛውም ሀገር የሚገኝ ዳኛ፣ አቃቢ ህግ፣ የፀጥታ ሰራተኛ፣ የጦር አባል፣ ቁጣው ሲፈስ ሹመትና ጉልበት እውቀትና ሃብት አያድነውምና አውቃችሁ ጠብቁ ወይም ፈጥናችሁ ውጡ፡፡

መ/ ማንኛውም ሰው ወይም መንግስት በቂ መረጃ ሳይሰጥ የሚያፍን ከሆነ በየአቅሙ ብርቱ ቅጣት ያገኘዋል፡፡ በዚህ ድርጊት ምህረትን አያገኛትም፡፡

ሠ/ ማንኛውም አሰናካይ እንቅፋት ሰው ሁሉ ይፈዝበታል፡፡ ሞትን እየለመነ ያልፋል፡፡ ይጨልጣታል፡፡

ረ/ በ7/3/1998 የተገለፀውን የመጀመሪያ መልእክት በ27/9/2000 የተገለፀውን ሁለተኛ መልእክት ለሕዝብ ሳትገልጹ አፍናችሁ ያስቀራችሁ ግለሰቦች፣ የአገር መሪዎች፣ የእምነት ድርጅት መሪዎች፣ የዜና ማሰራጫዎች፣ አለም አቀፍ ድርጅቶች፣ በአጠቃላይ መልእክቶቹ ደርሶአችሁ የናቃችሁ የቃለላችሁ ያፌዛችሁ ሁሉ አሁንም ይህ የአፈጻጸም ውሳኔ ቢደርሳችሁ እንደቀድሞው ስተታችሁን ብትደግሙ፣ ደግሞም ታደርጋላችሁና፣ በመጀመሪያ የቁጣውን እሳት ትጋታላችሁ ይህ ሲደረግ ሌላውም ይማራልና በዚህ ስተት ያለቅጣት አትታለፉም፡፡

መጽሐፈ ምሳሌ 16 ፡ 5

ሰ/ ይህንን መልእክት በመናቅ፣ በማፌዝ፣ እንደ እብድ ንግግር በመቁጠር ከቀደመው ክፋታችሁ፣ ትእቢታችሁ፣ እውቀታችሁ፣ ሃብታችሁ፣ በመመጻደቅ በጨበጣችሁት የመሳሪያ ጉልበት በመመካት ጸንተው የሚቆሙ መሪዎች፣ አገሮች፣ ቡድኖች፣ ድርጅቶች፣ የእምነት ተቋሞች፣ ግለሰቦች፣ ባለእውቀቶች፣ ፈላስፎች፣ ሊቆች፣ ጀነራሎች አሉና በመልዕክቱ አምኖ የተጸጸተና የተመለሰ ሰው ምንም ይሁን ምን ከላይ ከተጠቀሱት ፈጽሞ ራሱን ማራቅ አለበት፡፡ በክፉ ስራቸው መተባበር መታዘዝ የለበትም፡፡ እነዚህ ለቁጣው ማረፊያ የተሰናዱ ጠፊ ናቸውና፡፡

ሸ/ በየትኛውም አገር ያለ አገርን የሚጠብቅ መሪ፣ ወታደር፣ እንደተሸከመው የሕዝብ ሃላፊነት መጠን ቁጣው ሲበረታ አደጋው ሲጨምር ጠረጋው ሲያይል ሕዝቡ ወደ እውነቱ እንዲመለስ መጣር አለበት፡፡ በከንቱ ምክንያት እየደረደረ መፍትሔ አመጣለሁ እያለ ጊዜውን ማባከን የለበትም፡፡ ስብሰባ፣ እቅድ፣ ውይይት፣ የመፍትሔ ውሳኔ ድንማ ሁሉ ይታቀዳሉ እንጂ የሚያመጡት ውጤት ስለሌ ማንኛውም ሰው በዚህ መልእክት የታዘዘውን የተነገረውን እንዲፈጽም እንዲረዳ ማድረግ ግዴታ ነው፡፡

መጽሐፈ ምሳሌ 12 ፡ 26

ወደ መልእክቱ ምንጭ ወደ እግዚአብሄር ሕዝቦች ማረፊያ መቀመጫና ማዘዣ ስፍራ /ኢትዮጵያ/ ለመምጣት መመሪያ ማግኘት ለሚፈልጉ ማናቸውም ሰዎች እንደግለሰብም፣ እንደቡድንም፣ እንደድርጅትም፣ እንደአገርም በፈለጉት ቅርጽ ሆነው ለመምጣት ቢሹ ያሉበት አገር እና አስተዳደሩ በሁሉም መልኩ መርዳት ይገባዋል፡፡ በአገሬ ያለው መንግስት ምን ማድረግ እንዳለበት በራሱ የሚያስፈልገው መመሪያ ይሰጣልና በኢትዮጵያ በኩል ምንም እንቅፋት እንዳይኖር ይደረጋል፡፡

በኢትዮጵያ ያሉ ማናቸውም ድርጅቶች፣ ማህበሮች፣ ተቋሞች፣ የቤ/ክ መጠለያዎች፣ አገልጋዮች፣ መዕመናች ለሚመጣው ሁኔታ ሁሉ እራሳችሁን ማዘጋጀት አለባችሁ፡፡ ድርብ ሃላፊነት ይጠብቃችኋል፡፡ ከየትኛውም አለም የሚመጣ እንግዳ ወንድም እህታችሁን እግዚአብሄር እንደሰጣችሁ ቸርነት መጠን በቅንነት፣ በንፅህና፣ በትህትና፣ በፍቅር ልዑል እንዳስተማራችሁ ሆናችሁ ማገልገል ግዴታችሁ ነው፡፡

በኢትዮጵያ ተ/ኦ/ቤ/ክርስቲያን መሠረት የታነጻችሁ፤ ውድ አባቶቼ እናቶቼ አበው የተዋህዶ እምነት መምህራን፣ ሊቀ ሊቃውንት፣ የዜማ፣ የቅኔ፣ የአቋቋም መምህራን፣ የድጓ መምህራን በየጫካው የወደቃችሁ መነኮሳት፣

ባህታዊያን፣ በየገጠሩ በእምነታችሁ ፅናት ከቤ/ክ ተባራችሁ በመንከራተት ላችሁ አገልጋዮች ምእመናን በሙሉ ከእንግዲህ የሚጣለው ተጥሎ ለተጋድሎአችሁ ከጌታችሁ ክብርን ምስጋናን በረከትን ታገኙ ዘንድ ታዟልና በተባረከችው ኢትዮጵያ ! አለምን በምትመራው ውድ አገራችሁ ኢትዮጵያ ! የልዑል የክብሩ ማረፊያ ኢትዮጵያ ! እነሆ ስራውን ትረከቡ ዘንድ የአፈጻጸም ውሳኔ ተላለፈ፡፡ በመሆኑም ለደስታውም፣ ለመጽናናቱም፣ ለአገልግሎቱም፣ ራሳችሁን አዘጋጁ፡፡

በመላው አለም በክብር በፀጋው ተሞልታችሁ ለኢ.ኦ.ተ.ቤ.ክ ለድንግል እናታችሁ፣ ለአባታችሁ፣ ለወዳጆቻችሁ፣ ለሚካኤል፣ለገብርኤል፣ ለሩፋኤል፣ ለፋኑኤል በጥቅሉ ለእውነት እምነታችሁ ለማገልገል ተዘጋጁ አንበሶች የልዑል አረበኞች ተፅናኑ፡፡

መጽሐፈ ምሳሌ ም 30 /6/ 29 – 31

ትንቢተ ሚልኪያስ፡ ም 3 ፡ 1 – 6

ደ/ መንፈሳዊ አገልግሎትን ወደ ንግድ ለመለወጥ የሚያስቡ ካሉ አሁኑኑ ሌላ አለም ለመኖር ቢያስቡ ይቀላቸዋል፡፡ አልምርምና እንግዳችሁን በፍቅር ያለ ዋጋ አስተናግዱ፣ የአባቶቻችሁን ህግ ተከተሉ ፈቅዶ በፍቅራችሁ ደስ ብሎት ለሚባርካችሁ፣ ስጦታም ለሚሰጣችሁ በትህትና ተቀበሉ እንጂ እንደ ንግድ የአገልግሎት ዋጋ አትቀበሉ፡፡ ቀድሞም ስራችሁ ንግድ የሆነ በግልፅ የንግድ ቤት መሆኑን አሳውቁ በተለይ ቤት አከራዮች ቤት የእግዚአብሄር መሆኑን እወቁ የምታደርጉት ሁሉ ለንግድ ሳይሆን ከፈጣሪ ለሚገኝ በረከት ይሁን፡፡

ያለፉትን፣ በቅጣት የተጠረጉትን፣ በክፋት የጸኑትን፣ የማይበሉትን የአመጽ ሃብት የሰበሰቡትነ፣ አብረዋችሁ የሌሉትን፣ ሁሉን ትተው ወደ አፈርነት የተቀየሩትን ወገኖች አስቡ፡፡ እናንተ የቀራችሁት የነሱን ስራ ለመድገም አይደለም ከዚህ ፍጹም ራቁ እኔም አላልፋችሁምና፡፡

**17 ከቅጣት በኋላ የሚፈጠር መንፈሳዊና ስጋዊ አኗኗር አስተዳደር ምን ይመስላል፡፡**

1. አለም የሚጠብቃት በትርን እሳት ፈፅሞ አይታው የማታውቀው ነው፡፡ በዚህ የቁጣ ፍሰት አመፀኞች በሙሉ ይጠረጋሉ፤ ምንም መሸሸጊያ ማምለጫ ቀዳዳ ያጣሉ፡፡ የሰው ዘዴ ሁሉ ከንቱ ይሆናል፡፡ አዲስ ስርአት ይፈጠራል፣ አዲሱ አስተዳደር ይዋቀራል፡፡
2. ኢትየጵያ የአለም ሁሉ መንፈሳዊም ስጋዊም መሪ ትሆናለች፡፡
3. በአለም አንድ እምነት አንድ ጥምቀት መልከ ብዙ አንድ ሕዝብ ይሆናል፡፡
4. ቋንቋ ዛሬ ያለው የአለም የቋንቋ አጠቃቀም ከስሞ የኢትዮጵያ ቋንቋ አማርኛ የአለም መግባቢያ ቋንቋ ይሆናል፡፡ መላው አለም እንግሊዚኛን እንደሚያጠና ሁሉ ያ ቀርቶ አማርኛ ዋናው መግባቢያ ይሆናል፡፡ የሥራም ቋንቋ ይደረጋል፡፡
5. በኢትዮጵያ የሚቆመው ብርሃናዊ አገዛዝ በመላው አለም ሰው ዘር በሙሉ የሚመቸውን የአስተዳደር፣ የፍትህ፣ የኢኮኖሚ፣ የገንዘብ፣ የትምህርት፣ የጤና፣ የመገናኛ ወዘተ አሰራሮች ያሰፍናል፡፡
6. በኢትዮጵያ የሚቆመው የኢትዮጵያ ተዋህዶ ኦርቶዶክስ በመላው አለም ያለውን የሰው ዘር መንፈሳዊ ሕይወት በራሷ ቀኖናና ስርአት ከልዑል በሚሰጣት ትእዛዝ ትመራለች ቅድስና የተሞላበትን መንፈሳዊ ሥራ ትሠራለች፡፡ ለአለም ብርሃን ሆና ታበራለች፡፡
7. በቤ/ክርስቲያን የመንፈስ ቅዱስ አመራር የሚሾሙ አባቶች ፣አገልጋዮች በመላው አለም ይበተናሉ ሕዝቡን ይመራሉ፡፡ ያንጻሉ ያስተምራሉ፡፡
8. መንፈሳዊ አገልግሎት ሁሉ መሠረቱ የሚጣለው በኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤ/ክርስቲያን ስረአት አሰራርና ትምህርት ይሆናል፡፡ የሚቋቋሙ ቤ/ክርስቲያኖች በቤተ ክርስቲያኗ አመራርና ፈቃድ መሠረት ይሆናል፡፡

9. በኢትዮጵያ የሚጸናው የልዑል ዙፋን በሥላሴ የታመኑ የተቀቡ አገልጋዮች የሚቀመጡበትና ከነሱ በሚፈሰው መንፈሳዊና ስጋዊ አመራር እንደ እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ ፈቃድና አመራር በመላው አለም በሚዋቀረው ስርአተ አገዛዝ ሕዝብ በሙሉ መንፈሳዊውንም ሥጋዊውንም አመራር ያገኛሉ፡፡

በመላው አለም ያለው የወሰን አከላለል ሁሉ ለአስተዳደር፣ ለሕዝብ አኗኗር፣ ለጉርብትናው፣ ለመቀራረቡ፣ ተፋቅሮ ለመኖሩ በሚመች ሁኔታ ይስተካከላል፡፡ የቀደመው ቅኝ ገዥዎች አሻራ ይወገዳል፡፡

በመላው አለም ያለው የሥጋ አሠራር መንፈሳዊ ሕይወትን የማያዳክም የማይጎዳ መሆኑ ሲረጋገጥ ተግባራዊ ይሆናል፡፡

አለም የምትተዳደርበት መንፈሳዊ ሕግና ስጋዊ ሕግ ወጥና አንድ ብቻ ይሆናል፡፡ ዓለም አንድ ሕገ መንግስት ብቻ ይኖራታል፡፡ በሕገ መንግሥቱ ተመስርቶ በማይቃረን በማይሻር መልኩ በየአለሙ ገፅታ ለተዘረጉ የከባቢ አስተዳደሮች ሕጎች ይደነገጋሉ፡፡ የሚወጡ ሕጎች በሙሉ ከዚህ ከኢትዮጵያ ማእከል ቀርበው ይፀድቃሉ፣ ይሻገራሉ፣ ይታረማሉ፣ ይሻሻላሉ፡፡

የፀጥታ ኃይሎች በመላው አለም በመንፈሳዊ ስነ ምግባር በሕግ አግባብ ታንፀው በቅንነት የሚያገለግሉበት ስርአት ይደራጃል፡፡ ፍትህ በመንፈሳዊና ስጋዊ አሰራር ምን እንደሚደረግ ወደፊት ከመንፈሳዊ አባቶች ከሕግ ባለሙያዎች ጋር በመቀናጀት ወጥ ስረአት ይዘረጋል፡፡ እውነትን ብቻ መሠረት የደረገ የፍትህ ስርአት ይደራጃል፡፡

ትንቢተ ሚልኪያስ፡ ም. 4 በሙሉ

አለም በውስጧ ብዙ ሕዝብ እንደማቀፏ መጠን የሕዝብን ሃብት ጠቅልሎ በጥቂት ግለሰቦች ሰብስቦ መክተት ዛሬም የሚታየውን የገብጋቦች አለም እንዲወገድ ያደርጋል፡፡

በተለይ አሜሪካ አውሮፓ ከብዙ ጥፋት ፍሰት በኋላ ስለሚንበረከኩ ጉዳታቸው እጅግ ይከብዳል፡፡

በአለም ያሉ ዛሬ ሲታዩ ትልቆች መሪዎች ባለሃብቶች ሁሉን አድራጊዎች ሊያውቁት የሚገባ ነገር ቢኖር በኢትዮጵያ በፍትህ አደባባይ ቀርበው ቅን የፈጣሪን ዳኝነት ያገኛሉ፡፡

ሥጋዊ አሰራሮች የእለት ተእለት ክንዋኔዎች ሁሉ ምንዝርናን፣ ሌብነትን፣ ክፋትን፣ ተንኮልን፣ ማታለልን፣ ማጭበርበርን፣ በወንድም ላይ በደል መፈጸምን ከመንፈሳዊ ሕይወት መስመር መውጣትን የሚያስወግድ ፈፅሞም የማይሸከም ሆኖ ይደራጃል ይዋቀራል፡፡

**18 አለም የተሸከመችው የጥፋት መሣሪያ እጣ ፈንታስ**

ሀ/ አለም ለረጅም ዘመን ለመፋጇያ መሣሪያን ስታደራጅ ኖራለች የመጀመሪያው የጥፋት መሣሪያ ድንጋይ ነበር፡፡ ቃየል ወንድሙን በዲያቢሎስ ግፊት፣ በቅናት ተነስቶ የገደለው በድንጋይ ነበር፤ ከዚያ ጊዜ ጀምሮ የጥፋት መሣሪያ አደራጅቶ ወንድምን መግደል ተዘወተረ፡፡

ለ/ የጥፋት መሣሪያዎች አንድ ሰው መግደል ብቻ በማዘውተራቸው ሰው በጠላት ግፊት የመግደያ መሣሪያዎቹን እያሻሻለ መጣ ከድንጋይ ወደቀስት ከቀስት ወደብረት እያለ አንድ ሰውን መግደል ተለመደ፡፡ የሰው ስጋ ብርቱ የጠላት መሳሪያ ነውና በሥጋ ፍላጎቱ የማይረካው ሰው ብዙ የተሻሻሉ መሣሪያዎችን ሠራ፡፡ ከብዙ ዘመን ጉዞ በኋላ ሰው ታላላቅ የሰውና የንብረት ጥፋት የተደረገበትን 1ኛው የአለም ጦርነትን 2ኛው የአለም ጦርነትን አካሄደ፡፡ አንድ ሰው ከመግደል አልፎ በሰራው ፈንጂ፣ ጀት፣ መድፍና ታንክ በሺና በሙቶ መፍጀት ጀመረ፡፡ ይህ መጠን ያላረካው ዲያቢሎስ ጥበቡን እንደተሞላ ነውና፡፡ የተሻለን የጥፋት መሣሪያ ለሰው አስጨበጠ ኒዩክለር ተሠራ በጃፓን ተሞከረ ከ300 ሺ ያላነሰ ሰው ፈጀ በዚህ ያልረኩት የዲያቢሎስ አሽከሮች የምድርን ሰው መላልሶ የሚያጠፋ ኑዩክለር በብዛት ሰሩ ይህ አልበቃቸውም የኬሚካል መሣሪያ ሠሩ ሰውን በጣጥሶ የሚያጠፋ፣ ኒውትሮን ሰሩ፡፡ ሕይወት ያለውን ብቻ ለይቶ የሚገድል፣ ባዮሎጂካል መሳሪያ ሰሩ በሽታ አምጪ ቫይረሶችን ጨራሽ

አውዳሚ ባክቴሪያዎችን በላብራቶር አደራጁ ስንቴ ሰውን ሊያጠፉት እንዳሰቡ የሚገርም ነው፡፡ ከ9 የማያንሱ አገሮች ይህንን የኒዩክለር መሣሪያ ተሸክመዋል፡፡

ትንቢተ ሚኪያስ 5፡- 10 - 15

ትንቢተ ኢሣኢያስ 24፡- 1 13

በዚህ አልቆሙም እጅግ ግዙፍና የረቀቁ መርከቦችን፣ ሚሳኢሎችን፣ መድሮችን፣ ታንኮችን፣ አጥቂ ሳተላይቶችን በጥቅሉ ሰው የማያውቃቸውን የረቀቁ የጥፋት መሣሪዎችን አከማቹ ሰሩ፡፡ ተዘጋጁ ወንድማቸውን ሊገድሉበት የረቀቁ የጥፋት መሣሪያዎችን አከማቹ ሰሩ ተዘጋጁ ወንድማቸውን ሊገድሉበት እንደ ቃዬል አንዴ አይደለም መልሰው መላልሰው ሊያጠፉበት አለሙ ዛሬም በዚያው ሕግና አላማ ውስጥ አሉ፡፡ ታላላቅ መንግስታት ለሃብታቸው ዋስትና ለወንጀላቸው መሸፈኛ ለድሃ መርገጫ ደሃ መንግስትና ሕዝብ ለመዝረፊያ ተጠቅመውበታል ዛሬም እየተጠቀሙበት ይገኛሉ፡፡ የአለም ዳኛ ነን የሚሉ ታላላቅ ጉልበተኛ መንግሥታት በዚሁ መሣሪያቸው በሰበሰቡት ሃብታቸው በየቦታው ባደራጁት ተገዥ አሽከሮቻቸው አለምን ወደ ፍፁም ጥፋት እየገፏት ይገኛሉ፡፡ ይህን መሣሪያ የጨበጡት እነዚህ ሀገሮች አሜሪካ ከራሽያ፣ አረብ ከአሜሪካ፣ ኮሪያ ከኮሪያ፣ ሕንድ ከፓኪስታን፣ እስራኤል ከአረብ ከፍልስጤም፣ አንዱ አገር ከአንዱ አገር በቅኝ ገዥዎች በተከለለ ድንበር ሲፋጁ ሲነታረኩ የሚታዩበት የዘወትር የአለም ድራማ ነው፡፡ የሰው ልጅ ልብ ብለህ አስተውል ጌታ ባይጠብቅህ ዲያቢሎስ የደገሰልህ ድግሥ ስንቴ ከመቃብር እያወጣ እንደሚገልህ /ቢቻል/ አስብ አሜሪካ 10 ሺ የኒዩክለር አረር፣ ራሺያ 8ሺ የኒዩክለር አረር፣ ቻይና የኒዩክለር በሺ አረር፣ ፈረንሳይ በሺ የሚቆጠር አረር፣ እንግሊዝ በሺ የሚቆጠር አረር፣ ሕንድ፣ ፓኪስታን፣ እስራኤል ከዚያም በመቶ የሚቆጠር የኒዩክለር አረር ተሸክመዋል፡፡ ለአለም ጥፋት የአንዱ አገር በቂ ነው፡፡ በዚህ አልቆሙም ይህንኑ መሣሪያ ጠፈር ላይ ሰቅለዋል፡፡ ከዚህ በላይ ወንጀለኛ ምን ይምጣ? ታዲያ ይህ እንዴት ይወገዳል፡፡

**ሀ / የተሸከሙትስ መሣሪያ እጣ ፈንታስ?**

- ይህ የጥፋት መሣሪያ የተሸከሙ አገሮች ለራሳቸው የደገሱት ነው፡፡
- በእግዚአብሄር የተመረጡ የትም የሁኑ የት ምንም ይፈጠር ምን የሚነካቸው የለም፡፡
- የተሸከሙት መሣሪያ በሙሉ ከምድረ ገጽ ይጠፋል፡፡ ሲጠፋም እነሱኑ የጥፋት አለቆችን ይዞ ይሔዳል፡፡

ትንቢተ ሕዝቅኤል ም 26 /27/ በሙሉ

- እነዚህ አገሮች በኪሳቸው የሚነድ እሳት የከተተን ሰው የመስላሉ፡፡
- አጠፋፉን ሁሉ የሚያየው ስለሆነ መመልከት ለታደሉት ነው፡፡
- የሚጠፉ መልካሙን ሳያዩ ከጥፋት መሣሪያው ጋር አብረው ይበናሉ፡፡
- እንዴት? ያንን ለሃያሉ የሠራዊት ጌታ ውሳኔ አስፈጻሚ የብረሃን መላእክቶች እንተወው፡፡

**ለ/ አለም በምን ትመራለች ማእከሉስ የት ይሆናል?**

- አለም ከትቢያ በምትነሳው የረሃብ ምሳሌ በሆነችው በአገሬ ኢትዮጵያ ትመራለች፡፡ ትገዛለች፡፡
- ከታላቁ የቁጣ ፍሰት በኋላ አለም በውድም በግድም ይህንን የልዑልን ውሳኔ ይቀበላል፡፡ ተግባራዊ ያደርገል፡፡ ይገዛበታል፡

የአለም አመራር ማእከሉ በኢትዮጵያ ዋና ከተማ ይሆናል፡፡ አለም ቸሩ አምላክ ባነገሠው ንጉሠ ነገሥት ከሱ ጋር አብረው በሚሾሙ የልዑል አገልጋዮች ትመራለች፡፡ ንጉሡም በታላላቅ ሽማግሌዎች የእግዚአብሄር ሰዎች ይከበባል፣ ይመከራል፣ ይታገዛል፡ የአለምን አመራር የሚይዘው የልዑል ባሪያ በዙፋኑ ላይ ሲሆን አብረውት የሚሰሩ በሚሰጣቸው የማእረግ ደረጃ በመሆን ለመንፈሳዊ ጉዳይና ስሰጋዊ ጉዳይ የማማከር ተግባር የሚያከናውኑ ይኖራሉ፡፡

አለም ቸሩ አምላክ በቀባው አባት በኢትዮጵያ ተዋህዶ ኦርቶዶክስ ቤ/ክ አባትና መሪ ከሱም ጋር አብረው በሚቀቡ በእግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ በሚመሩ የእምነታችን አባቶች ትመራለች፡፡

መንፈሳዊ አባቶች በመላው አለም ይመደባሉ፡፡ መንፈሳዊና ስጋዊ አሰራሩ ተጣምረው በእግዚአብሄር ፈቃድ የሚመሩ ስለሆነ እንደየሰው ብዛት እርቀት የአገሩ ስፋት እየታየ የአገልጋዮቹ ምደባ ይፈጸማል፡፡ በየደረጃው የሚመደቡ ሁሉ የራሳቸው የስልጣን ሽፋንና የመወሰን ጣሪያ ይኖራቸዋል፡፡ የህንንም የሚወስን ሕጋዊ አግባብ የደራጃል፡፡

በሥጋው ስራና አገልግሎት የሚመደቡት አለምን በሚገዛው የቅድስናና የፅድቅ ሕገመንግሥት ስለሚመራ ከዚህ ጋር አግባብ ያላቸው ሕጎች እየወጡ በዚያ መስፈርትና ማእቀፍ የመላው አለም የአስተዳደር የአገዛዝ የአመራር የኢኮኖሚ የገንዘብ፣ የማሕበራዊ አገልግሎት በተያያዥነት ይደራጃል፡፡

በልማድ የደጉ ባህሎችና የአካባቢ አኗኗሮች ከመንፈሳዊና ሥጋዊ አሰራር ጋር የሚስማማው ተዋህዶ የማይስማማው ተጥሎ የአኗኗር ሁኔታ መሠረት ይይዛል፡፡

ትንቢተ ዘካሪያስ ም፡ 4 /5/ በሙሉ
የዳዊት መዘ. 131 /132/ 6 – 18

## 19 የአስተዳደር ማእከላት

በመላው አለም የአስተዳደር ተዋረድ በዚህ መልክ ይሆናል፡፡

**ሀ/ አፍሪካ** ይህ አህጉር በአራት ይከፈላል 1ኛው ምስራቅ አፍሪካ 2ኛው ደቡብ አፍሪካ 3ኛው ሰሜን አፍሪካ 4ኛው ምዕራብ አፍሪካ ሲሆኑ ደሴቶች በሚቀርቡአቸው አካሎች ይካተታሉ፡፡

**በዚህ** የአፍሪካ 4 አካል እንደ አገር መሪ በእያንዳንዱ ክልል በዋናው ማእከል የሚሾሙ መሪዎች ከሙሉ መንግስታዊ ስርአት ጋር ይደራጃሉ፡፡ የተቀረው አስተዳደር ተጠሪነቱ ለዚሁ ማእከል ይሆናል፡፡ 4ቱም የአፍሪካ መሪዎች ተጠሪነታቸው በኢትጵያ ላላው ለዋናው ማእከልና የንጉሠ ነገሥት አስተዳደር ይሆናል፡፡ የክልል መሪዎችም የንጉስ ማእረግና የተሟላ መንግስታዊ ስርአት ይኖራቸዋል፡፡ ይህንኑ ተከትሎ መንፈሳዊው መዋቅርም ይህንኑ እየተከተለ የራሱን መንፈሳዊ የአስተዳደር የአመራር ስርአት ያደራጃል፡፡

**ለ/ አውሮፓ** ይህ ክ/አህጉር ለሁለት ይከፈላል 1ኛ ምስራቅ ክልል 2ኛ ምዕራብ ክልል ይሆናል፡፡

ሁለቱም የአውሮፓ የየክልል መሪዎች እንደ አገር መሪ በየክልሉ ከዋናው ማእከል ይሾማሉ፡፡ የተቀረው በሥራቸው የሚዋቀረው አስተዳደር ተጠሪነቱ ለክልሉ መሪዎች ይሆናል፡፡

መንፈሳዊ አመራሩ የአስተዳደሩን አከላለል ተከትሎ የራሱን አስተዳደራዊ መንፈሳዊ የአመራር ስርአት ይዘረጋል፡፡ ሁለቱም የክልል መሪዎች ተጠሪነታቸው ለንጉሠ ነገሥቱ ይሆናል፡፡

**ሐ/ ስካንዲኒቪያ** ይህ ክልል 1 መሪ ይኖረዋል፡፡ አወቃቀሩም ከላይ በ ሀ/ለ እንደተጠቀሱት ይሆናል፡፡

**መ/ አውስትራሊያ** ይህ ክልል በዙሪያው ያሉትን ደሴቶች በሙሉ አካቶ በ1 የክልል መሪ ይተዳደራል፡፡ አወቃቀሩም ከላይ በሀ/ለ እንደተጠቀሰው ይሆናል፡፡

**ሠ/ ሰሜን አሜሪካ** ይህ ክ/አህጉር በሁለት ይከፈላል በሰሜንና በደቡብ የየክልሉ መሪዎች በሀ/ለ እንደተመለከተው ይዋቀራሉ፡፡

**ረ/ በደቡብና ሰሜን አሜሪካ** የሚገኙ ደሴታማ አገሮች ራሳቸውን ችለው በአንድ የክልል መሪ የተዳደራሉ፡፡ አወቃቀሩም በሀ/ለ እንደተጠቀሰው ይደራጃል፡፡

**ሰ/ ላቲን አሜሪካ** ይህም በሁለት ይከፈላል 2 የክልል መሪዎች ይኖሩታል፡፡ አወቃቀሩም በሀ/ለ እንደተገለጸው ይሆናል፡፡

ሸ/ **ኤሺያ** ይህ ክ/አጉር በ7 የክልል መሪዎች የመራል

ሸ/1 ራሺያ፤ ሞንጎሊያ ክልል 1

ሸ/2 ቻይና፤ ሆንግ ኮንግ ክልል 2

ሸ/3 ጃፓን፣ ኮርያዎች፣ታይዋን ክልል 3

ሸ/4 ህንድ፣ ፓኪስታን ክልል4

ሸ/5 ቬትናም፣ ታይላንድ፣ ካምቦዲያ፣ በርማ፣ ፊሊፒንስ፣ ኔፓል፣ ባንግላዴሽ፣ ላኦስ ክልል 5

ሸ/6 ካዛኪስታን፣ ታጀኪስታን፣ ኡዝቬክስታን፣ ተርኪሚስታን፣ አርመኒያ፣ አዘርባጃን፣ ኪርግስታን፣ ጆርጂያ ክልል6

ሸ/7 ኢራን፣ አፍጋኒስታን ክልል 7

ቀ/ **መካከለኛው ምስራቅ** ሳኡዲ አረቢያ፣ የመን፣ ኳታር፣ ባህሬን፣ ኩዌት፣ ኤሚሪትስ፣ ጆርዳን፣ ኢራቅ፣ ሊባኖስ በሁለት የክልል መሪዎች ይመራል፡፡ በሀ/ለ ባለው አወቃቀር ደራጃል፡፡

በ/ **እስራኤል** የኢትዮጵያ አምላክ ልጅ ከአባቷ ቤት ያልገባች በአመፅ ያለች ልጅ ናት፡፡ ቢሆንም ከማእበሉ የሚተርፉት የኢትዮጵያ ታናሽ ወንድም ይባላሉ፡፡ አስተዳደራቸው በራሳቸው የውስጥ አስተዳደር ሙብት ይተዳደራል፡፡ መንፈሳዊ አመራሩን ግን ከኢትጵያ ባለው ማእከል ይመራል፡፡ ይደራጃል፡፡

## 20/ *ሀ.* አስተዳደሮች ተዛምዶዎች በመንፈሳዊ አይን እንዴት ይጠራሉ፡፡ እንዴትስ መልካም ይሆናሉ፡፡

ወገኔ የሰው ዘር በሙሉ ልብ ብለህ በስጋህ ሳይሆን በመንፈሳዊ ሚዛንና አይን እይ ! ለማታየው አትይ አይን አለህ አታይምና ጆሮ አለህ አትሰማምና አእምሮ አለህ አታስተውልምና፡፡

ባለብረሃኑ ወገኔ የሰው ዘር አስተውል አድምጥ !

በዛሬው ጠፊ አለም መጪውን አትለካ የዛሬ አለም የበሸቀጠ በሃጢያት ባህር የተዋጠ በዲያቢሎስ የጨለማ ሥራ የተተበተበ ነው፡፡ ይህ አለም ይጠረጋል ይጸዳል፡፡ ዲያቢሎስ ከነጭፍራው በእሳት ይጠረጋል፡፡ የሚተው የለምና ወደ መልካሙ ዘመን የሚሻገረው የዛሬው ልበ ጠማማ አይደለም ልበ ቅኑ እንጂ ብርሃን የሚያየው ፈጣሪውን የሚወድድ እንጂ የዲያቢሎስ ልጅ አይደለም፡፡ ስለዚህ መጪውን ምን ይመስላል ብለህ አትጨነቅ መጪው ከቅጣቱ በኋላ እጅግ መልካም ይሆናል፡፡

የሰው ልጅ ይዋደዳል፣ ጠብ ክርክር ይጠፋል፣ ሁሉም በአንድ እምነት በተዋህዶ ይቆማ፡፡ በአንድ ፈጣሪውን ያመሰግናል፡፡ ሰው ለፈጣሪው ቅርብ ፈጣሪ ለሰውም ቅርብ ይሆናል፡፡ አለም በቸርነቱ ጠል ትረሰርሳለች ሰው ከመደሰቱ የተነሳ ፈጣሪውን የሚያመሰግንበት የሚሰራበት የሚደሰትበት የቀኑ ብርሃን ለምን መሸ ይላል፡፡ ሌሊቱ የጣፈጠ እንቅልፍና እረፍት ያለበት ከፈጣሪ ተገናኝቶ መባረኪያ ስለሆነ ለምን ነጋ ይባላል፡፡

ወንወድሞቼ እህቶቼ ዛሬ የጨለማ አሰራር ነው ያለው፡፡ ያኔ የብርሃን አሰራር ነው የሚሰፍነው፡፡ ለማን ትሰጣለህ ሁሉ አለው፡፡

ስለ ችግር ማን ይነግርሃል ሁሉም ከችግር ተላቋል፡፡ ይህንን ታያለህ አምላክህን ትለምናለህ ሁሉንም ይሞላልሃል፡ በዚህ የበረከት ዘመን ፈጣሪ ሰውን እንደዚያ ቅርብ ሆኖ የሰማበት የሚሰማበት ዘመን አልነበረም አይኖረምም፡፡ ስለዚህ ሁሉ ጨለማ ሲገፈፍ እየጠራ ይመጣል፡፡

› አለም አንድ የመገበያያ ገንዘብ ይኖረዋል፡፡ የዛሬው ጠንካራ፣ ደካማ ገንዘብ የሚሉት ንግግር ይጠፋል፡፡

## 21/ **የመሪዎች ማረፊያ ማእከል የት ይሆናል፡፡**

ይህ ከአስተዳደሮቹ አወቃቀር አከላለል በኋላ የሚወሰን ይሆናል፡፡ በክልልነት፣ በአገርነት የሚቆሙ ሁሉ ሊኖራቸው የሚገባ የውስጥ ስልጣን አስተዳደር የመወሰን ርቀት የሥልጣን ተዋረድ አለምን በሚመራው ሕገ መንግሥትና በዚሁ መሠረት በሚወጣው ሕግ ይወሰናል፡፡

## 22/ በመላው አለም የሚፈሰው መንፈሳዊ አመራርና አገዛዝ ስርአትና ፍሰት እንዴት ይሆናል

**መዝሙር 67 ፡ 11 – 35**

› ይህ በግልፅ እንደተነገረው አለምን የሚመራው የሚያስተዳድረው የሚገዛው አንድ ንጉሠ ነገሥት ሲሆን በየክልሉ የሚወጡ መሪዎችም ንጉሥ ይሆናሉ፡፡ ከነሱ በታች በየአገሮቹ የሚመደቡ መሪዎች ይኖራሉ /ፕሬዘዳንት፣ ጠቅላይ ሚ/ር፣ ሚ/ር ወ.ዘ.ተ./

› ይህንን አወቃቀር ተከትሎ ከንጉሠ ነገሥቱ በሁሉም ጉዳይ የማይለዩ በመንፈሳዊ ስርአት አለምን የሚመሩ መንፈሳዊ አባት ይኖራሉ፡፡ በንጉሠ ነገሥቱና በመንፈሳዊ አባቱ በነሱም ዙሪያ ባሉ መንፈሳዊና ስጋዊ አማካሪዎች በሚደረግ ምክክር በልዑል ፈቃድ ፀንቶ በየክልሉ መንፈሳዊ አባቶች ይሾማሉ፡፡ በየአገሩም እንዲሁ መንፈሳዊ አባቶች ይሾማሉ፡፡ የማእረጋቸው ስያሜ በመንፈሳዊው መሪ አባት በሚመራው የሲኖዶስ ውሳኔ ይወሰናል፡፡

› ማንኛውም ሥጋዊ ሥራ መንፈሳዊውን ሥራ በማይጥስ በማያፈርስ መልኩ ይመራል፡፡ ይህንን ለማድረግ በሁሉም ጉዳይ መንፈሳዊ አገልግሎት ሰጪ ኃላፊዎች በውሳኔ ውስጥ ይገባሉ ያልተስማሙበት ጉዳይ እስከ ጫፍ ድረስ ታይቶ ይወሰናል እንጂ ተቃውሞአቸውን በመጣል የሚደረግ ውሳኔ አይኖርም ቢደረግም በሕግ አግባብ ቅጣት የሚያስከትል ሲሆን ፈጣን እርምት ይወሰድብታል በፍትህ አሰራርና ከመንፈሳዊ አካሄድ ጋር ተጣጥሞ ይዋቀራል፡፡

› ይህን የልዑል ትእዛዝ ለማስፈጸም ተገደውም ሆነ ፈቅደው የሚመጡ ማናቸውም ግለሰብ ቡድኖች መንግስታቶች የእምነት ተቋሞች ወዴት መምጣት አለባቸው ዝርዝር መመሪያ ከየት ያገኛሉ እንዴት የግንኙነት መስመር መፍጠር ይችላሉ፡፡

› **ሀ-** ማናቸውም የሰው ዘር ተገዶም ሆነ ፈቅዶ የሚመጣው ወደ ኢትዮጵያ ብቻ ነው፡፡

› እዚህ ለመምጣት ሲገደድ ወይም ፈቅዶ ሲወስን ወዲህ የሚመጠውን መረጃ ማግኘት መሰናዶ ማድረግ ይገባዋል፡፡ ለአጭርም ቆይታ የሚረዳውን ነገር መያዝ ይገባዋል፡፡

› መረጃ ከኢትዮጵያ ኤምባሲ በውጪ ካሉ ኢትዮጵያውያንና ከራሱ አስተዳደር መጠየቅ ይቻላል፡፡

› ይህንን የልዑል ትእዛዝ ያመጡት የእግዚአብሄር አገልጋዮች ወደፊት በተከታታይ በሚገለጹ ፅሑፎች አድራሻዎችን ስልኮችን ፈክሶችን ኢንተርኔቶችን እንዲዘጋጁ በማድረግ ለመላው አለም እንዲገለፅ ያደርጋሉ፡

› ከዚህ ከመጡ በኋላ ጊዜ ሳይጠፋ የሚያስፈልገውን መረጃ ያገኛሉ ሊያደርጉ የሚገባዎትን ሁሉ መመሪያ ያገኛሉ፡፡

› ለአፈጻጸም ውሳኔው እንቅፋት የሚሆኑ የሚወሰድባቸው ተግሳፅና እርምጃ

› ሀ- በዚህ የእንቅፋት ሥራ የሚሰማሩ ማናቸውም ሰው ቡድን ድርጅት የእምነት ተቋም መንግሥት በመንግስት ስር የተደራጁ ወታደራዊና የፀጥታ የምክር ቤት አባሎች ባለሃብቶች ሁሉም የዚህ የእንቅፋት ስራ ሃሳቢና ፈጻሚ ሁሉ እንደወንጀላቸው ክብደትና ቅለት እርምጃ ይውስድባቸዋል፡፡

› ለ- ምን እርምጃ ይወሰዳል? በመጀመሪያ የዚህ የጥፋት ሰዎች በልዑል ሰራዊቶች ተለይተዋል ፡፡ ቅጣቱ **ሲጀመር እነሱን የሚዘል አይደለም፤ ስለዚህ እየተቀጡ** ተገደው ይፈጽማሉ፡፡ ፈቅደው የሚፈጽሙት የታዘዙትን ለመፈጸም በልባቸው በግልጽም አቋም በመያዛቸው በዚህ ርዕስ አይታሰቡም፡፡

**የዳዊት መዝ ፡ 124 ( 125 )**

› ሐ- ለእምቢተኞች የሚላከው የሚበላቸው እሳት ነው፡፡ እየላጩ እየቆላ ሞትን እንዲፈልጉት የሚያደርግ በመሆኑ እንኳን የሚፈጸምባቸው የሚመለከተውንም እጅግ የሚያስደነግጥ ነው፡፡

› ለአፈጻጸም የመታዘዝ ግዴታ ለሁሉም

› ሁሉም የሰው ዘር እንደ መልክቶች አግባብ መታዘዝ አለበት

› የዚህ ዘር ነኝ፣ የዚህ እምነት ተከታይ ነኝ፣ መሪ ነኝ፣ ክብር አለኝ፣ ሃብት አለኝ፣ እኒህ ሁሉ የተረፈ ሰው ሊያስበቸው የሚገቡ አየደሉምና ይጠንቀቁ፡፡ ከሌለው ከምድሪቱ በቁጣ ከተወገደው ወገኑ እሱ የተለየ አይደለምና፤ የሚለየውም ለምህረት በመታሰቡ ብቻ ነው፡፡

ለ፡-

ሀ- ቀደም በ7/03/1998 ዓ/ም የተገለጸውን መልእክት ቀጥሎም በ27/09/2000 ዓ/ም የተገለጸውን መልእክት አንብቦ ተረድቶ መገንዘብ ያስፈልጋል፡፡

ለ- የአሁኑ መንግስታችን በእግዚአብሄር ፊት ምን ይመስላል?

በግልጽ የሚታወቅ ነው፡፡ አፋቸውን ሞልተው በመገናኛ ብዙሃን እግዚአብሄር መኖሩን የማያምኑ መሆኑን የተናገሩ ናቸው፡፡ የእምነትን አገር የማያምን የሚመራበት ዘመን ማለት ነው፡፡ ስለ ውስጥ ህይወታቸው ብዙ ቢታወቅም ነገ እግዚአብሔር ስለሚገልጠው መናገር አያስፈልግም፡፡

እንግዲህ መሪዎቻችን ልታውቁት ይገባል፡፡ ያላችሁት በኢትዮጵያ ! እየገዛችሁ ያላችሁት በኢትዮጵያ ያለውን ህዝብ ነው፡፡ ይህ ህዝብ ደግሞ አናውቅም በምትሉት በእግዚአብሔር የሚገዛ የተወደደ የተመረጠ ህዝብ ነው፡፡ የመረጣትን ያጸደቃትን እምነት ተወህዶን ለብዙ ሺ ዘመን ሕይወቴ ብሎ ተሸክሞ የመጣ ሕዝብ ነው፡፡ ለማታውቁት እግዚአብሔር ማንነቱን በቤቱ የቅናት ቁጣ ሊያሳውቃቸው የወሰነ ስለሆነ ልትዘጋጁበት ይገባል፡፡

ሐ. ጠመንጃና ታንክ ይመጣል ብላችሁ አትገሠሉ ያ የለም ፡፡ ከጠመንጀው ሁሉ የሚከፋው ሁሉን ከንቱ የሚያደርገው የእግዚአብሔር እሳት እዚያው አጠገባችሁ አለ፡፡ ስለሆነም ይህ የአፈጻጸም ውሳኔ ለህዝብ መበተን ሲጀምር ለእግዚአብሔር የብርሃን ተዋጊ መላእክቶች የልዑል እግዚአብሔር ትዕዛዝ ፈጻሚዎች አብሮ ይደርሳል፡፤ ስለሆነም እግዚአብሔር ማንነቱን ካሰወቃችሁ በኋላ እንነጋገራለን ማለት ነው፡፡

እስከዚያው በማናቸውም ጉዳይ አንዴ አይደለም አስሬ መላልሳችሁ አስቡና ተጓዙ፤ ሁሉም ድርጊታችሁ ሃላፊነትን ያስከትላልና፡፡

ቀደም ባሉት መልእክቶች መተላለፍ ጉዳይ ላይ ማንንም ባለመቃወማችሁ በዚህ መልካም ተግባር ነው እላለሁ፡፤ እስከአሁንም እድሉን ያልነፈጋችሁ በዚህ ነው፡፡

መ- ለሕዝብ ለመግለጽ ግድ ነውና እስክትገደዱ ሳትቆዩ መግለጽ ትችላላችሁ፡፡ የኔን ማንነት ግን ከኔ ፈቃድ ሳታገኙ በራሳችሁ መግለጽ አትችሉም፡፡

የኢ/ተ/ኦር/ቤ/ክ ጉዳይ ላይ እጃችሁን ከማስገባት ተቆጠቡ፡፡

የዳዊት መዝ ፡ 115 (በሙሉ )

አነሰም ተለቀም ማንኛውም አገር ያሉ መሪዎች ከሰበሰቡት መሳሪያ ጋር ሕዝብን ከሚነዱበት የጸጥታ ኃይል ጋር ይጠረጋሉ፤ መደበቂያም ያጣሉ፡፡

ከላይ የተዘረዘሩትን እርምጃዎች በሙሉ የሰው ዘር ከተፈጠረ ጀምሮ ያላቸው በቅንብር የሚያጠቁ ምንም እረፍት የማይሰጡ እንኳን ለሌላው ለራስ መከላከል የማይችሉ ተደብቆ ሸሽቶ መሸሳ የማያመልጡ ናቸው፡፡

ከላይ የተጠቀሱት አጥፊዎች በምህረት የተሰበሰቡትን ፣ በልዑል የተለዩትን ፣ ምልክት የተደረገባቸውን፣ የድንግል ልጆች፣ የከበሩ የቅዱሳን መላእክት ልጆች፣ ወዳጆች፣ አይነኩም፣ ወደ እነሱም አይደርሱም፡፡

በእግዚአብሔር የተወደዱ የምህረት ወገኖች ፈቅደው በታዛቸው፣ በግቢያቸው ያስጠለሉት ይድናል፡፡

በጉልበቱ፣ በኃይሉ ሊጠለል የፈለገ ደግሞ ከታዘዘለት የሚከፋውን አደጋ ይቀበላል፡፡

ይህ ሁሉ ይደረጋል፣ ይፈጸማል፣ አንዱም አይወድቅም፣ አንዱም አይቀርም፡፡

“ አንድ ማሰታወሻ ብነግራችሁ መልካም ነው፡፡”

ስለ ሰው ልጅ ጥፋትና ክፋት ከልዑል ፊት የተደረገ ሰፊ፣ ረጅም ክርክር ፣ ፍርድ ምህረትና ውሳኔ ፤ እንዲሁ ድንገት የተከናወነ አይደለም፡፡ የአምላካችንን የትእግስት ርቀት የሳየ፣ የእናታችንን ጽናት ያስመሰከረ፣ የወዳጆቻችን የከበሩ መላእክት ለሰው ያላቸውን ፍቅርና ወዳጅነት ያረጋገጠ ነው፡፡

በዓመተ ዓለም ሰው በኖረው ኑሮ ሁሌ እያጠፋ እየተቀጣ መጥቶአል፡፡ የኖህ ዘመንን ማሰብ ፣ የሰዶምን ቅጣት ማሰብ በቂ ነው፡፡ ከዚያም በለይ የተመረጡ ህዝቦች በእስራኤላውያን ለእኛ ትምሕርት ሆነው መጥተዋል፡፡ ሲያምጹ፣ ሲቀጡ፣ ሲጸጸቱ፣ሲማሩ፣ በእነሱ እኛ የፈጣሪን ትግስት፣ ርህራሄ፣ ቁጣ አይተናል፡፡ እንደ ቃሉ ጌታ ዋጋን ሊከፍል መጣ፤ ፈጸመ ፡፡ ለሰው ጸንቶ የቆመ፣ የምህረትና የዘለአለምን ሕይወት እንዲወርስ የቆመ፣በደምና በሥጋው የታተመ ፈቃዱን አጸና፡፡ ዛሬ 2000 ዘመን ሲያልፍ በዚህ የምህረት ቃል ኪዳን ሰው እንዲጠቀም እንደተዘረጋም አለ፡፡

የሰው ልጅ ግን ከእለት ወደ እለት ወንጀሉ ሃጢያቱ እየከፋ መጣ፤ የንጹሃን ደም መፍሰስ ጀመረ ሃጢአት ነገሰ  በፈጣሪ ፈንታ ፍጡሩ ዲያቢሎስ አምላክ ሆነ የፈጣሪ ህግ ተሻረ የዲያቢሎስ ህግ ተግባራዊ ሆነ፡፡

ይህ ሁሉ ልዑል እግዚአብሄር አብ እግዚአብሄር ወልድ እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ በዙፋኑ እየተቀመጠ ዳኝነት ሲሰጥ ቆየ፡፡

መጽሐፈ አስቴርን በሙሉ ያንብቡ

የዳዊት መዝሙር 105 (106) 13 – 40

በዳኝነቱ (በችሎቱ) ሁሉ፤ ድንግል ለሰው ማማለዷን እንባ ማፍሰሷን ታከናውን ነበር፡፡ ቅዱሳን የከበሩ ወኖቹ መላእክትም ሚካኤል፣ ገብርኤል፣ ሩፋኤል፣ ኡራኤል፣ ራጉኤል፣ ሳቁኤል ሁሉ ለሰው ጥፋት በጥብቅና በአማላጅነት ቆመው ጌታ መሃሪ ነውና ፊታቸውን እየተቀበለ ኖሮአል፤ በትንሽ አባታዊ ቅጣት ሲያልፍ ኖረ፡፡ ሰው እንዲጸጸት ንስሃ እንዲገባ ሁሌ ፈቃዱ ስለሆነ ለ2000 ዘመን ታገሰ፡፡ አንድም ቀን የእናታችንን የወዳጆቻችንን ጥብቅናና መማለድ በችሎቱ አላጠፈም ሁሌም እያመመው ትእግስቱን እየፈተነው ኖሯል፤ ታግሷል፡፡

ግን ዛሬ እንኳን ጌታ ጠበቆቻችን ሊከራከሩ፣ ሊማልዱ፣ ሊለምኑ አፈሩ፡፡  ሰው ፈጽሞ ጠፋ በልዑል ፊት የሚቀርብ ቁራጭም መልካም አጣ፡፡  አብርሃም ከጌታ ሲሟገት 50 ጻድቅ ቢኖር ፣ 45 ቢኖር፣ 30 ቢኖር፣ 10 ቢኖር፣ 5 ቢኖር እያለ ምህረት ለሶዶም ሊያመጣ ተሟገተ በዚህ ሁሉ ቁጥር እሺ አለ ጌታ  አንድ ሰው ብቻ ነበርና፤ አብርሃም ምንም ባለመኖሩ ደነገጠ አፉን ያዘ፡፡  ይህም ሆኖ ኖህ በደረቅ ስፍራ መርከብ ሲሰራ ሲያፌዙበት እሚሰማው  አጣ ፤ የልዑል ቁጣ ነዳ ነበርና ከመርከቡ ኖህን ካስገባ ፣ በታዛው የሚጠለሉትን ከሰበሰበ በኋላ፣ በውጭ ዘጋው ኖህን ዝጋ አላለም እራሱ ዘጋው፡፡

ዛሬም እንግዲህ ይህ ሁሉ የድንግል ክርክር፣ ልመና፣ የቅዱሳን የከበሩ መላእክት ልመና፣የቅዱሳን ልመና፣ ሁሉም ሲፈጸም ሲፈቀድ ኖረና ዛሬ ለምህረት የሚያበቃ ቁራጭ ተግባር ሲጠፋ ሁሉም አፉን ከደነ፡፡  አበቃ የሰው ልጅ ስማ፣ የልዑል ልጆች በእምነት ድንኳናቸው ገቡ ከውጪም ልዑል ዘጋው ያንተም ጉዳይ ተደመደመ ተዘጋ፡፡

እጅግ አዝናለሁ ይህን ስል ! ይህን መርዶ ስናገርህ እጅግ ይዘገንነኛል ምን ይደረግ አበቃ ተዘጋ፡፡ በአብርሃም እቅፍ እንዳለው አልአዛርና እንደ ባለጸጋው ሁላችንም ተለያየን፡፡

ቸሩ ፈጣሪ ስለቅን ፍርዱ ይመስገን ይከበር ልዑል ኃያል መካር ጌታ እግዚአብሄር አብ እግዚአብሄር ወልድ እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ የተመሰገነ ይሁን፡፡ ፍርዱን እንደ ፀሐይ ብርሃን የሚያወጣ ጌታ ለዘለአለም ስሙ ይባረክ፡፡ አሜን፡፡

**23 የመጨረሻው ማሠሪያ ቃልና ትእዛዝ**

› የማናቸውም አገሮች ህዝቦች የህዝብ መሪዎች በመላው አለም ተበትናችሁ ያላችሁ የሰው ልጆች በሙሉ፤ በየትኛውም የአኗኗር ደረጃ ላይ ሁኑ፡፡

› ይህ ቃል ለሁላችሁም ከታመነው የልዑል ባርያና ታዛዥ የወጣ፤ በልዑል ፈቃድ የጸና ነውና አድምጡ!

ዓለም እነ ጳውሎስን እብዶች ብላለች ዓለም በልዑል ስም የመጡትን እነማንን ተቀበለች፣ ተሳለቀች፣ አሰረች፣ ገደለች፣ አሳደደች እንጂ ዓለም ለእግዚአብሄር ባለ አእምሮ የሆነን ሰው ለእናንተ እብድ ነው ትላለች፡፡ ስለዚህም ሰምታም አታውቅም፡፡ በመሆኑም ብትሰማም ስማ ባትሰማ አትስማ ! እንዳላችሁት የእብድ ቃል ስለሆነ አንብባችሁ ሳቁበት ተሳለቁበት ! ይመሽ ይነጋ አይምሰልህ በሳቅ በፌዝ የፈጀኸውን ጊዜ በሺህ እጥፍ አብዛኛውና ያ ጊዜ ያንተ የሞት መለመኛ ይሆናል፡፡

› የሰው ዘር ስማ እኔ የነገርኩህን ከራሴ አላመነጨሁም ከፈጣሪ የተነገረኝን እንጂ፡፡ ስለሆነም ከ7/3/1998 ዓ.ም. እስከ 19/7/2001 ድረስ ተነግሮህ አድምጠህ ንቀህ ትተኸዋል፡፡ ዛሬ ይህንን የውሳኔ አፈጻጸም ስትሰማ አሁንም እንደለመድከው ያው ይመስልሃል ንቀህ እምትኖር ያ አበቃ፡፡

ይህ የውሳኔ አጻጻም ከወጣና ከተፈለገው አቅጣጫ መሄድ ከጀመረ ከመጀመሪያው የመድረሻው ቀን ጀምሮ ዓለም የጠረጋውን ምንነት በሁሉም የዓለም ገጽታ በሁሉም የሰው ዘር ኑሮ ዙሪያ ታያለች፡፡ ከዚያች ዕለት ጀምሮ በቁጥር 1 በቁጥር 2 የተጠቀሱት የቅጣት ዓይነቶች ይፈሳሉ፡፡ ማቆሚያ የላቸውም የትኛውም ብልሃት ዘዴ አያቆማቸውም እንዲያውም የሰው ልጅ ትእቢቱን ካጸና እጅግ ታይቶ የማይታወቅ ጥፋት በዓለም ሁሉ ይሆናል፡፡

በዚህ ሰዓት በዓለም ሁሉ ያሉ የአገር መሪዎች ዓለም አቀፍ ድርጅቶች ከነሹሞቻቸው /ከነአገልጋያቸው ግንባር ቀደም ተጠራጊ ይሆናሉ፡፡ ሲነገራቸው አልሰሙም ለወገናቸው አላሰሙምና እንግዲህ የሰው ልጅ ይህን ስነግርህ በተለይ ምንም በማያውቁት ሕፃናት ጉዳት ልቤ ቢከፋም ያንተ የአዋቂው የክፋት ውጤት የጎዳቸው በመሆኑ ላንተ ላላጋጩ ሲያንስህ ነው፡፡ ሕፃናት ቢሄዱም ወደ ጌታ እቅፍ ነው የሰሩት ወንጀል የለምና፡፡

**24. በመጨረሻም፡-**

ማንኛውም የአዳም ዘር በሙሉ አድምጥ !

መልእክት አንድን በ7/3/1998 የወጣውን መልእክት ሁለትን በ27/9/2000 ዓ.ም. የወጣውን በሙሉ እናም ይህንን የአፈጻጸም ውሳኔ መልእክት በሚገባ አንብባችኋል ብዬ አምናለሁ፡፡

ሁሉም እንደተረዳው መጠን አይቶታል፣ የናቀውንም ንቋል፣ የደነገጠውም ደንግጧል፣ የሳቀውም ስቋል ብቻ እንደመሰለው እንደ ተመሰረተበት አይቶታል ፈጽሞም ባያየው ንቆታል፡፡

አሁንም ባበቃውና ባለቀው ሰዓትም ቢሆን ሁሉንም መልእክቶች ከ1፣2፣3 ያሉትን በአንድ ማስታወሻ አካል መጽሔት ቀርቦልሃልና አንብበው ካልፈለግህም ምርጫህ ነው አታንብበው ከድንበርህ የምትዘለውም ተሳደብ አፌዝ እሳት ላይ ቆመህ ነውና ይህን የምታደርገው ለጠፊው አዝናለሁ፡፡

የዳዊት መዝ. 82(83)

ዛሬ በዓለም ምን እየሆነ ነው? የቀደሙት መልእክቶችስ ምን ምልክት እያሳዩ ነው? ታዩ ዘንድ በነሱ ተመስርተው እየተከናወኑ ያሉትን በግልጽ የሚታዩትን እንደ ምሳሌ እንኳ እንይ

› የዓለም ኢኮኖሚ በቀውስ ውስጥ መውደቅ በመልእክት 2 እንደተጠቀሰው

› ሪሴሽን እጅግ መክፋቱ የበጀት ጉድለት እየጨመረ መምጣቱ ስራ ፈት መጨመሩ

› የተፈጥሮ አደጋ እጅግ መበርከቱ

› የምግብ እጥረት ማየሉ፣ የሙቀት መጠን መጨመሩ

› የበረዶ ግግር በአውሮፓ እጅግ መከፋቱ

› በአውስትራሊያ ጎርፍና እሳት በአንድ ሲዘምቱ

› የገንዘብ ቀውስ መቀጠሉ የትላንት ፉከራ ዛሬ ባዶ መሆኑ

እነዚህ ሁሉ የምጥ ጅማሮ ናቸው፡፡ በዘመናችን አዋቂዎችና እንደኛው አገር ተፈላሳፊዎች ችግሮች ሁሉ በመፍትሔ የሚፈቱ ናቸው፣ በእቅድ፣ በዘዴ ማስተካከል፣ የመከላከል እርምጃ በመውሰድ የሚፈቱ ናቸው ባይ ናችሁ፡፡ አይ ሰው አይ የዘመኑ መሪዎች ስልጣን ላይ መውጣት ከማንም በላይ አዋቂ ያደረጋችሁ፡፡

የዘመናችን አዋቂና መሪዎች ጠመንጃ ያጎለበታቸው፣ እንዳሻቸው እንዲናገሩ ያደረጋቸው ናቸው፡፡ በራሳቸውም በሕዝባቸውም የነገ ሕይወት ላይ የሚፈርዱም ናቸው፡፡

› ከዚህ የአፈጻጸም መልእክት መውጣት በኋላ ምን ይከሰታል፡፡ በምልክቶቹ ያልደነገጣችሁ ይህንን ደግሞ ተቀበሉ፡፡

**25. ሀ. የተፈጥሮ ኃይሎች፡-**

› የተለያዩ ስያሜ ያላቸው ማእበሎች ባልታየ መጠን ይመጣሉ ይጠርጋሉ፡፡

› የከበደ ማግኒቲዩድ ያላቸው የመሬት መንቀጥቀጦች ካልጨረሱ አይመለሱምና በተከታታይ ይከሰታሉ ከባድ እሳተ ገሞራዎች ታይተው በማየታወቅ ጉልበታቸው ይወጣሉ ሳይጨርሱም አይቆሙም !

› ታይተው የማይታወቁ ጎርፎች የማያቋርጡ ጠርገው እስከሚጨርሱ የማይቆሙ ይመጣሉ፡፡

› እጅግ የከፋ የበረዶ ክምርና የጉም አፈና የማያቋርጥ ለረጅም ጊዜም የሚቆይ ይመጣል፡፡

› ያልታየ ንፋስ የቀላቀለ የዝናም መጠንና አጣጣል ቶሎም የማያቋርጥ ይጥላል ይጠርጋል፡፡

› እጅግ በጣም ፈጣን የሆነ የጫካ እሳቶች የከተማ እሳቶች ቶሎም የማይጠፉ ይመጣሉ፡፡ እሳቶች የታዘዙትን ሳያጠናቅቁ የማይቆሙ ይሆናሉ፡፡

› ታይተውም ተሰምተውም የማይታወቁ ኃይለኛ አውሎ ነፋሶች ብረቱ ቋጥኝን የሚፈነቅል ኃይል ያላቸው በቶሎ የማይቆም ከተማውንም ገጠሩንም ይጠርጋሉ፡፡

› የከፋ የአውሬዎች ጥቃት በመላው ዓለም ይዘወተራል፡፡ ትንቢተ ሕዝቅኤል 26፡ 8 – 21

› በፍጹም የማያስኬዱ የባህር፣ የውቅያኖስ ማእበሎች የታዘዙትን ስለሚፈጽሙ የማያቋርጡ

በአጠቀላይ እኒህ የተፈጥሮ ኃይሎች እጅ በእጅ ሆነው ባንድነት ባልታየ ኃይላቸው ፍጹም የሚያጠፉ ናቸው፡፡ በሙሉ ጉልበታቸውም ይዘምታሉ፡፡

**26. ለ. የኢኮኖሚ ቀውስ፡-**

› የኢኮኖሚ መጨማደድ እጅግ ይከፋል

› የኢኮኖሚ ቀውስ እጅግ ይከፋል

› የገንዘብ ቀውስ ከአሁኑም እጅግ ይከብዳል

› ያልታየ ያልተሰማ ሪሴሽን

› ያልታየ ያልተሰማ የበጀት ጉድለት

› የመላክና የማስገባት ውድቀት ይመለከታል እጅግም አስቸጋሪ ይሆናል

› የምግብ ችግር እጅግ ይከፋል ረሃብ ያላያቸው ይራባሉ፡፡

› ሰጪ የነበሩ ፍፁም ያጣሉ፡፡ አጥተውም ይለምናሉ

› ብርቱ በሽታዎች ይነግሳሉ እጅግ ብዙ ጥፋት ያደርሳሉ

› ብርቱ ባክቴሪያዎች፣ ቫይረስ ቫይረሶች፣ ታላቅ ተከታታይ ጥፋት ያደርሳሉ የታዘዙትን ሳይፈጽሙ

አይቆሙም

**27. ሐ. የፖለቲካ ቀውስ፡-**

› ሁሉም ይደጉም አይደጉም፣ ይጡም አይጡም፣ ያላቸውም የሌላቸውም ሀገሮች እርስ በእርሳቸው የሀሳብ፣ የፖሊሲ፣የድርጊት፣ የእቅድ አለመስማማት ያነሳሳሉ፡፡ በብርቱም ይጋጫሉ፡፡

› ማናቸውም ዓለም አቀፍ ድርጅቶች እንደ EU, AU, UN, SEATO, LATIN UNITY, ARAB LEAGUE ሁሉም በግጭት ይሞላሉ ማንም ከማንም መስማት መስማማት ያቅተዋል ድርጅቶቹም የመፈራረስ የመዳከም እጣ ይገጥማቸዋል፡፡ ይበተናሉም፡፡

› ማናቸውም እቅዶች ስምምነቶች ይፈርሳሉ፡፡ በተለይም ትልልቅ ነን የሚሉ ሃገሮች ግጭት እጅግ ይከፋል፡፡

›ኃያል የሚባሉ አገሮች እጅግ በከባድ ቀውስ ይቀጣሉ፡፡ ዳግምም አያንሰራሩም በዚያው ያከትማሉ፡፡

› ጦርይት ይነግሳል፣ የሕዝብ ለሕዝብ ፍጅት ይከፋል የሃየማኖቶች ግጭት እጅግ ይከብዳል ብዙም ያጠፋል፡፡

› መሪዎች ይጮሃሉ የሚሰማቸውም ያጣሉ ያደራጁት የጸጥታና የጦር ኃይል አይታዘዝም የመዳከም የመበተንም እጣ ይገጥማቸዋል፡፡ ህዝቦች ለማንኛውም የመንግስት ሃይል አይታዘዙም አይፈሩምም ሕግ የተባለ ሁሉ የሚያከብረው ያጣል፡፡

› ሰላም ስሙ እንጂ ምግባሩና ምልክቱ ፈጽሞ ይጠፋል፡፡

መዝሙረ ዳዊት፡ 78(79) ፡ 6

ከላይ ያሉ አደጋዎች በሙሉ ይከናወናሉ ሰው በሙሉ በመልእክቱ እንደተጠቀሰው መገዛት አለበት እጅን ለኢትዮጵያና ለብርሃናዊ ዙፋናዊ መንግስት እምነቱን ለኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን መስጠት አለበት፡፡ ከዚህ ውጭ የሚመጣ መፍትሔ የለም፡፡ አደጋዎች፣ ጥፋቶች ሁሉ በነጠላ በስፋት የሚቆሙት የሚያልፉት እጁን ለሰጠው ብቻ ነው፡፡

**28. መ. ማህበራዊ ቀውስ፡-**

› ሥራ ፈትነት ታይቶም ተሰምቶም በማይታወቅ ሁኔታ በመላው ዓለም ይሰፍናል፡፡

› ማናቸውም ማህበራዊ አገልግሎቶች በየትኛውም ዓለም ይወድቃሉ፡፡

› የማህበረሰብ ግጭቶች የዘር ግጭቶች በየትኛውም የአለም ክፍል ይሰፍናሉ፡፡ የእምነቶች ግጭት ይከፋል፡፡

›የጤና አጠባበቅ ስርአት ይጠፋል፡፡

› ትራንስፖርት ፍጹም ይበላሻል በየትኛውም አለም መኪና ፣ ባቡር፣ አውሮፕላን፣ መርከብ ሁሉም ለመገልገል ያስቸግራል አደጋቸውም የበዛ ይሆናል፡፡ ለምህረት ያልታደሉትን ለማጥፋት ሞት ሁሉንም መገልገያዎች ወደ መግደያነት ይለውጣቸዋል፡፡

› በየእለቱም የምንገለገልባቸው ሁሉ ለእኛ ማጥቂያ ይሆናሉ፡፡

› ኤሌክትሪክ መገናኛ ግድብ ሁሉም ይወድቃሉ፡፡

**29. ሠ. ወታደራዊ መገልገያዎች፡-**

› ማናቸውም ለፀጥታና ለድንበር ተብለው የተሰሩ ወታደራዊ መሳሪያዎች በሙሉ ከንቱ ይሆናሉ፡፡ የያዝናቸውንም ይዘው ይጠፋሉ፡፡

› ለዚሁ ተብለው የተከማቹ ያከማቹዋቸውም የሚገለገሉባቸውም ሁሉም አብረው ይጠፋሉ፡፡

› ሁሉም ሃያላን ተብዬዎች የሰበሰቡት መሳሪያዎች በሙሉ ጌቶቻቸውን ስለሚበሉ በታላቅ ድንጋጤ

ይዋጣሉ፡፡

› ሁሉም የጦር አዛዥ የኒዩክለር ኬሚካል ባዮሎጂካል፣ ኒውትሮን የታጠቁ ሳተላይቶች ሁሉም ጌቶቻቸውን ይዘው ይጠፋሉ፡፡

መጽሐፈ ሳሙኤል ካልዕ 22፡ 8 – 16

› ዛሬ የምታዩት የጥፋት ምልክት እጅግ በከበደ መጠንና ኃይል ሊጠርጋችሁ ወጥቷል፡፡ በተለይ እናንተ የፖለቲካው መሪዎች ሕግ አውጪ፣ ሕግ ወሳኞች የጸጥታ መዋቅሮች፣ ቢሮክራቶች፣ ተቃዋሚም ደጋፊም ፓርቲዎች፣ ወታደሮች ከነአዛዦች፣ ዳኞች፣ አሳሪ ፈቺዎች፣ የመጀመሪያው የጥፋቱ ሰለባዎች ትሆናላችሁ፡፡ ምንም አይነት የእስትንፋስ ጊዜ አይሰጣችሁም፣ ለማንኛውም ወንጀሎችና ኃጢያቶች ተጠያቂ ናችሁና፡፡ በሂደት የሚበላችሁን ስታዩትና በውስጡ ስትገቡ ልታስታውሱት የሚገባው ይህ ነው፡፡

› ትዳኛላችሁ፣ ትቀጣላችሁ፣ ትታሰራላችሁ፣ ይህም የሚሆነው እንደተሸከማችሁት የሃላፊነት ድርሻ መጠን ነው፡፡ በእናንተ ሃላፊነት ስር ያለውም እንደ ድርሻው መጠን ቅን ፍርዱን ያየዋል፡፡

› ማናቸውም የፍርዱ ሂደቶች ከዚሁ በኢትዮጵያ ይከናወናል፡፡

› በፍቃዳችሁ እዚህ በሚሰየመው ችሎት መቅረብ አለባችሁ፡፡ ይኸውም ቅን ፍርድን በአባታዊ ቅጣትና ምህረትን ለማግኘት ነው፡፡

› ወይም አለመምጣትና አለመቅረብ ነው፡፡ ስለሆነም በዚያው ሆኖ በራሳችሁ ላይ በሕዝባችሁ ላይ በአገራችሁ ላይ የሚፈጸመውን መቀበል ነው፡፡

› በመከናወን ላይ ያሉት የጥፋቶች ምልክቶች እናም መጪው እጅግ ብርቱ ጥፋት ካላጠፏችሁ የማይመለሱ ናቸው፡፡ ስቃያችሁን በማራዘም ሞትን በመንፈግ እንድትለምኑ በማድረግ የሚያጠፈችሁ ናቸው፡፡ መንገድ የለምና፡፡

› አንዱና ብቸኛው መንገድ ራስን ወዶና ፈቅዶ ፍትሕ ላለበት የፍርድ ሂደት ራስን መስጠት ብቻ ነው፡፡ በኢትዮጵያ በሚቋቋመው ፍ/ቤት በኔው በድሃው ጎጆ፡፡

በዚህ በድሃው፣ የልዑል የታመነ አገልጋይ፣ አእምሮው የተቃወሰ እያላችሁ ከምትጠሩት ቅዠታም ከምትሉት፣ እብዱ ቤት ለፍርድ ትቀርባላችሁ ትዳኛላችሁ፡፡

እኔ ምንም በሉኝ የፈሊጋችሁትን ስያሜ ስጡኝ አዎን ነኝ !

ስድብ ትችት ነቀፋ ልብሴ ናቸውና ጎስቋላ ነኝ፣ አቧራ ብናኝ ነኝ፣ ማንም ቁም ነገር የሚለኝም አይደለሁም፣ አዎን ነኝ መቼስ አይደለሁም አልኩና የምትሉትን ሁሉ ነኝ እርካታ ይስጣችሁ እንጂ ለእኔ ጭንቄ አይደለም፡፡ እውነቱ ግን ሌላ ነው ልብ በሉ በዚህ ድሃና ሃጢያተኛ ላይ የእግዚአብሄር ፀጋና ኃይል ሲጨመርበት ግን ከአእምሮአችሁ በላየ ከምታስቡትም ውጪ ይሆናል፡፡ ይህም ነው እየተከናወነ ያለው፡፡ ለእናንተ ከንቱ ብሆንም ለሠራዊት ጌታ እግዚአብሄር ግን የሚወደኝ ልጁ ነኝ፡፡ ፈጠረኝ፣ አሳደገኝ፣ በእድሜዬ ሁሉ መራኝ፡፡

መጽሐፈ ሳሙኤል ካልዕ 23፡ 2 – 7

በበረሃውና በእሳቱ አሳለፈኝ፡፡ ሰው ሊገምተው ከሚችለው በላይ በሆነ ሰቆቃ ባልወድደውም ፈቃዱ ነበርና በዚያም ውስጥ ሞትን ጓደኛ አድርጎ አሳለፈኝ ዝርዝር ታሪኩን ልተወውና፡፡

ዛሬ የማደርገው ሁሉ በተሰጠኝ ትእዛዝና ፈቃድ ብቻ መሆኑን ልታውቁት ይገባል፡፡

በቀደሙት ሁለት መልእክቶች ብዙም ስለራሴ የገለጽኩት ባይኖርም ዛሬ ግን በአባቴ የፈቃድ በመሆኑ ለአምላኬ ምን እንደሆንኩ ታውቁ ዘንድ በመጠኑ እገልጻለሁ፡፡

ከሁሉም በላይ ግን አንድ ቁም ነገር ልታውቁ ይገባል፡፡ ይኸውም ማንኛውም ሰው በሱ ፊት እኩል መሆኑን ነው፡፡ የተከፈለውም የሃጢያት ዋጋ ለሁሉም የሰው ዘር የተደረገ የፍቅር ዋጋና መስዋእት ነው፡፡ ልዩነቱ ያለው ግን በኛ ፈቃድ ላይ ነው፡፡ በፍጹም ልባችሁ ነፍሳችሁና ሃሳባችሁ ካመናችሁትና ከወደዳችሁት የምትወዱዱ ልጆቹ ናችሁ፡፡ እውነቱም ይህ ነው፡፡

ከላይ እንዳላኩት እኔ ታናሹ ልጁ የልዑል ባሪያ፣ የሥላሴ ባሪያ፣ የድንግል ባሪያ፣ የአምላኬን በጎች እጠብቅ ዘንድ በመልካምም ሥፍራ አሳርፍ ዘንድ ባባቴ የታዘዝኩ ነኝ የት ድረስ ነው ስልጣንህ ትሉ ይሆናል፡፡ ልዑል ነው ያዘዘኝ የሚመራኝ ምድሪቱም በኔው በትንሹ በሃጢያተኛው በሥላሴዎች በተወደደው ባሪያ ትገዛለች ትመራለች፡፡ እኔ ለበጎች እኖራለሁ፡፡ ለቀበሮች ደግም ሞታቸው ነኝ፡፡ ቀሪ ሕይወቴ ለአባቴ ክብር ቃልና ፈቃድ መፈፀም መስዋእት መሆን አለበት፡፡ እኔም እንግዲህ ይኸው ነኝ ከኔ ከባሪያው ጋር አብረው የሚከብሩ እጅግ የተወደዱ፣ የተሾሙ፣ የተቀቡ፣ የታመኑ ሁሉ በተፈቀደው ሰአት ወደብርሃኑ ማማ ይወጣሉ፡፡ ዛሬ በየትም ተጥለዋል፣ በየደጁ ወድቀዋል በረሃብ ጠውልገዋል፣ በሰው ተንቀዋል እንደ ውሻ ተቆጥረዋል፡፡ ወንጌልን በጨበጡ ተተፍተዋል ተስቆባቸዋል፡፡ ከሃዲዎች መጫወቻ አድርገዋቸዋል፡፡ በአባታቸው ቤት ባይተዋር ሆነዋል፡፡ ይህ ግን አበቃ፡፡ የዳዊት መዝ፡ 149

የልዑል ልጆች ከውርደት ወደ ክብሩ ማማ ሊወጡ በተወደደ አንደበታቸው ባማረ እግራቸው ምድሪቱን በአምላካቸው ቃል ሊያረሰርሱ ይገባልና ይሆናልም፡፡ ማነው የሚነካቸው ማነውስ የብረሃን ልጆቹ ፊት በክፋት የሚቆመው በቃ ! ኢዮብ 5፡ 17 – 2

የተዋህዶ ኦ/ቤ/ክ ጉዳይ ላይ እጃችሁን ከማስገባት ተቆጠቡ በውስጧም የሰገሰጋችኋቸው የምን ጉዳይ ይሁን የምን ሰራተኞቻችሁን /ለእናንተ የስጋ ስራ የተሰማሩትን/ አስወግዱ

› ቤተክርስቲያን በተመለከተ የሚቀጣት እግዚአብሄር ነው

› አንድም ሰው እንዲነካት ሙብት የለውም፡፡

› ተዋህዶ እምነት ላይ የማይዘምት ማን አለ?

**በእምነት መስመር ያሉ**

በአገራችን ያሉ፡- ካቶሊክ፣ ሙስሊም፣ ፕሮቴስታንት ሌሎችም

በውጪ ያሉ ፡- ካቶሊክ፣ ሙስሊም፣ ፕሮቴስታንት፣ ሂንዱም፣ ቡዲሂስቱም ሁሉም ተቋም ቀስቱ

በኢትዮጵያ ተዋህዶ ኦርቶዶክስ ቤ/ክ ላይ ነው፡፡

በመንግስት መስመር ያሉ፡- የራሴው መንግስት እናንተና በኢትዮጵያ ጉዳይ ሁሌ የሚታመሙት

**የውጭ መንግሥታት በሙሉ**

› በውጭ ያሉ አለም አቀፍ ድርጅቶችና ተቋሞች በሙሉ ዘመቻቸው በኢት. ተዋህዶ ቤ/ክ ሌ ነው፡፡

› በነዚህ በውጭ የሚደገፉ የአገር ውስጥ የተለያዩ ተቋሞች ዘመቻቸው በኢት. ተዋህዶ ቤ/ክ ሌ ነው፡፡

ሁሉም ከአያት ቅድመ አያቱ የወረሰውን ተዋህዶን የማጥፋት ዘመቻ ሲፈጽምና ሲያስፈጽም እንጂ ሲጸጸት አላየንም፡፡ ዲያብሎስ አለምን ይነዳል የምንለውም ለዚህ ነው፡፡ አለም በሙሉ የሱ ታዛዥ ነው፡፡ የኛም መንግስት የት እንደቆመ ስለምናውቅ የማን የዘመቻ ምድብ ውስጥ እንዳለ ጠንቅቄ የማውቅ ነኝና ተጠንቀቁ፡፡

ማንም እምነቴን ሊቀጣ አይችልም፡፡

ቤቱን የማጸዳው እኔው ልዑል ባሪያ ነኝ፡፡ ሌባም ይሁን ቀጣፊ፣ ተኩላም ይሁን ምን፣ በኦት.ተ.ቤ.ክ ውስጥ ያለውን ሁሉ ችግር የሚፈታው በራሱ በፈጣሪዋ እንጂ ሥጋ ዳኛ ሙብት የለውም፡፡ ደግሜ እላለሁ በዚህ በአባቴም ቤት በእናቴ ቤት በወዳጆቼ ቤት የሚደረገው ጥፋት አይሆንልኝምና አልራራም፣ አልምርምም፣ደጋግሜ የማስጠነቅቀው ለዚህ ነው፡፡

ስለዚህ ከቤ/ክ መሪ እስከ አገልጋይ ስር ድረስ ያሉትን በሙሉ ማንም ውስጧ እንዳይገባ፡፡

› ቤ/ክ ተዘመተባት እንጂ በማን ላይ ወጣች? ቤ/ክ፣ ገዳማት፣ ተቃጠሉባት እንጂ የማንን እምነት ማምለኪያ ነካች፡፡

መዝ፡ ዳዊት፡ 95 ( 96 ) 13

› መነኮሳትም፣ ባህታውያኗ፣ አገልጋዮችም፣ ተፈጁ፣ ተሰዉ፣ ተቃጠሉ እንጂ እሷ ማንን ነከች፡፡ ጅማ፣ አሰቦት ገዳም፣ ጅጅጋ፣ ሐረር ፣ ድሬዳዋ፣ ወሊጋ፣ ሁሉም ምስክር ናቸው፡፡ ነገ ቅድሚያ በፍርድ ወንበር የማየው ይህንን ነው፡

ከአህዛብ እምነት ጋር የኢ/ኦ/ተ/ቤ/ክርስቲያንን እምነት በመደመር የምትወነጅሉ የመንግስት ተቋማት ነገ በምንም መልኩ አትታለፉበትም ፈጥናችሁ ታረሙ፡፡

› ማንኛውም በኢትዮጵያ ውስጥ ያለ የእምነት ሰው ሊያውቅ የሚገባው ቢኖር መጪው አደጋ ከፊቱ የተደቀነው ፈታኝ እሳት ቀላል አይደለም፡፡

ከመሪ እስከ ተመሪ ያለ ሁሉ ይፈተሻል ማን ያመልጣል? ማንስ ይሻገራል? አዎ በቀደምቶቹ መልእክቶች እንደተጠቀሰው ቅን፣ የዋህ፣ ትሁት፣ ፈጣሪውን የሚፈራ ሰው ይሻገራል፡፡

› ማንኛውም የተዋህዶ እምነት ተከታይ እንደቃሉ እየኖረ መሆኑን ይመርምር፡፡

› ተመሳስሎ ማለፍ አይቻልም የሚፈትሽህ የሥጋ ዳኛ እንዳይመስልህ የእግዚአብሄር መንፈስ እንጂ ይህ ምስክር በእሳት እያለፉ ለሚወጡት የሚመለከት ነው፡፡

› ወጣቶች

› ሴት ወጣቶች እጅግ ታላቅ ቁጣ በእናንተ ላይ ነው ምንዝርናን፣ ቅጥፈትን፣ ውሸትን፣ ሱሪ መወተፍን፣ ራቁት መሄድን እጅግ የከፋውን ስራ ሁሉ እየሰራችሁ ስላላችሁ ለእናንተ የሚመጣው እሳት እጅግ ከባድ ነው፡፡

› ወንዶችም እንዲሁ አመንዛሪ፣ ቀጣፊ፣ ውሸታም፣ ሌባ፣ እናት አባታችሁን የናቃችሁ፣ ታላቅ ማክበርን የማታውቁ፣ ስለሆናችሁ የእናንተም እጣ በታላቅ እሳት መበጠር ነውና ተዘጋጁበት፡፡

› ተዋህዶ እምነት የምትከተሉ ወጣቶች ለእምነት መቅናት ጥሩ ነው እምነቱን በተግባር መግለጽ ግን መሰረታዊ ግዴታ ነው፡፡ ስለዚህም ከምንዝርና፣ ከውሸት፣ ከሌብነት፣ ከመጥፎ ሱሰኝነት፣ ሰው ከመናቅ፣ ከማዋረድ፣ ከመጥፎ ተግባሮች ሁሉ ራቁ በእምነቱ ስም ንግድ የምታካሂዱ ሁለገብ የእምነት ነጋዴዎች እጣችሁ እጅግ መጥፎ መሆኑን እወቁ፡፡

30. **ማጠቃለያ፡-**

ባለአእምሮ ነኝ፣ አስተዋይ ንኘ፣ አዋቂ ነኝ፣ ሁሉንም እምመዝን ነኝ፣ የምትል የሰው ዘር በሙሉ አድምጥ ስማ፡፡

ምድርና ሰማይን የዘረጋ አምላክ ባርያ እኔ የሥላሴ ባርያ ለእናንተ ደግሞ እብዱ፣ በሽተኛው፣ አእምሮውን የተነካ ነኝ፡፡ አዎ ነኝ፡፤

የዳዊት መዝ፡ 123(124)

አባቴ ባከበራቸው፣ በወደዳቸው፣ በሾማቸው፣ በቀባቸው፣ አገልጋይ በጎቹ ላይ እስከዛሬ ያላገጣችሁ ሁሌ በኔ ፊት እንደማትማሩ እንድታውቁ እፈልጋለሁ፡፡ ምህረትን የምትለምኑት ከገፉችኋቸው የልዑል ልጆቸ ነው፡፡ እነሱ ሲምሩአችሁ እምራለሁ አለበለዚያ እናንተን የበግ ጸሮች አላልፍም እንግዲህ እኔ ይህ ነኝ በየትኛውም አለም ኑር ሂድ የምታገኘው እኔኑ የሥላሴ ባሪያና አገልጋዩን ነው፡፡ እምዳኝም እኔው ነኝ በቃ እወቁት የኢትዮጵያን ክብር

እወቁት የእምነት አርበኞቹን አገር እወቁት የብረሃን ፍርድ ምን እንደሚመስል ተረዱት ባታምኑም እውነቱ ይህ ነው፡፡

ስለኔ በመጠኑ ተረድታችኋል ብዬ እገምታለሁ ስንተያዩ ደግሞ ይበልጥ ሁሉም ይገለጣል፡፡ ለዘመናትም በእድሜዬ ስኖር ይህ የአባቴ የፈቃድ ሚስጥር በውስጤ ተሸፍኖ ኖሯል፡፡ ዛሬ ጫፉን ገልጫለሁ ቀሪውን ድግሞ በጊዜው ታውቁታላችሁ፡፡

መጽሐፈ ነገሥት ቀዳማዊ መዕ፡ 18 በሙሉ

እንግዲህ ይች ለእናንተ ለክፉዎች መጥፋት የምትተጋው ምድርና ባህሪዋ፣ ለልዑል ልጆች፣ ለድንግል ልጆች፣ ለከበሩ መላእከት ወዳጆች መጥፋት የምትተጋው ምድር ከቅጣት በኋላ ለሁሉም የእግዚአብሄር በጎች በረከቷን ትሰጣለች፡፡ ደስም በሏት ታደረገዋለች፡፡ ለሁሉም የልዑል ደስታ ደስታዋ ነውና፡፡ ጠላት ደግሞ ከናንተው ጋር ወደሲኦል መኖሪያው ይካተታል፡፡ ምድር ከክፉዎች፣ ከጠማሞች፣ ከተኩላዎች፣ ከቀበሮዎች፣ ከእባብ፣ ከጊንጦች፣ ከዘንዶዎች ትጸዳለች፡፡

**31. ትእዛዝ !!**

1. አንድ ነገር ላስታውስ በምድሪቱ ሕግ ንጉሥ፣ ፐሬዚዳንት፣ ጠ/ሚኒስትር፣ ጀነራል፣ ሚኒስትር፣ ዳኛ፣ አቃቤ ሕግ ወ.ዘ.ተ. ሁሉም በተሰጠው የስልጣን ክልል የመወሰን አቅም አለው፡፡ የወሰነውንም ውሳኔ ሕጉ በሰጠው የስልጣኑ ክልል ይወስናል፡፡ ተፈጻሚም ይሆናል፡፡ ያስራል፣ ይገላል፣ ያሳድዳል፣ ይወርሳል፣ ያሰቃያል፣ ይሰውራል፣ ወዘተ...

መሪም ከሆነ ጦርነት ያውጃል፡፡ ታዲያ ማን ስልጣን ሰጠህ ቢባል፣ ሕዝብ መረጠኝ፡፡ ባለው ሕገ መንግሥትና ሕግ በሰጣኝ ስልጣን ወሰንኩ የሚል መልስ ይመጣል፡፡

የአለም ገዢ መልሱ ይህ ነው፡፡

ወደኔ ስንመጣ ግን ማን ስልጣን ሰጠህ ስልጣንህስ የት ድረስ ሃይል አለው? የመሳሰለው ጥያቄ ይነሳል፡፡ ዋጋም ተሰጥቶት ላይነሳ ይችላል፡፡ ይሁንና ለሚያየው ይህ ነው መልሱ፡፡ የኔ ስልጣን ምድርና ሰማይን ከዘረጋው ፈጣሪ የተሰጠ ነው፡፡ እናንተንም በሚነቅል፣ በሚተክል ጌታ የምታመን ነኝ፤ የምጠበቅም ነኝ፡፡

ሁሉን የፈጠረ ጌታ አገልጋይና ባሪያ ነኝ፣ የተወደድኩም ልጅ ነኝ ስለዚህ በስሙ ያመንኩበትን ከሱ የታዘዝኩበትን ሁሉ ትእዛዝ እገልጽ ዘንድ ስልጣኑ አለኝ፡፡ ከእናንተ ከዲያቢሎስ አባታችሁ የአገኘሁት ስልጣን አይደለም፡፡ ሁላችሁንም ከፈጠረ፣ ከሚሸር፣ ከሚያጸና፣ የሁሉ ፈጣሪ የተሰጠኝ ስልጣንና ሙብት ነው፡፡

ትንቢተ ኢሳኢያስ ም፡ 43 በሙሉ

2. በቀደሙት ሁለት መልእክቶችና በዚህ በሶስተኛው የአፈጻጸም ውሳኔ የተገለጡት ቅጣቶች በሙሉ በመላው አለም ተፈጻሚ ይሆናሉ፡፡ ማንም የሰው ዘር ከዚህ ውሳኔ ውጪ አይሆንም፡፡

› ስለዚህ በአባቴ

በፈጣሪዬ ስም ይህን ትእዛዝ ተፈጻሚ እንዲሆን አጽንቻለሁ፡፡

3. በፈጣሪዬ ስም አዛለሁ ሁሉም ቅጣቶች ሲሆኑና ሲከናወኑ እኔ የአምላኬን ምህረትና ፈቃድ እስካልጠየቅሁ ድረስ እንዳይቋረጡ ወስኜአለሁ፡፡ የአምላኬንም ፈቃድ ጠይቁ አስወስኜበታለሁ፡፡

4. መሪም ተመሪም፣ የእምነት መሪም ተመሪም፣ ነገሥታትም የጦር አለቆችም በምድረ ስልጣን አለን የምትሉ ሁሉ ከአገሬ መሪ ጀምሮ እግዚአብሄር በቀባቸው ልጆቹ ፊት አምናችሁ አለምንም ቅድመ ሁኔታ እስክትንበረከኩና የፈጣሪን ልጆች ክብር ልክ እስክታውቁ ድረስ ምህረት አይኖርም፣ የስትንፋስ ጊዜ የለም፣ የመትረፍ እድል የለም፣ ሞትንም በቀላሉ ማግኘት አይቻልም፡፡ ትእቢታችሁ ሙልጭ ብሎ እስከሚጠፋና ከንቱም መሆናችሁ እስክታውቁ ድረስ መጠኑን እያከበደ የሚሄደው ጥፋት አይገታም ፈጽሞ ታዟልና፡፡

ትንቢተ ኢሳኢያስ ም፡ 45፡ 9 – 25

5. በማናቸውም የልዑል ልጆች ላይ የሚቃጣ የጥፋት ሀሳብና እቅድ ገና ሲታሰብ የሚጠረግ መሆኑን የዚህ ሃሳብ አመንጪ፣ አቃጅ፣ አዛዥ ምንም እድል የማይሰጠው መሆኑን በተጨማሪ ተወስኗል፡፡

6. የፈጣሪ ፈቃድ ሐሳብ፣ ትእዛዝ፣ ውሳኔ፣ ምክር ግሳጼ ሁሉም በዚህ የመጨረሻው ሰአት በኔ በታመነ አገልጋዩ በባሪያው ተገልጾአል፡፡ በመሆኑም አንድም ሳይቀር ተፈጻሚ ይሆናል፡፡ እንዲሆንም ታዟል፡፡

7. ማናቸውም ሚዲያዎች፣ ፕሬሶች፣ መጽሔቶች፣ ጋዜጦች፣ ዌብ ሳይቶች፣ ኢንተርኔቶች፣ ፋክሶች ሁሉም የፕሮፖጋንዳ መሣሪያዎች፣ በመላው አለም እራሳቸውን አንሰራፍታችሁ ያላችሁ ሁሉ ይህንን መልእክት ሳትጨምሩ ሳትቀንሱ አስተላልፉ ለሕዝብም ግልፅ አድርጉ ይህንን የማያደርግ ማንም ይሁን ማንም በየትኛውም አለም ይኑር ፍፁም በእሳት ይበላል፡፡ የተረፉትም ለፍርድ ይቀርባሉ፡፡ ያለምህረትም ቅጣት ይቀጣሉ፡፡ መልእክቱን በአግባቡ ካስተላለፉ ደግሞ ታዘዋልና በምህረት ታያሉ፡፡

8. ሁላችሁም የታመናችሁ የአባቴ ልጆች የኢትዮጵያ ተ/አ እውነተኛ ልጆች በየትኛውም አለም ያላችሁ የልዑል ልጆች በሙሉ ይህንን ልታውቁ ይገባል፡፡

ሀ/ ከፈጣሪ ጋር የራሳችሁ ግንኙነት እንዳላችሁ አምናለሁ፣ ስለዚህ በሰው ሁሉ ፊት መብራታችሁ የበራ ይሁን በየእለቱ በቅድስና ተግባራችሁን ተወጡ፡፡

ለ/ ቅን፣ ታማኝ፣ ትሁት፣ ከአለም ጉድፍ የራቀ፣ ከስሜታዊነት የጸዳ፣ እውነተኛ ሁሉንም በፍቅር የሚያይ በማናቸውም የሥራ ዘርፍ የተጋ፣ በሁሉም ኃላፊነት የታመነ ሁኑ፡፡

ሐ/ ለፈጣሪዬ ፈቃድ ትእዛዝና ቃል ትጉ፣ አትፍሩ፣ በጠላት ፊት በጥንካሬ ቁሙ፡፡

9. በመላው አለም ለምትገኙ የየትኛውም ተዋረድ ባለሥልጣኖች በሙሉ ሁሉም የፖለቲካ መሪዎች ሁሉም ባለስልጣኖች፣ የሁሉም ዘርፍ የእምነት መሪዎች፣ የጦር አለቆች፣ የፀጥታ ሃላፊዎች፣ ዳኞች፣ ጠበቆች፣ አቃቢ ሕጎች ፣ ባለሃብቶች፣ በከፍታም በዝቅታም የምትገኙ የጥፋት ሠራተኞች በሙሉ ይህ ትእዛዝ ተፈርሞ ከወጣበት ጊዜ ጀምሮ የልዑል የቅጣት እጅ በሙሉ ሃይሉ መለቀቁን እናም እናንተን ማሳደድና ማጥፋት እንደሚጀምር እወቁ፡፡ ይህም በልዑል ሥም ታዟል ማንም ሊያመልጥ አይችልምና፡፡ እኔም በአባቴ ስም በፈቃዱ መሠረት አጽንቼዋለሁ፡፡

ለ/ ለጥቂት ጊዜ በሥልጣናችሁ ብትቆዩ እንኳን በዚያው ትዘልቃላችሁ ማለት አይደለም፡፡ በተፃራሪው ማናቸውም የታዘዙ ጥፋቶች ሁሉ በናንተ ላይ ተፈጻሚ እስከሚሆኑ ብቻ ነው፡፡

ሐ/ከዚህ ትእዛዝ መውጣት እለት ጀምሮ የማንኛውም አገር ባለሥልጣን በየትም አለም ያለ ገዥ ሁሉ ስልጣኑ ከንቱና የማየሰራም ተደረጓል፡፡ እንዲሆንም በአባቴ ስምና ፈቃድ መሠረት አጽንቼዋለሁ፡፡

መ/ ማናቸውም ሃላፊነትና ሥልጣኖች በሙሉ በየትኛውም የአለም ክፍል እውንና ዘላቂ ሥልጣን የሚሆነው አባቴ ሲፈቅድ በስሙም እኔ በሪያው ትእዛዙን ፈርሜ ወጪ ሳደርግ ብቻ ነው፡፡ ከዚያ ውጪ የምድር ባለሥልጣን ሁሉ ሥልጣኑ በፈጣሪ አምላኬ ትእዛዝ ተሽሮአል፡፡ እኔም የልዑል ባሪያ በፈጣሪዬ ፈቃድና ስም መሰረት አጽንቼዋለሁ፡፡

› በዚህ አፈጻጸምና በቀደሙት መልእክቶች የተጠቀሱት ማናቸውም መቅሰፍቶች ምድር ላይ የሰፈነውን ጨለማና ስርአቱን ፈጽሞ ጠርገው እስከሚያጠፉና በምትኩ የፈጣሪ ፈቃድና ትእዛዝ እንዲሁም ውሳኔና የብርሃን ስርአት እስከሚሰፍን የሚወርደው የቁጣ እሳትና በትር እንዳይቆም የሰውም ትእቢት ፈጽሞ እስከሚጠፋ እንዲቀጥል እኔ የልዑል ባርያ፣ የሥላሴ ባርያ፣ የድንገል ባርያ፣ ምድርና ሰማይን የዘረጋው አባቴ የሠራዊት ሁሉ ጌታ እግዚአብሄር በሰጠኝ ስልጣንና ሃላፊነት መሠረት በፈቃዱና በስሙ ተፈጻሚ እንዲሆን እኔም በከበረው ስሙ ወስኜአለሁ፡፡

ሠ/ በአባቴ ስም በልዑል ስም የማጸናው ጊዜያዊም ሆነ ዘላቂ ሹመት ሁሉ በየትኛውም የአለም ክልል ተፈጻሚ ይሆናል፡፡ ይህ በሚጸናበት ሥፍራ ሁሉ ሁሉም ነገር ሰላም ይሆናል፤ በረከቱን. ቸርነቱን ሁሉ አባቴ ያፈሳል፡፡ በእውነት የፀናች የጌታም የብርሃን አገዛዝ ትሰፍናለች፡፡ ከዚህ ውጭ ከፍም ዝቅም የሚል ነገር የለም፡፡ ያኔ ብቻ ነው እጅግ የጤሰውና የነደደው የልዑል የሠራዊት ጌታ እግዚአብሄር ቁጣ መስከን የሚጀምረው፡፡ ከዚህ ውጪ የሚጨመር የሚቀነስ ነገር የለም፡፡

አበቃ በእርግጥ ተረዱ አበቃ !! ማንም ከላይ ከተጠቀሱት ትእዛዞች ውጭ ሊሆን አይችልም ቢሞክርም በእሳት ይጠረጋል፡፡

› አባቴን ፈጣሩዬን ለኔ ሁሉም የሆነውን አምላኬን አመሰግነዋለሁ

› ለእናቴ ለድንግል በውጣ ውረዱ በሕይወቴ ሁሉ ያልተለየችኝን ከልቤ አመሰግናታለሁ፡፡

› ለወዳጆቼ እጅግ ለምወዳቸውም ፈጥነው ለሚያደምጡኝ እንደ አይናቸው ብሌን ለሚጠብቁኝ ሊቀ መላእክት ገብርኤል፣ ሊቀ መልእክት ሚካኤል፣ ሊቀ መላእክት ሩፋኤል፣ ሊቀ መላእክተ ፋኑኤል፣ ሊቀ መላእክተ ራጉኤል፣ ሊቀ መላእክት ኡራኤል ሊቀ መላእክት ሳቁኤል ለከበሩ የብርሃን መላእክት ሁሉ ምስጋናዬን ከልብ አፈሳለሁ፡፡

› ለአባቶቼ፣ ለእናቶቼ፣ ለወንድሞቼ፣ ለእህቶቼ ፣ ለልጆቼ የአባታችን፣ የእናታችን የወዳጆቻችን በረከት ቸርነት፣ ጥበቃ ፈጽሞ አይለያችሁ፡፡ የልዑል የሠራዊት ጌታ እግዚአብሄር ልጆች ጽኑ፤ አይዟችሁ ይኸው የተጠበቀው ሰአት ደረሰ፤ በጸሎት በጾም ትጉ ሁሉን ለሚያውቅ አባታችን ሸክማችሁን ሁሉ ንገሩ አሳርፉ በአመጽ ውስጥ አትግቡ ስራው ሁሉ የእግዚአብሄር ነውና የሥጋ ድጋፍ አይፈልግም፡፡

የአብርሃም አምላክ፣ የይስሃቅ አምላክ፣ የያእቆብ አምላክ የባርካችሁ፡፡ አሜን፡፡

ከታመነው ከተወደደው የልዑል ባርያና አገልጋይ<br>
ከታመነው የድንግል ልጅ<br>
ከታመነው የከበሩ መላእክቶች ወዳጅ

ተፃፈ -----------------

ቀን 19/7/2001 ዓ.ም.

# አመሰግናለሁ፡፡

ቀን፡ 01 - 06 – 2002 ዓ. ም

ለመላው ህዝበ ክርስቲያን የተዋህዶ ልጆች በሙሉ!!

## በተዋህዶ እምነታችሁ በጽናት ለቆማችሁ በመላው አለም ፊት ለተበተናችሁ ሁሉ!!

በዛሬው መልእክት ውስጥ ስለምታገኙት ከማንሳቴ በፊት ላሳስባችሁ የምወደው ጉዳይ አለ፤ አውነተኛይቱ የተዋህዶ እምነት ከሌላው ሁሉ ከሚለያት እጅግ ብዙ ንገር ዋነኛው በተግባር ሁሌም የሚገለጸው የእምነቱ ጽናት ነው፡፡

> እምነት ተስፋ ስለምናደርገው ነገር የሚያስረግጥ የማናየውንም ነገር የሚያስርዳ ነው፡፡ ለሽማግሌዎች የተመሰከረላቸው በዚሁ ነውና፡፡ ዓለም በእግዚአብሄር ቃል እንደተዘጋጁ ፣ ስለዚህም የሚታየው ነገር ከሚታዩት እንዳልሆነ በእምነት እናስተውላልን፡፡ ዕብራውያን ፲፣ 1 – 3

ያለ እምነት ምንም አይነት መንፈሳዊ ትርፍም የለም፡፡ እምነትስ ከሌለን እንዴትስ ከእግዚአብሄር የተሰጠንን ተስፋና ስጦታ እንቀበላለን፡፡ እግዚአብሄር የሰጣቸውን ተስፋ አባቶቻችን በእምነት ተቀብለውም አይተውትም አለፉ በነሱም የእምነት ጽናት ፈጣሪችን ተደስቶበታል፡፡ ያለ እምነት ፈጣሪን ማስደሰት አይቻልምና! ሞትን የሚያህል እዳ ሄኖክ ሳይቀምስ የለፈው በእምነቱ ፈጣሪን ስላስደሰተ ብቻ ነው፡፡ በታመነው ቸሩ ፈጣሪ ለበጎው ቀን የታተማችሁ አባቶቼ እናቶቼ፣ ወንድሞቼ እህቶቼ፣ እንዲሁም ልጆቼ፤ ከ4 አመት በላይ የእግዚአብሄርን ፍርድ፣ ተስፋ ለታመኑ ልጆቹ የሰጠውን ተስፋ በተከታታይ በወጡት መልእክቶች አይታችሁአል፡፡ መልእክቶቹ ሁሉም የሰው ዘር ያምነዋል ተብሎ አልማጣም፡፡ ለጥቂቶቹ ለተመረጡት በስጋ አይን የማያዩትን በእምነት ግን አጥርተው ለሚያዩት የተሰጠ የልኡል ድምጽ ነው፡፡ ስልሆነም ነው በዛሬው መልእክቴ መግቢያ በተግባር ስለሚገለጥ እምነትላሳስባችሁ የፈለግሁት፡፡ ( የዛሬውንም የተቀደሙትንም መላእክቶች ሁሉ አንብባችሁትም ሆነ ሳታነቡት አስቀድማችሁ ታላቅ የእምነትን ምንነት አስረጅ የሆነውን የእግዚአብሄር ቃል ወደ ዕብራውያን ምዕራፍ ፲ በሙሉ አንቡት)፡፡ እጅግ ብዙዎች በመልእክቱ ተሰናክለዋል፡፡ በቁጥር ቢያንሱም ጥቂቶች ደግሞ አትርፈዋል፡፡ ምኞቴ ሁሉም የሰው ዘር በእግዚአብሄር የሚገኘውን በረከትና ህይወት ቢያተርፍ ነበር፡፡ አልሆነም አንጂ!! በመላው አለም ከተበተነው የሰው ዘር ኢትዮጵያውያን የተዋህዶ ልጆች በዚህ የመጨረሻው ፈተና ዘመን ከአባቶቻችን እምነት በረከት በሰነቁት ስንቅ ባለ ድል ሆነዋል፡፡ ሌሎች ግን በስጋ እውቀታቸው ፣ በሃብታቸው፣ በጥበባቸው ሲለኩ፣ ሲፈተሹ፣ ሲተነተኑ፣ የተዘጋባቸውን መንፈሳዊ ጥበብ በዲየብሎሳዊ መነጽራቸው ሊያዩ ሲሞክሩ ተሰናክለው ቀርተዋል፡፡ ወገኖቼ በአለም አይን አትዩ እግዚአብሄር በቸራችሁ የእምነት መንፈሳዊ ዐይን እንጂ! በዚህ መልዕክት ብዙ አይነት ትችቶች፣ ስድቦች፣ ሽሙጦችና ቀጥተኛ ተቃውሞዎች ደርሰዋል፡፡ ለእውነታችን መለኪያውም ይህው ዲየብሎሳዊ ዘመቻ ነው፡፡ እንግዲህ የሁሉም ነገር ማብቃት ወደ ጽሁፉ ስትገቡ ስለምታረጋግጡት፣ ለውሾች ይህንን ብርሃን ተስፋን አብሳሪ ቃል አትበትኑ፡፡ የቀደሙት መልእክቶች ለሁሉም የሆነው ተፈረደበትም ፍርዱን እንዲያውቅ፤ የተጸጸተም በንስሃ እንዲመለስ፣ ባለድሉም በእምነት ትርፉ ፈጣሪው የቸረውን አስገራሚ ጸጋ ሊያፍስበት ነው፡፡ ስለሆነም የልዑል ብሩካን በሁሉም ነገር ዝግጁ ሁኑ፡፡ ጊዜ ስለሌለ መልእክቱን ይደርሰው ዘንድ ይገባል ብላችሁ ላመናችሁበትና ቅዱስ የእግዚአብሄር መንፈስ እንዳሳሰባችሁ ልክ ለየዋህ፣ ቅን ደግ፣ ቸር ለሆነ የእግዚአብሄር ወገን በፍጥነት አድርሱ፡፡ ይፍጠን ያልኩት ጊዜው በማልቁ መሆኑን ተረዱ፡፡ መልካም የመረዳት ንባብ!!

በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ አኀዱ አምላክ አሜን

ለመለው የኢተዮጵያ ተዋህዶ ቤተ ክርሰቲያን ልጅ ለሆንክ ሕዝበ ክርስቲያን በሙሉ

በመላው ዓለም ተበትነህ፣ ከእውነት ጋር ቆመህ፣ ተወደህ፣ ለበጎው ቀን በእግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ ታትመህ ላለህ ወገኔ በሙሉ፡፡

የዛሬው መልክቴ ጊዜው በማለቁ፣ ለሕዝበ ክርስቲያን የተዋህዶ ልጆች ማጽናኛ፣ ማበረታቻ፣ የመልክቱንም የስርጭት ሁኔታ ለመግለጽ፣ ባገራችን የለውን መንግስታችንን በተመለከተ ከፈጣሪ የተላለፈበትን ውሳኔ ለማሳወቅና ወገኔ የተዋህዶ ልጆች ስለምታደርጉት ዝግጅት ለማሳሰብና ለመምከር የታሰበ ነው፡፡

አባቶቼ፣ እናቶቼ፣ እህቶቼ፣ ወንድሞቼ፣ እንዲሁም ልጆቼ፤ የልዑል ልጆች፣ የድንግል ልጆች፣ የቅዱሳን መላእክት ወዳጆች፣ የታመናችሁ የተዋህዶ ልጆች፣ ሠላምታዬ ይድረሳችሁ፡፡ መልካሙን ቀን በመናፈቅ በትእግሰት ቆማችሁ፣ በጾም በጸሎት ተግታችሁ፣ ረሀብን፣ ችግርን፣ እስራትን፣ ስቃይን ፣ ማጣትንና መንከራተትን ታግሳችሁ፣ ለደረሰባችሁ ብርቱ ፈተና ሁሉ እምነታችሁን መመከቻ አድርጋችሁ፣ ለበጎ ቀን ለዘላለም ለማይጠፋ የአግዚአብሄር ጸጋ፣ የክብር ወራሽ የሆናችሁበትን ክቡር የደሙን ማህትም ተተግናችሁ ላላችሁ ሁሉ!

በተወደደችው፣ በተመረጠችው የተዋህዶ እምነታችሁ ጸንታችሁ ለቆማችሁ ሁሉ! እንዲሁም በዚች የመጨረሻዋ ሰአት ከተለያዩ የጥፋት መንገድና እምነት ፣ ለሁሉም የሰው ዘር ይደርስ ዘንድ በተላለፈው የልዑል መልዕክቶች ራሳችሁን በመውቀስ በመጸጸት ወደ አባታችሁ ወደ ቸሩ አምላክ እናም ወደ ተወደደችው ሩህሩሀዋ እናታችን ወደ ቅድሰት ድንግል ወላዲተ አምላክ እቅፍ የተመለሳችሁ ሁሉ ! ከከብራችሁ መገለጫ ማማ ከኢትዮጵያ ጀምሮ በመላው አለም ለተበተናችሁ አባቶቼ፣ እናቶቼ፣ ወንድሞቼ፣ አህቶቼ፣ እንዲሁም ልጆቼ በአባታችን በቸሩ ፈጣሪ በናታችን በቅድስት ድንግል ማሪያም ስም የአክብሮት ሰላምታዬ በድጋሚ ይድረሳችሁ ! ባላችሁበት ሁሉ፣ የአምላካችንና የአባታችን የእግዚአብሄር አብ የእግዚአብሄር ወልድ የእግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ አንዱ አምላክ ቸርነትና በረከት ፣ የእናታችን የቅድስት ድንግል ማሪያም የእናትነት ጸጋ ፣ በረከትና አማላጅነት ፣ የወዳጆቻችን የሊቀ መላእክት የቅዱስ ሚካኤል ፣ የሊቀ መላእክት ቅዱስ ገብርኤል ፣ የሊቀ መላእክት ቅዱስ ሩፋኤል፣ የሊቀ መላእክት ቅዱስ ራጉኤል፣ የሊቀ መላእክት ቅዱስ ኡራኤል፣ የሊቀ መላእክት ቅዱስ አፍኒን ጥበቃ፣ ቸርነት ፣ ምልጃና የምህረት ጥላ ይክበባችሁ እላለሁ !!

በዛሬው መልዕክቴ

1ኛ/ የምትጽናኑበትን፣ የምታርሙትን፣ የምታደርጉትን፣ መሰረታዊ ጉዳይ በማንሳት ለመምከር !

2ኛ/ ጊዜው በማለቁና በመፈጸሙ ሁለንተናዊ ዝግጅት እንድታደርጉ ለማሳሰብ !

3ኛ/ በአሁኑ ሰአት አገዛዙን አክብዶ ያለው የኢትዮጵያ መንግስት እድል ፈንታው መጠናቀቁንና ይህንንም የእግዚአብሄር ወዳጆች እንድታውቁ በዝርዝር ለማሳወቅ የተዘጋጀ የመጨረሻ የመሰናዶ መልእክት ነው፡፡

ወደ ዝርዝር መልእክቶቹ ከመሄዳችን በፊት ጠቅለል ያለ የመግቢያ ማስገንዘቢያዎችን እናንሳ!

ሁላችሁም እንደምታዩትም እንደሰማችሁትም፣ አለማችን ሲመከር ሲዘከር ሲገሰጽም ቆየ፣ ነገር ግን አላደመጠም እንደውም በንቀቱ ዘለቀ፣ ናቀ፣ የጸባኦትን ቃል አቃለለ፡፡ በቸርነቱ፣ በፍቅሩ ወሰን ያልተበጀለት አምላክ በዘረጋለት ምህረት ላይ አላገጠ፡፡ ተወቀሰ አልሰማም፣ ተገሰጸ አልደነገጠም፣ ተመታም ልቡ አልተሰበረም፣ ታዲያ ምን ይደረግ ! ሁሌ በፈጣሪ ላይ ታብዮና አላግጦ መኖር አይቻልም፡፡

ትዕግስትም ፣ ቸርነትም ሁሉ ማብቂያ አለው፡፡ ስለሆነም የግድ የታበየ ልበ ደንዳና የሚገጥመውን እጣ መቅመስ ነው፡፡ ዛሬ የምታዩትን እያያችሁ ነው፡፡ ምድር በየሳምነቱ የመንቀጥቀጥ ምልክቱአን እያሳየች ነው፡፡ ሲብስም እንደ ሃይቲና እንደ ቻይና የጥፋት በትርዋን እያሳረፈች ነው፡፡

የካረቦን ልቀት አንቀንሳለን ብለው የተሰበሰቡ 15ሺ ሊቆች፣ የ195 አገር መሪዎችና አጃቢዎች ተሰብስበው ሲደናቆሩ ሰምተነል፡፡ ደቡብና ሰሜን ጫፍ ያለው በረዶ ቀለጠ፣ የምድር ሙቀት ጨመረ እናቁመው ሲሉ ሰማን፤ ልብ በሉ ፣ መልዕክት 1.2.3. ምን እንዳሉት እዩት፡፡ እነሱ ይህን ብለው ሲመለሱ ልዑል ጠፋብን ያሉትን በረዶ በቤታቸው ደጅ በአውሮፓ፣ በአሜሪካ፣ በኤሽያ የ2 ሜትር ከፍታ የለው በረዶ ከመረላቸው፡፡ ታዲያ ማነው የአየር ንብረቱ ባለቤት! የዲያቢሎስ ሊቃውንትና መሪዎች ወይሰ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሄር፡፡ ህሊናው ያልታወረ ያውቃል፣ የተከደነበት ደግሞ በለመደው የዲየብሎስ ቱልቱላ የደናብራል፡፡ የሚደንቀው ከተሰብሳቢዎቹ ውስጥ አንድም መሪና የአየር ሊቅ ነኝ ባይ የፈጣሪ ተግሳጽና ቁጣ ነው ሲል አልተሰማም፤ከኛው አገር ጉድ ጀምሮ፡፡ ሁሉም ሊቃውንት ትንታኔ ሲሰጡ ሰምተናል፣ ድሆች መሪዎች ደገሞ ፣ ዶሮ ብታልም ጥሬዋን እንዲሉ በዚህ አጋጣሚ ሰፋ ያለ የልመና አኩፋዳ አሰናድተው ይዘው ቢቀርቡም በተስፋ ሰነድ ብቻ ተመልሰዋል፡፡ ምክንያቱም የጌቶቻቸው ቤት እንደድሮው አፍሶ የሚሰጥበት አልሆነም፡፡ የገንዘብ ምንጭ መንፎልፎሉ ቀሪና ጭልጭል ይል ጀምሮአል፡፡ ኢዮብ 38፣ 27-30 መጽሐፈ ሄኖክ 16፣ 18- 37

አወቅን በለጸግን ፣ ተመነጠቀን የሚሉ ሁሉ ወደ ጨለማ የሚወስዳቸውን ጎዳና ጀምረዋል፡፡ ፍጥነቱም ከእንግዲህ ይጨምራል፡፡ ከአንዱ እሳት ወንፊት ወደ ሚጠበው የእሳት ወንፊት ( በመልእክቶቹ እንደተገለጸው) እየተሸጋገሩ የተጻፈላቸውን ጎዳና ተያይዘውታል፡፡ እኛም በፈጣሪያችን ጉያ ሆነን የሚሆነውን መታዘብ ብቻ ነው፡፡

ሰለ መልዕክቶቹ (1.2.3.) ስርጭትና የት ድረስ እንደሄዱ ብታውቁ መልካም ነው፡፡

በእንግሊዝኛ ቁንቃ የተዘጋጀው የተሙላው መልዕክት፣ ከዚህ ለሚከተሉት አገሮች ኤምባሲዎች፣ በአደራ እንዲረከቡ ከነሸኚው ተልኮአል፡፡ በሸኚው ደብዳቤ ውስጥ የተጠቀሰው ለየተወከሉበት አገር መሪዎች አንዲሰጡና ህዝባቸውም እድል ፈንታውን እንዲውቅ እንዲያደርጉ ተገልጾላቸዋል፡፡ እነማን እነማን ደረሳቸው ፣ ከሞላ ጎደል ከዚህ የሚከተሉት ናቸው፡፡

የተባበሩት መንግስታት የአውሮፓ ህብረት፣ እንግሊዝ፣ ፈረንሳይ፣ጀርመን፣ጃፓን፣ ቻይና፣ራሺያ፣ስዊዲን፣ኖርዌይ፣ብራዚል፣ ህንድ፣ ግብጽ፣ ኢራን፣ ደቡብ አፍሪካ፣ አውስትራሊያ፣ ጆርዳን፣ በቀጥታ ሲደርሳቸው፤ ሰውዲ፣ ስፔን፣ ፖርቹጋል፣ ዱባይ፣ የመን፣ አማን፣ ኤሚሬትስ፣ አርጀንቲና፣ ኮስተሪካ፣ ሃየቲ፣ ፍልስጤም፣ ናይጀሪያ፣ ኮሶቮ፣ ቬትናም፣ አልባኒያ፣ መቄዶንያ ኒዘርላንድ ሆንግኮንግ፣ ታይላንድ፣ ካምቦዲያ፣ ግሪክ፣ ቤልጂየም፣ ኬኒያ፤ ቆጵሮስ፣ ሰዊዘርላነድ፣ ማሌዘዥያ፣ እስኮትላንድ፣ ባንግላዴሽ፣ ኤርላንድ፣ ኢታሊ፣ ባቲካን፣ ካናዳ፣ ኦስትሬያ፣ ፓኪስታን፣ ለነዚህና ለሌሎችም በተዘዋዋሪ እንዲደርሳቸው ተደርጎአል፡፡

ከ30 የማያንሱ የታወቁ በአወሮፓ፣ በኤሽያ፣ በአሜሪካ፣ በመካከለኛው ምስራቅ ያሉ የእምነትና የሙያ ዩኒቨርስቲዎች፣ ሚዲየዎች፣ ፕሬሶች(ጋዜጣና መጽሔቶች) በኢሜል አድራሻቸው ደርሶአቸዋል፡፡ ከነዚህም ዋና ዋናዎቹን ለመጥቀስ፤

ሲ. ኤን. ኤን፣ ፕሬስ ቲቪ፣ ቢቢሲ፣ ዘ ኢኮኖሚስት፣ ኒውስ ዊክ፣ ዋሽንግተን ፐስት፣ ሚድል ኢስት ጆርናል፣ ሚደያ ሱልጣን፣ ደቡብ ቻይና ሞርኒንግ ፖስት፣ ኔት ዎርዝ፣ የመሳሰሉ መጽሄቶች፣ ጆርጅ ታውን ዩኒቨርሲቲ፣ ኢነተርናሽናል ስኩል ኦፍ ብሬመን (ጀርመን)

ከዩኒቨርሲቲዎች፡- ሴንት ሜሪ ዩኒቨርሲቲ(ከቶሊክ)፣ ብሪቲሽ ስኩል ዋሽንግተን፣ አክስፎርድ ዩኒቨርሲቲ፣ ግሎባል ሄድ ኦፍ ሴኪዩሪቲ፣ ሴንትራል ኢሮፐያን ዩኒቨርሲቲ፣ አቴንስ ዩኒቨርሲቲ፣ ብሪቲሽ ኮሎምቢያ ( ፓስፊክ ኢንስቲቲዩት ፎር ክላይሜት ሶሉቲነ)፣አውስትራሊያ ኢንብሩክ ዩኒቨርሲቲ፣ ዩኒቨርሲቲ ኦፍ ፔንስልቫኒያ፣ እና ሌሎችም፡፡

ከላይ በከፊል የተዘረዘሩትን አገሮች፣ ተቆሞች፣ ሜዲያዎች፣ ፐሬሶች፣ መጽሔቶች፣ ዩኒቨርሲቲዎች ደርሱአቸው እኔም መድረሱን አረጋግጬ፣ እነሱም ሰምተው ንቀው ትተውታል፡፡

አንድ መጽሔት ብቻ እሱም ዘኢኮኖሚሰት የተባለ አርሞ ቀነሶ ጨምሮ ለማውጣት ፈቀድ ቢጠይቀኝም እግዚአብሄር ትዕዛዝ አይለወጥም  አይሻሻልም ብዬ ቐንቐን የቐንቐን አጠቃቀሙን ብቻ ማስተካከል እንደሚችል በአክብሮት ገልጨለታለሁ፡፡

ይህ ሁሉ የተበተነው በኔ በኩል ቢሆንም ሌሎች ወንድሞቼና እህቶቼ እንዲሁም በተዋህዶ እምነታቸው የጠነከሩ አባቶች እናቶችና ወጣቶች እጅግ በብዙ እንዲሰራጭ አድርገዋል፡፡ 2/3 ኛው የአለም ክልል ደርሶታል ማለት ይቻላል፡፡ በመልእክቱ ስርጭት አብዝታችሁ ለደከማችሁ ወንድሞቼና እህቶቼ እንዲሁም ወጣት ልጆቼ እግዚአብሄር ይባርካችሁ፣ የበጎውን ቀን ወራሽ የድርጋችሁ፡፡ አይዞአችሁ ጊዜው ተጠናቐል፡፡

የአገሬ መሪዎች ስለ መልዕክቱ ምን ያህል የውቃሉ ፤ ባጭሩ ሁሉም መልዕክት ደርሱአቸዋል፡፡ በሚገባም ያውቃሉ፡፡ መልዕክት አንድም በመረጃ ሰረተኞቻቸው ፣ መለዕክት 2ን አማርኛና እነግሊዝኛውን በቀጥታ ለራሳቸው ለጠቅለይ ሚኒስትር ፣ 133 ገጽ ያቀፈውን ሙሉ መልዕክት አማርኛውንም አንግሊዝኛውንም እንዲሁ በቀጥታ ለጠቅላይ ሚኒስትር የደረሳቸው ሲሆን ይህ መልዕክት ለህዝበ ክርስቲያኑ ሲሰራጭ ደግሞ ለጠቀላይ ሚኒስትራችን በዚሁ መልዕክት ውስጥ የምታዩትን 3ኛ ደብዳቤ እንዲደርሳቸው ተደርጎአል፡፡

ባጠቃላይ ይህ ለህዝበ ክርስቲያኑ የተዘጋጀ መካሪ፣ አበረታች፣ አዘጋጅና ስለ እውቀቱ አመላካች መልዕክት ስታገኙ ለመንግስትም የሄዱትን ሸኚ ደብዳቤዎች በሙሉ ታገኙታላችሁ፡፡

እንግዲህ ልብ ልትሉ የሚገባው በግሌም ሆነ በወንድሞቼና እህቶቼ በኩል ከ4 ዓመት ጀምሮ ማለትም ከ1998 ኅዳር 7 ጀምሮ ለመላው የሰው ዘር የፈጣሪን ፍርድ በተከታታይ ሳሳውቅ ስናሳውቅ ቆይተናል ፡፡ ሁሉንም ሂደት እንደተረዳችሁት ይህንን እውነትና የፈጣሪ ፍርድ አንድም መንግስት፣ አንድም ድርጅት፣ ወይም ሚዲያ፣ ወይም ፐሬስ ትንፍሽ አላለም፡፡  በኛ አገር ያልደረሰው የለም ( ድርጅት፣ ሚዲያ፣ ግለሰብ፣ መንግስት፣ የሃይማኖት ተቋአም ወዘተ...) ሁሉም ተዳርሱአል፡፡ ስለዲያብሎስነታቸው ታዲያ ከዚህ የበለጠ ምን ማስረጃ ያስፈልጋል፡፡

በቤተ ክርስቲያናችን ያሉትስ! በራሳችን የተዋህዶ ቤታችን ተኮልኩለው በዘመኑ አጠራር አርቶ ጴንጤ፣ ጸጋ፣ ቅባት፣ የሚል ስውር ማጥቂያ ይዘው በኛው የእምነት ቐንቐ እየማሉ እንደ ምስጥ የእምነት

መሰረታችንን የሚቦረቡሩ የዲያብሎስ የውስጥ አርበኞች ሆነው ህዝበ ክርስቲያኑን ከአባቶች መንገድ ሊያወጡ እየደከሙ ያሉ አሉ፡፡

የተዋህዶ እምነታችን የራሱአ ቀኖና፣ የራሱአ ስርአተ ቤተ ክርስቲያን ፣ ስርአተ አምልኮ ያላት ናት፡፡ የማስተማር ስርአቱአ፣ የዜማ ስረአቱ፣ የአምልኮ ስረአቱአ፣ የአጽዋማት ስርአቱአ፣ የመዘከርና የበአላት አከባበር ስርአቱአ ሁሉ በአባቶቻችን ያልተቆረጠ የእምነት ተግል የተገነባ ነው፡፡ ታዲያ ለጥፋቱአ የሚዘምቱና የሚሰሩ ከውጪ ያሉ ብቻ አይደሉም፣ ነገር ግን የበግ ለምድ ለብሰው በራስዋ ቐንቐ እየማሉ ከውስጥ ሆነው የሚቦረቡሩ ሆኑ እንጂ ! እነዚህንም የበግ ለምድ ለባሾች በዚህ መልክ እራሳቸውን ሲገልጡ ታውቐቸዋላችሁ፡፡ ያሬዳዊ ዜማችንን ሲያጠፉ፣ ትውፊታችንን ሲያናንቁና ሲጥሉ ሲሽሩም፣ ያአምልኮ ስርአቱን ሲንዱ፣ አጽዋማተን ስያበላሹ፣ የበአላት አከባበርን እንደ ኍላ ቀርነት ሲቆጥሩ፣ የአባቶቻችንን ድንበር ሲያፈርሱ ታገኙዋቸዋላችሁ፡፡ ከዚህም በላይ በእምነቱ ቤት የሚያገለግሉት የሚኖሩት ለእምነቱ ከፈጣሪ ለሚገኘው በረከትና ህይወት ሳይሆን ከአገልግሎቱ ለሚገኝ የስራ ትርፍ (ሳንቲም) ብቻ ነው፡፡ እነዚህንም ሳንቲም  በወደቀበት ከክብራቸው ወድቀው ሲያነሱ ታዩዋቸዋላችሁ፡፡ ለመሆኑ የትኞቹ አባቶቻችን ናቸው ለገንዘብና ለሆዳቸው ሲሉ፣ ቃሉን፣ ዜማውን፣ ትምህርቱን ሲቸረችሩ የነበሩ፣  ትምህርቱን፣ ዝማሬውን፣ ከሚወዱትና ከታመኑለት አምላክ የሚመጣውን ወቀሳም ሆነ በረከት እንዲሁም የፍርድ ቃል ሁሉንም ስለራሳቸው ሥጋ ሳይጨነቁ በነጻ ያገለግሉ አልነበረም፤ እራሳቸውን ጎድተው ተርበው፣ ተንከራተው ሰመያዊውን ዋጋ በመናፈቅ አልነበረም ወይ የእንግድነት ዘመናቸውን የከደኑት፤ የቱን ሕንጻ ገነቡ፣ የቱን መኪና፣ አሽከረከሩ፣ የቱንስ የጣፈጠ ምግብ በሉ፣ ሁሌ ተረበው፣ ምኔም ተንከራተው፣ እየደለም እንዴ ለዛሬው ዓለምን ያስደመመና ያስገረመ የእምነታቸውን በረከት የተረፉልን፡፡

ዛሬ ግን የሚያስደንቁ ሰዎች ተፈጥረዋል፡፡ ደፋሮች ናቸው፡፡ በልዑል ደም ላይ ይረማመዳሉ፡፡ መዳኛቸውን መነገጃ አድርገዋል፡፡ የተሰጣቸውን አንደበትና ልሳን ለንግድ ለስጋ ትርፍ አውለውታል፡፡ በርግጥ አይብሉ አይባልም ለእለት ኑሮአቸው አይድከሙ ማለት አይቻልም፤ የሚኖሩት ለእምነታቸው ከሆነ የእለቱን እንጀራ ከሸፈኑ በበቃቸው ነበር፡፡ እነሱ ግን ፍጹም ለንግድ አውለውታል፡፡ ቃሉን እንደ ሸቀጥ እየቆነጠሩ ቁጥር 1፣ ቁጥር 2 እያሉ የማያቐርጥ የፋብሪካ ምርት የሚያወጡ ይመስላሉ፡፡

በግሌ ከልዑል የተላከን መልዕክት የላኩላቸው በአሁኑ ሰአት ተዋቂ ሰባኪያን የሚባሉዋቸውን ባገልግሎታቸው ክብር ሰጥቼ በቀድሚያ ነበር ሙሉውን መልዕክት የላኩላቸው፡፡ ተደስተው የተቀበሉ እንዳሉ ሁሉ ከስውር የጥፋት ስምሪታቸው ጋር የተጋጩባቸው ደግሞ በመልእክቱ ላይ የልተገባ ነቀፋና ትችት ሲሰነዝሩ ተሰምተዋል፡፡ እኔ ግድ የለኝም ለግሌም የሚደርሰው ጉዳት ምንም ስፍራ አልሰጥም፤ በእግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ ታዝዤ ላስተላለፍኩት መልዕክቶች ሁሉ እሚከፈለውን ዋጋ ልከፍልበት ስለሆነ በድጋሚ ለማረጋገጥ እመወደው በእግዚአብሄር ስራ ላይ እንቅፋት እንፈጥራለን ብላችሁ ለምትደክሙ ሁሉ ሰአቱ ስለተፈጸመ ዋጋ መክፈላችሁ ማየቀር ይሆናል፡፡ 133 ገጽ የያዘውን መልዕክት በነጻ ስሰጣችሁ፣ በአክብሮት በፐስታ ታሽጎ ለመምህር እከሌ እያልኩ ነበር፡፡ አክብረው ለተቀበሉት አክብሮቴን አየገለጽሁ ለአላጋጮቹ ደግሞ የልኡልን ፍርድ በትዕግስት ጠብቁ እላለሁ፡፡ እኛ ከራሳችን አንናገርም እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ እንደመከረን ፣ በአንደበታችንና በልባችን ፈቃዱን እንዳኖረ መጠን እንጂ !!

ለሁሉም የሚናገሩትን ሰሙ፣ ከፉውን ጣሉ በጎውን ጨብጡ ፤ እነሱ ለስጋቸው ይድከሙ፤ እናንተ በእግዚአብሄር ጸጋ የሚጠቅመውን ያዙ፤ ምንጊዜም ከመንገድ የወጣውን ጣሉ፡፡ ራሳችሁን፣ ቤተ ክርስቲያናችሁን፣ የጸናች የተዋህዶ እምነታችሁን ጠብቁ፡፡

በዚህ አጋጣሚ የእግዚአብሄር ባርኮት የሚገባቸው አሉ፡፡ ምንም እንኳአን በውስጣቸው  የተለያየ አለማ የነገቡ፣ ከጠላት ሰፈርም ከማህበሮቹም የተቀደሰ ተግባር ውስጥ እግራቸውን የተከሉ፣ ሁለት ዛፍ ላይ እንደ መውጣት ያህል እንደአንጋሬ የተወጠሩ ቢኖሩም ( በውስጣቸው ያሉ ቅኖች ይበዛሉና ) እንደ ማህበረ ቅዱሳን፣ የሰንበት ትምህርት ቤቶች፣ የጽዋ ማህበራት፣ እንዲሁም የተለየዩ መንፈሳዊ ማህበራት ሁሉ እግዚአብሄር የከብራችሁ ፣ የአባቶቻችን የእምነት ጽናት ያላብሳችሁ እያልኩ በውስጥም በውጪም ያለ የከፋ የዲያብሎስ ውጊያ ቢበረታባችሁ ማብቂያው ላይ ናችሁና አይዞአችሁ እላለሁ፡፡

እንዲሁም ለጸናች የተዋህዶ እምነት በጽናት የቆማችሁ፡- አባቶቼ፣ እውነተኛ ባህታውያን፣ በየበርሀው የወደቃችሁና የምትንከራተቱ መነኮሳት፣ ከዘመኑ የዲየብሎስ አሽከርነት ራሳችሁን በማራቃችሁ ተገልላችሁ፣ ተገፍታችሁ፣ በእንክርት የምትገኙ ፣ በከፍታም በዝቅታም ያላችሁ እውነተኛ የእግዚአብሄር አገልጋዮች ሁሉ እግዚአብሄር ያክብራችሁ፡፡ ቸሩ አምላክ ለበጎው ቀን የተማችሁ ናችሁና አይዞአችሁ፤ ወጣት የተዋህዶ እምነት አርበኞች በርቱ፤ ዘወትር በልዑል ቅዱስ መንፈስ የምትቃጠሉ ሁኑ፡፡ እኔም አጠገባችሁ ነኝ፡፡ ከወንድሞቼና ከእህቶቼ ጋር በመሃላችሁ አለሁ፡፡ ሁሉንም እያየሁ እየታዘብኩ ነው፡፡ ደስም ይበላችሁ፣ ሁሉ አልቋልና፣ አብቅቶ አገራችን ኢትዮጵያና ቅን፣ የውህ፣ ትሁት፣ ልጆቹአ ወደ ብርሃን ይሻገሩ ዘንድ ታዙአል፡፡ ይህም ላለው መንግስት ተገልጾለታል፡፡ እኛም ለመጨረሻው ሰአት በጥፍራችን ቆመነል፡፡

በዋናው መልክት እንደተረዳችሁት ዓለም ዋሾ ቀጣፊ አታለይ የዲያብሎስ ቀጥተኛ አገልጋይ መሆኑአን መስክራለች፡፡ መልዕክቶቹ የደረሳቸው አገሮች በንቀት ተሞልተው ዛሬም ሰዶምን በህጋቸው እያጸደቁ ነው፡፡ የቅርቦቹን አነህንድን መጥቀስ ይቻላል፡፡ ይህ ዓለም ምን ያህል አንደ በሽቀጠ ልትረዱ ትችላላችሁ፡፡ በጥቅሉ ከተወሰነ ሰው በስተቀር የሚበዛው እዛው በጭለማ እየዳከረ በአመጽ ገፍቶ የቁጣው አሳት እስከሚበላው እየጠበቀ ይገኛል፡፡

በመጀመሪየው ገጽ እንደ ገለጽኩት በዚህ መልዕክቴ 3 መሰረታዊ መልእክቶችን  ለማስተላለፍ የታሰበ ሲሆን

በአነደኛው ተራ ስለተጠቀሰው ብናነሳ፣

ሀ/ ሁላችሁም አንደምትረዱት የተዋህዶ እምነታችንን ከሁሉ የሚለያት ልጆቹአ ዘወትር በእግዚአብሄር ህግ እየተደሰቱ፣ በቅድስና ህይወት ተሞልተው በዜማው፣ በዝማሬው፣ በማህሌት፣ በወረቡ፣ በቅኔው ረክተው ፤ በአምላካቸው በረከት እረስርሰው፣ ትሁት፣ ደግ፣ ቅን፣ የዋህ፣ በሆነ የየእለት ሕይወታቸው፤ አምላካቸውን መስክረው፣ እውነታቸውን አንግሰው ፣ ሃሰትን አርቀው፣ ለበጎ ስራ ተግተው፤ ቅድስናን ከሚያጎድፍ ሕይወትንም ከሚያጠፋ ሃጢአት እርቀው፣ ሌብነትን፣ ውሸትን፡ በሃሰት መመስከርን፣ ንቀት ጥላቻን፣ አባት እናት ያለማከበርን፣ ወንድምን መጥላትን የመሳሰለውን የሃጢያት አዝመራ፣ ከልባቸው ነቅለው እንዲጉአዙ ከአባቶቼአ  ጀምሮ እያስተማረች የለች ቤተ ክርስቲያን ነት፡፡ ስለዚህ ለበጎ ቀን የታተማችሁበትን ቅዱስ መንፈስ ከሚያሳዝን ተግባር እርቃችሁ፣ በንስሃ ተፈውሳችሁ፣ በፊታችሁ ለቀረበው በረከት ልትዘጋጁ ይገባል፡፡

ጌታ በእናንተ የሕይወት ምስክርነት በፊቱ በብርሃንነት ልትመላለሱ ወዶአችኍአል፡፡ አገራችን ኢትዮጵያን የዙፋኑ ማረፊያ፣ የስሙ መመስገኛ፣ የበረከቱ መፍሰሻ ምንጭ ትሆን ዘንድ ወዱአል፡፡ ከዓለም

ሁሉ አብልጦ ወደዳችሁ፤ የሚወዳትን እናቱን ለእናንተ እናት ትሁናችሁ አለ፡፡ ሚከኤልን፣ ገብርኤልን፣ ሩፋኤልን፣ ፋኑኤልን፣ የሁላችሁም ጋሻና የበረከት መፍሰሻ አደረገ፡፡

በፍጹም ልባችሁ፣ በፍጹም ሃሳባችሁ፣ በፍጹም ነፍሳችሁ አምላካችሁን ውደዱ፤ በምልጃዋ እዚሁ ያደረሰቻችሁን ድንግልን ውደዱ፤ በሕይወት ትኖሩ ዘንድ፣ በምልጃው፣ በጥበቀው የረዱአችሁን ቅዱሳን መላእክትን እነ ገብርኤልን፣ እነ ሚካኤልን፣ እነ ሩፋኤልን፣ እነ ፋኑልን፣ እነ ራጉኤልን፣ እነ ኡራኤልን ውደዱ አክብሩም፡፡ ኣለምን አትምሰሉ ከእርኩሰት ስራቸው ራቁ፤ በተለያየ የስጋ ትርፍ እየተደለላችሁ ለዲየብሎስ ካደሩ የጨለማ ሰራተኞች ጋር አትተባበሩ፤ ሁለት እግር ስላላችሁ ሁለት ዛፍ ልትወጡ አትችሉምና ወደ ፈጣሪያችሁ ብቻ አስቡ፡፡

ዛሬ በአገራችን ያለው ስርአት ፍጹም ዲያብሎስን ያነገሠ ነው፡፡ የመናፍቅ፣ የተረት አማኞች ጠበቃ ነው፡፡ ጥንቆላን ኮከብ ቆጠራን ልዩ ልዩ ትብተባን ያጎለመሰና በዚያም የሚገለገል ነው፡፡ ታዲያ ከዚህ ስርአት ጋር ወግኖ ነገ ደግሞ የእግዚአብሄርን ቀን አገኛለሁ ማለት ከንቱ ዘዴና ምኞት ነው፡፡ ዲየብሎስ እጅና እግሩ ሲቆረጥና ሲጣል፣ ሰራዊቱም አብሮ ይወገዳል ይጠፋል፡፡

ምሳሌ ላንሳላችሁ መንግስታችን ዛሬ ምርጫ እያለ ይዳክራል፣ የዚህም ምርጫ መራጭ፣ ተመራጭ፣ አስመራጭ፣ ታዘቢ ፣ጠባቂ፣ አስፈጻሚ መሪውም ሁሉ የሚደከሙት ለማነው፡፡ የሚለፈት የትኛውን ስርአት ለማንጻት ነው፡፡ አዎን የጨለማውን ስርአት፡፡ የዲየብሎስን ስርአት ለማንገስ ነው፡፡ ከዚህ የዘለለ ምንም ተግባር የላቸውም፤ ታዲያ ከዚህ የጨለማ ስራ ጋር እግዚአብሄር ምን ግኑኙነት አለው፡፡ እግዚአብሄርን የሚሹ፣ በእምነት፣ በጽናት ፈጣሪ የገባላቸውን የተረጋገጠ ተስፋ የቀኑን መድረስ በመናፈቅ፣ የሱን ብርሃናዊ መንግስት በጉጉት በመጠባበቅ ላይ ይገኛሉ እንጂ በጨለማው አሰራርና የዲያበሎስ የውሸት ተውኔትና ድራማ እየተጠለፉ፣ በፍርፋሪ እየተደለሉ አይወድቁም፡፡ የእግዚአብሄር ሕዝቦች ምርጫቸው እነሱ የሚወዱት እሱም የሚወዳቸው ቸሩ ፈጣሪ ሊያቆምላቸው የወሰነውን የራሱን ብርሃናዊ አገዛዙን እንጂ፤ ሲፈጫቸው ሲቆላቸው ለጥቂቶች የዲያብሎስ ውለጆች ቆሞ ሲያሰቃያቸው የኖረውን የጨለማ አገዛዝ አይደለም፡፡

ዲያብሎስ እኮ ትላንት ያያችሁትን የጨለማ ስርአት በምርጫ ተብዬ የዲሞክራሲ ድራማ መልሶ ለመጫን ነው የህልም እሩጫ የያዘው፡፡ ያ ዘዴ ለረጅም ፣ በሺዎች ለተቆጠሩ ዘመናት የእግዚአብሄርን ሕዝብ ሲፈጭበት ሲቆላበት ኖሩአል፡፡ ዛሪ ያ ዘመን ዳግም ላይታይ ሞቶ ሊቀበር በልዑል አምላካችን ተወስኖአል፡፡ ቅድሚያ የብርሃን ክብርንና ነጻነትዋን ከመላው ዓለም ካሉ አገሮች ቀድማ ትጎናጸፍ ዘንድ ኢትዮጵያ ታሰበች፡፡ ከመልእክቱ እንደምትረዱት ኢትዮጵያ የዓለም ብርሃናዊ የልዑል አገዛዝ የዙፋኑ ማረፊያ እንድትሆን የተመረጠች በመሆኑ በቀጣዩ ነጻ ለሚወጡ አገሮችና፣ ሕዝቦች መሰብሰቢያ ፣ መደራጃ፣ ሙሉ መንፈሳዊና ስጋዊ አመራር ማግኛ ስለምትሆን ያለው የአሁኑ መንግሰት መንግስታዊ አሰተዳደሩን በልዑል ለተቀቡና ለተሾሙ ሕዝቦች እንዲየስረክቡ ተወስኖአል፡፡ የኢትዮጵያ ወደ ብርሃናዊ ክብርዋ መምጣት፣ ለኣለም ደግሞ የሚጠፋው ጠፍቶ የሚቀረው ቀርቶ ወደ ለዑል በረከትና ጉያ የመሰብሰቡ ምልክት ይሆናል፡፡ ዲያብሎስ ለዘመናት የዘረጋውን የጨለማ ዘመን ለማቆየት ቢየልምም ያ ምኞት እንጂ ከእንግዲህ እውን አይሆንም፡፡ የሱ ዘመን ተፈጽሞአል፡፡ በመጨረሻው ሰአት ከሱ ጋር መወገን ራስን በፈቃድ የማጥፋት ያህል ነው፡፡ ለመጪው የብረሃን ዘመን ሳይደርሱ ከሚቆረጡት እንዳትሆኑ ተጠንቀቁ፡፡ ምክርን ብትንቁ ነገ ዋጋ መክፈላችሁ አይቀርምና ! ባለቀና በተጠናቀቀ ሰአት ከሚጠፉ ጋር መሆን አብሮ ለመጥፋት ብቻ ነው፡፡

የጊዜን ማብቃት ያልተረዱ በሆዳቸው ብቻ የሚያስቡ አንድ ተረት በሚገባ ይገለጽላቸዋል፤ ተረቱም፡- አንድ እድሜ የጠገበ ጅብ ሁለት ልጆች ነበሩት፣ የአንደኛው ልጁ ስሙ መንሾለላ ሲባል የሁለተኛው ልጁ ስም ደግሞ መዝሩጥ ይባላል፡፡ታደያ ከእለታት ባንዱ ቀን አያ ጅቦ ሁለቱንም ልጆቹን ይዞ ምግቡን ሲፈልግ ሳይቀናው ቀይቶ ሌሊቱ ተጋመሶ ከቆየ በኍላ አንድ ጌታው የረሳውን አህያ በጫካ ያገኛሉ፡፡ ይህንኑ አህያ ተጋግዘው ይጥሉታል፡፡ ሶስቱም ሊበሉ ሲቀርቡ አባት ጅብ የለም ወደያ ፈቀቅ በሉ አህያውን መስባትና ያለመስባት ልይ ብሎ ብቻውን ይበላ ጀመር ልጆቹም አባታችን ለኛም እንብላ እንጂ ቢሉት ቆዩ ስባቱን እያየሁ ነው ካለ በኍላ ለመንጀለላ አነድ ጆሮ ወረወረለት፡፡ ለመዝሩጥ ግን ፍጹም ከለከለው፡፡ በዚህ ሁኔታ ላይ እያሉ መንጋት ጀመረ፡፡ ሁለቱም ልጆች ስለሰጉ አባታችን ነጋ እኮ እንሂድ አሉት፡፡ አባት ጅብ መብሉ ስለጣመው ዝም በሉ የጨረቃን ንጋትና የአህያን ስባት የማውቀው እኔ ነኝ በማለት ማሳሰቢያቸውን ናቀ፡፡ እንደተፈራው አልቀረም የአህያው ባለቤት ጎረቤቶቹን አሰባስቦ ጦርና መጥረቢያ ይዞ ሲፈልግ ፣ እጅግ ሆዱ የከበደ ጅብ በአህያው ላይ ተከምሮ ሲነጭ ደረሰ፡፡ በሁኔተው የደነገጡት ሁለት ልጆች በሩጫ ተፈተለኩ፡፡ አባት ጅብ አደጋ ውሰጥ መውደቁን ሲያውቅ ልጆቹን እንዲህ እያለ መጣራት ጀመረ፡፡ ልጄ አድነኝ መንሾሎላ ሲል ልጅ ደግሞ አባቴ ምን ሰጠከኝ ከአንድ ጆሮ ሌላ በሎት ገሰገሰ፡፡ አድነኝ ልጄ መዝሩጥ ብሎ ሁለተኛ ልጁን ተጣራ ልጁም አባቴ እንደበላህ እሩጥ ብሎት አመለጣ፡፡ ሆዳሙ አባት ብቻውን ሲኀሰር ብቻውን በመጥረቢያ ተቀጥቅጦ ሞተ፡፡ የህን ምሳሌ በከንቱ አለነሳሁም፡፡ ለዛሬዎቹ አልነጋም ባዮች እጣቸው ይህው እንደሆነ ስለሚያሳይ ነው፡፡

በሆዳቸው የሚያስቡ በሰፊው ዘርግተዋል፣ የሚጠፋውን ዲያቢሎስ ተመክተዋል፡፡ አለቅጥም ደረጅተዋል፡፡ አሁን ድንገት ሰአቱ አለቀ፤ ብርሃን መጣ ጨለማው ሊገፈፍ ነው፡፡ ያልበሉት የበይ ተመልካች የሆኑት ቀድመው አመለጡ፤ነገር ግን ደርጅተው የከበዱት የጨለማውን ስርአት ተስፋ የደረጉት አሁንም እዛው ባሉበት ናቸው፡፡ መጨረሻውንም አነሆ ሳይርቅ ልናየው ነው፡፡

ስለዚህ የብርሃን ልጆች ከጨለማው ውጡ ራቁ፤ ከእንግዲህ በኢትዮጵያ የሚጸናው አንድ እምነት እስዋም በልዑል ፊት የከበረች ተዋህዶ፣ የተለያየ ቀለም፣ ቸንቸ ያለው አንድ ሕዝብ፤ አንድ ጌታ እግዚአብሄር አብ እግዚአብሄር ወልድ እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ፤ አንድ እናት ቅድስት ድንግል ማርያም ወላዲተ አምላክ፤ የከበሩ ተራዳኢ ቅዱሳን መላእክት ቅዱስ ሚካኤል፣ ቅዱስ ገብርኤል፣ ቅዱስ ሩፋኤል፣ ቅዱስ ፋኑኤል፣ ቅዱስ ራጉኤል፣ ቅዱስ ኡራኤል፣ ቅዱስ ሳቁኤል፣ ቅዱስ አፍኒን ምድራችን በዚህ መልክ አጅግ በረቀቀው የእግዚአብሄር ጥበብና በረከት ጸጋም ትከበባለች፡፡

ለ/ ጊዜው ማለቁን ከላይ ገልጫለሁ ፡፡ ለመንግስታችን በተላከው ደብዳቤ ላይ እንደተገለጸው የጊዜ ገደብም አርፎበታል፡፡ በተጠቀሰው የጊዜ ገደብ ይህ ያለው መንግስት ራሱንና ስርአቱን በእግዚአብሄር ለተቀቡ እንዲያስረክብ የሚገልጽ ደብዳቤ ተልኮለታል፡፡ ደብዳቤውንም ከዚህ መልእክት ጋር ተያይዞ ታገኙታላችሁ፡፡ ስለሆነም ምን ዝግጅት ማድረግ አለባችሁ፡፡

ከላይ እንደ ገለጽኩላችሁ ራሰችሁን በቅድስና፣ በጽናት ከመጠበቅ አልፋችሁ ከዚህ እንደሚከተለው ለታደርጉ ይገባችኍአል፡፡ ይህ ትእዛዝ እውነተኛ የተዋህዶ እምነት ላላቸው ላገራቸውም ለህዝባቸውም ቀናኢ ለሆኑ ብቻ ነው የሚመለከተው፡፡

... መናፍቀንን በጥንቃቄ ለይታችሁ እወቁ፣ አድራሻቸውን፣ ተግባራቸውን በምንፍቅናቸውም ሆነ በራሳቸው ዙሪያ በቂ የአድራሻ ሰነድ፣ ማንኛውንም የጥፋታቸውን ርቀት የሚገልጽ ሁሉንም ማስረጃ ያዙ፣

በጥንቃቄ አኑሩ፣ በተለይ በዋናነት ያሉትን በጥንቃቄ አጥኑ፡፡ በክረት የሚታወቁትን ተረት አማኞችንም እንዲሁ በተመሳሳይ መንገድ አጥኑ፡፡

... በቤተ ክርስቲያን ውስጥ ታላቅ ጥፋት በማድረስ ላይ ያሉትን ኦርቶ ጴንጤን፣ጴጋ፣ ቅባት የሚባሉትን ለይታችሁ እወቁ፤ በማናቸውም እነሱን የተመለከተ ማስረጃ ሁሉ ጨብጡ፣ እንዲሁም ለእምነቱ ሳይሆን ለፖለቲካ ተልእኮ ያደሩ የበግ ለምድ ለባሾችን በሚገባ ለይታችሁ እወቁ፤ የዘር ልክፍተኞችን ፣ ዘራፊዎችን፣ አገሪቱንና እምነታችንን ከማናቸውም መሰረት ተነስተው የሚጠሉና ሃብትና ንብረቱአ ላይ ግን እጅግ የሰለጠኑትን በሚገባ አጥርታ ችሁ እወቁ፡፡

...ለጨለማው ስርአት እጅና እግር እንዲሁም መረማመጃው የሆኑትን ሁሉ በሚገባ እወቁአቸው፡፡

... በመላ አገሪቱ የተንሰራፋ የጥንቆላ፣ የቃልቻ፣ ተብታቢ፣ የኮከብ ቆጣሪ ሁሉ በሚገባ ለይታችሁ

መዝግባችሁ ያዙ፡፡

...ከዚህ በተረፈ ለመጪው መልካም ጊዜ የሚረዱ ማናቸውንም ማስረጃ ሳትቀንሱ በአግባቡ ያዙ፡፡

...በማናቸውም መልኩ ወደ ኃይልና እርምጃ አትሂዱ በነገር ሁሉ ታጋሽ ሁኑ ራሳችሁን ግዙ፡፡

ሆኖም በክፋት ተጭነው የወጡትን ህግ ረግጠው ለመጡ ለስንፍናቸው የሚመጥን ዝግጅትና

መልስ ይኑራችሁ፡፡

ጠቢቡ ሰለሞን፣ ሰነፍ ያወቀ እንዳይመስለው እንደስንፍናው መልስለት ይላልና፡፡

ሐ/ ያለው መንግስት እድል ፈንታ ምን ይመስላል፡፡

በዛሬው መላእክቴ፣ ዋናው ነጥብ የሆነው፣ በዚህ ወቅት ያለው መንግሰት እጣ ፈንታና የእድሜ ጉዳይ መታወቁ ነው፡፡

በታሪክ እንደምንረዳው ሆነ ከእግዚአብሄር ቃል እንዳወቅነው፣ በእግዚአብሄር ቃል ሲመራ በልዑልም ፈቃድ መሪውን ሲለውጥ፣ ሲያጸናም የታየው የእስራኤል ህዝብ ነው፡፡ እግዚአብሄር ለአለም ሁሉ፣ ስለ መንፈሳዊ ትምህርት፣ እምነት፣ ተጋድሎ፣ ስለ እግዚአብሄር ፍቅር ፣ ስለ አምላካችን ማንነት፣ ስለ ፈቃዱ፣ ግሳጼም ሆነ ቁጣው ምን እንደሚመስል፣ ታላቅ አስተምህሮን ለመለው ዓለም የስጨበጠው፣ በእስራኤል ሕዝብና በተጎራባች አገሮች የውደቅ ተነሳ ጉዞአቸው አማካኝነት ነው፡፡ በእርግጥ ከልዑል ፈቃድ የወጣ ምንም ዓይነት የአለም ክስተት የለም አይኖርምም፡፡ ሁሉም በእርሱ ህልው ከመሆኑ በፊት የተጻፈለትን ጎዳና ተጉዞ ለዛሬው ወቅት ደርሱአል፡፡ ለመጪውም ከሱ እስትንፋስና ቃል ውጪ የሚሆን የለም፡፡ የአለም ጉዞ በቅዱስ ቃሉ በሰማኒያ አሃዱ መጽሐፍ ቅዱስና በሌሎቹም ገድሎች፣ የቅዱሳን ታሪኮች፣ ድርሳኖች ላይ ተገልጹአል፡፡

ከሁሉም በላይ በቅዱስ ቃሉ፣ በመጽሐፈ ሄኖክ፣ በትንቢተ ዳንኤል፣ በዮሃንስ ራዕይ፣ ላይ ስለ ዓለም ጅማሮ ተጀምሮና ተጀምሮም ሆነ ተጉዞ ስለመጠናቀቅ ዓለም የምታሳልፈውን ውጣ ውረድ በሚገባ ተገልጦአል፡፡ ከዚህም የሚወጣ የወጣም ከንዋኔ የለም፡፡ ልብ ልትሉት የሚገባ ጉዳይ ቢኖር ግን ዛሬ

የምታዩአት የድሆች ተምሳሌት ኢትዮጵያ ከእንግዲህ የእግዚአብሄርን የብርሃን መንግስት ለሺ አመት ባለም ሁሉ ገና ( ከብራ ) በፍጹም የፈጠሪ ፈቃድ መርታ እምትጉአዝ ይሆናል፡፡ ዓለምም ከሺ ዘመን ፍጻሜ በኍአላ ወደ መጨረሻው ፍርድን የአለም መፈጸም ትደርሳለች፡፡ የህን ሁሉ ለምን አወቅህ የሚል በአንዳንዶች ህሊና ሊነሱ ይችላል፡፡ ልታውቁት የሚገባው ስለ ሰዶም ጥፋት እግዚአብሄር ለአብርሃም ደበቀው፤ አልደበቀውም፤ አስቀድሞ ነገረው ስለምልጃውም ተለመነውእንጂ እግዚአብሄር ከወደዳቸው፣ ከአከበራቸው፣ ከአጸደቃቸው፣በክቡር ደሙ ለገዛቸውና ላተማቸው ልጆቹ ምንም የሚደብቀው ሚስጠር የለም፡፡

ይህን ያነሳሁት የለ ምክንያት አይደለም፡፡ በልዑል ይሁንታና በታሪክ አጋጣሚ ይህ ያለው መንግስት ባላሰበውና ባላደራጀው፣ በፍጹም ባልገመተው የእድል መቁአጫና የአዲሱ የብርሃን ዘመን መምጫ መለያያ መንገድ ላይ ተገትሮአል፡፡ ሲነገረው በንቀት ያየን የነበረው መንግስታችን እስከ አሁን የጠጣትን ተጎንጭቶ በውን ወደሚያየው ገሃድ እነሆ ደረሶአል፡፡ የማምለጫም ቀዳዳም ተትቶለታል እንደ ለመደው በዲያብሎስ ምክር ወደ መፈጸሚያው ጨለማ ካልሄደ በቀር፡፡ በተሰጠቸው አጭር ጊዜ መታዘዝ ወይም አለመታዘዝ ምርጫቸው እንዲሆን እድሉ ተሰጥቶአቸዋል፡፡ ቢታዘዙ በቀደመው ሙሉ መልአክት እንደታዘዘው የምህረትና የቅጣት ተጠቀሚ ናቸው፤ ባይታዘዙ ደግሞ ቅጣት ብቻ የእድላቸው መቆጫ ይሆናል፡፡ እኔም ይህንኑ የሚያሳውቅ ጊዜውንም የሚያስረግጥ ዝርዝር ደብዳቤ እንዲደርሳቸው አድርጌአለሁ፡፡ ከእንግዲህ በኔና እነሱ መሃከል የተካሄደው የብርሃንና የጨለማ ውጊያ ወደ መቁጫው ደረሱአል፡፡

እኔም ሆንኩ መላው የተዋህዶ ልጅ የምንጠብቀው የፍጻሜ ሰአት መጥቶአል፡፡ እንግዲህ ሁሉም ነገር ተጠናቆ፣ ባጭር ጊዜ ለበጎው ቀን የታተሙ የልዑል ብርሃናዊ ልጆች እንደ ጸሀይ ሊያበሩ በተጠንቀቅ ቆመዋል፡፡ በቅዱስ መንፈሱ ሙላት፣ አገራችንና የተዋህዶ እምነታችንን፣ እኛም ህዝቦቹአ ድል ጨብጠን፣ የወደደንን ለክብሩ የመረጠንን አምላካችንን በሃሴት ተሞልተን ለማመስገን፣ ለዚህ ክብር ያበቃችንን እናታችንን ድንግልን ልናመሰግናት፣ እንዲሁም በግንባር ቀደምትነት የጨለማውን ኃይል ጠርገው ለድል ያበቁንን የከበሩ መላእክት ልናወድስ እመጨረሻው ሰአት በመድረሳችን ምስጋናችንን ለፈጣሪከልብ እናቅርብ፡፡ የያዝነው አብይ ጾምም ለታላቅ ምስጋና እናውለው፡፡

| | |
|---|---|
| አቤቱ በልቤ ሁሉ አመሰግንሀለሁ | እግዚአብሄርን አመስግኑ ስሙንም ጥሩ |
| ታምራትህን ሁሉ አነግራለሁ | ለአህዛብም ስራውን ንገሩ |
| በአንተ ደስ ይለኛል ሃሴተም አደርጋለሁ | ተቀኙለት ዘምሩለት |
| ልዑል ሆይ ለስምህ እዘምራለሁ | ታምራቱን ሁሉ ተናገሩ |
| በጠላቶችህ ወደ ኍአላ በተመለሱ ጊዜ | በቅዱስ ስሙ ተጉአደዱ |
| ይሰናከላሉ ከፊትህም ይጠፋሉ | እግዚአብሄርን የሚፈልግ ልብ ደስ ይበለው |
| ፍርዴንና በቀሌን አድርገህልኛልና | እግዚአብሄርን ፈልጉት ትጸናላችሁም |
| ጽድቅን እየፈረድህ በዙፋንህ ላይ ተቀመጥህ | የዳዊት መዝሙር 104(105) |

አህዛብን ገለጽህ ዝንጉዎችንም አጠፋህ

ስማቸውንም ለዘላለም ደመሰስህ

ጠላቶች በጦር ለዘላለም ጠፉ

ከተሞቻቸውንም ለዘላለም አፈረስህ

ዝክራቸውም ባንድነት ጠፉ

እግዚአብሄር ግን ለዘላለም ይኖራል

እርሱም ዓለምን በጽድቅ ይፈርዳታል

አህዛብንም በቅንነት ይዳኛቸዋል

ዙፋኑንም ለመፍረድ አዘጋጀ

ዳዊት መዝሙር 9

የእግዚአብሄርን ቃል የተናገሩአችሁን ዋኖቻችሁን

አስቡ የኑሮቸውንም ፍሬ እየተመለከተ በእምነታችሁ

ምሰሉአቸው፡፡

ዕብራውየን 13፤ 7

የእግዚአብሄር አብ ጸጋ፣ የእግዚአብሄር ወልድ ቸርነት፣ የእግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ፣ ማጽናናትና በረከት፣ የቅድስት ድንግል ማርያም እናታችን አማላጅነት የቅዱሳን መላእክት ተራዳኢነት ለልዑል ልጆች ሁሉ ይሁን! አሜን

ከታመነው የልዑል ባሪያና አገልጋይ

ይህ መልእክት እንዲሰጥ የተፈቀደው በተዋህዶ እምነት ውስጥ ላሉና ለእምነታቸውም ለመጪውም መልካም ዘመን በመንፈሳዊ ተጋድሎና ጽናት ውስጥ ላሉ ብቻ ነው!!

ለ <u>ክቡር ጠ/ሚኒስትር መለስ ዜናዊ</u> ቀን <u>19 – 10 – 200..</u>

በመጀመሪያ የከበረ ሰለምታ በልዑል እግዚአብሄር ስም አቀርባለሁ፡፡ ይህ ደብዳቤ የተጻፈው ስለ መልእክቱ መለስተኛ መግለጫ ለመስጠትና በኔ በኩል ያለውን እንደምታ ለማረጋገጥ ታስቦ ነው፡፡ ይህ ደብዳቤዬ የመጀመሪያም የመጨረሻም ነው፡፡ መልእክቱን ጠንቅቀው እንዲያነቡት በአክብሮት እጠይቅዎታለሁ፡፡ በህይወቶም በመጭው ዘመንዎም የሚወሰን የልዑልን መልእክት መያዙን እንዲረዱ አስገነዝቦታለሁና ! መልእክቱ ሁለት ገጽታ አለው፡፡ በእንግሊዝኛም በአማርኛም የቀረበ ነው፡፡ አንደኛው መልአክት የአገራችንን እድል ፈንታ የሚመለከት ሲሆን፣ ሁለተኛው መልእክት የዓለምን ሕዝብ እጣ ፈንታ ይመለከታል፡፡

በኅዳር 7/1998 ዖ . ም የተጻፈው የመጀመሪያው መልእክት በቀጥታ ለእርስዎ ባልክልዎትም በመረጃዎች በኩል ደርሶታል ብዬ አምናለሁ፡፡ ባያምኑበትም ዋጋ ባይሰጡትም፡፡ በሌላ በኩል ደግሞ ለሁሉም አገር ተወካዮች ባልክም ለዋና ዋናዎቹ 17 አገሮች ልኬ፣ የሁሉም መሪ የጋራ ባህሪ ነውና በንቀት ትተውታል፡፡ ነገ ከየወረወሩበት ቆሻሻ መጣያ እንደሚፈልጉት ባውቅም ስለድርጊቱ ብዙም አይገደኝም፡፡ ይህ ሁለተኛው መልእክት ለሕዝብ ደርሱአል፤ በበቂም ተዳርሱአል ብዬ ሳምን በመጨረሻ እልክላቸው ይሆናል፡፡ ዛሬም ወደ እርስዎ ከመላኬ በፊት ለህዝብ እንዲበተን አድርጌአለሁ፡፡ ለውጪዎቹ መሪዎች በድርጊታቸው ምክንያት አክብሮት ነፍጌአቸዋለሁ፡፡

በግድ ልናውቅ ይገባናል፤ እግዚአብሄር እግዚአብሄር መሆኑን፤ ቃሉም ቃል ማንም የማይሽረው፣ ማንም የማይለውጠው፣ የወሰነውንም ሆነ የፈቀደውን ከማድረግ በሰማይ ሆነ በምድር የሚያግደው እንደሌለ፣ በሚገባ ወደንም ሆነ ተገደን እንቀበለዋለን፡፡ እርስዎም ከዚህ ውጭ መሆን አይችሉም፡፡ ቢንቁ ወይም ወደ አልተገባ አካሄድ ቢያዘነብሉ እርግጠኛ ነኝ ጉዳቶ እጅግ ይከብዳል፡፡ ከመልእክቱ እንደሚረዱት አንዱም ነጥብ ሳይለወጥ ሳየጨምር፣ ሳየቀነስ ሁሉም የፈጸማል፡፡ የሰራዊት ሁሉ ጌታ እግዚአብሄር ይከብራል፡፡ ከፍ ከፍም ይላል፡፡ ካወቁበት ባለእድል፣ ካላወቁበት የከፋ ተጎጂ ነዎት፡፡ ባለ እድል ነዎት የልኩት የጥፋቱአም ቢሆን የዚች አገር መሪ በመሆንዎ ሲሆን፣ ካላወቁበት የጎዳሉ ያልኩት የእስካሁኑን ከፈጣሪ ጋራ መጋጨትዎን መቐጨት ካልቻሉ ነው፡፡

እኔ በፈጣሪዬ በልዑል ታዘዝኩ ! ላገልግሎቱም ታመንኩ እንጂ፣ ስልጣን፣ ክብር፣ ሃብት፣ በኔ ስፍራ ኖሮትም አያውቅም፡፡ የፈጠረኝን፣ የወደደኝን አምላኬን ለመታዘዝና ለማገልገል ግን ሁለመናዬን እከፍላለሁ፡፡ ለፈቃዱም እታዘዛለሁ፣ እገዛለሁም፡፡

በመሆኑም ከእንግዲህ የእርስዎ ጉዳይ ያለው በፈጣሪ እጅ መሆኑን ላረጋግጥሎት እወዳለሁ፡፡ በፈጣሪ የታዘዘውን፣ በልዑል እግዚአብሄር ችሎት የጸናውን ውሳኔ ለማስፈጸም ከኔ የመታገስ አቅም በላይ፣ ከእናንተም እንቢተኛ መንፈስ ጋር የተደመረ በመሆኑ ፣ እልባት ወደሚሰጠው ፣ ለታመነው፣ በልዑል እግዚአብሄር ፊት ለሚቆመው ለወዳጄ ለሊቀ መላእክት ቅዱስ ገብርኤል አሳልፌ ሰጥቻለሁ፤ ከዚህ ደብዳቤ ጋር ከፊተዎ መጥቶአል፡፡ የልዑልንም ውሳኔ እንዴት እንዲያስፈጽም ያውቅበታል፡፡ ሁሉንም ነገር በልዑል መልእክት እንደሰፈረው ይፈጽመዋል፡፡

ሌላው ሊያውቁት የሚገባው ቢኖር ( በአማርኛው መልእክት ውስጥ ያገኙታል ) በኔና በቤተሰቤ፣ በጉአደኞቼ ዙሪያ በየእለቱ የሚያሰማሩአቸው ቁጥር ስፍር የሌላቸው የደህንነት ሰራዊቶችዎ መፍሰስ ነው፡፡

ምን ይጠቅምዎታል፣ ለራሴም ገርሞኛል፡፡ በባለሃብቱና በእርስዎ፣ የተወሳሰበ ቁርኝነት ባጸኑ የአገርና የውጪ የመዋቅር አካላችዎ ወዳጆችዎ ፈሰስ የሚደረግለት ተቁአም እንደ ገነቡ አውቃለሁ፡፡ ብዙ የተለያዩ ተሸከርካሪዎች ፣ ሴት ወንድ ወሬ ለቀሚና ተከታታዮችዎን አሰማርተው አጅበውን ሲዞሩ ይውላሉ፡፡ ሁሉንም አውቃቸዋለሁ፣ እነሱን የመለየት ችግር የለብኝምና ! ከከንቱ ተግባረዎ እንዲቆጠቡ አሳስብዎታለሁ፡፡

ስልጣንዎን ለምነው የሚያስረክቡት እንጂ ! እኔ በመጠየቅ ሆነ በመጠየቅ እምወስድ አይደለሁም፡፡ ቢለምኑኝም ያለ ፈጣረዬ ትዕዛዝ የማልረከውብዎት ነኝ፡፡ ለምነው እንደሚያስረክቡ ግን አይጠራጠሩ ! ይህንንም ይረዱ ! ከዚህ በተረ ፈ ሁሉም የመጣው የአለምን የጥፋት ተግባር መነሻ አድርጎ አድልና እጣ ፈንታውን ለመወሰን በልዑል እግዚአብሄር ተወስኖ ስለሆነ ከመላው ዓለም መሪዎችና ህዝቦች ጉዳትና ቅጣት የእርስዎ አይብስምና እርስዎም በዙሪያየ ያሉ ታማኞቼ ፣ወዳጆቼ፣ ድርጅቴ፣ ኣገልጋዮቼ እንዲሁም ወዳጆቼ፣ ድርጅቴ፣አገልጋዮቼ እንዲሁም ወዳጆቼ ሚሉአቸው አገሮች ሁሉም የመጣውን የፈጣሪ የቁጣ እሳት ሊያውቅ የገባል፡፡ ሲጠረጉ አይደለም ማሰብ የሚቻለው እድሉ የለምና !

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን መሪዎች ፍጹም የጥፋት ሰዎች በመሆናቸው ለነሱ አክብሬ የምልከው መልእክት የለም በሰአቱ እንገናኛለን !!

ከሰላምታ ጋር

የሠራዊት ጌታ እግዚአብሄር የታመነ አገልጋይ ባሪያ፡፡

1 ኘው ሸኘ ደብዳቤ

ቀን 19 – 08 – 2001

ለ ክቡር ጠ/ሚኒስትር መለስ ዜናዊ

አስቀድሞ የአክብሮት ሰለምታዬን አቀርባለሁ፡፡

ከዚህ ቀደም ከ10 ወር በፊት የላኩሎትን መልእክት እያስታወስኩ፡፡ ምንም የተጠቀሙበት ስላልሆነና በንቀት ስለተዉት፣ ድጋሚ መላክ አልፈለግሁም ነበር፡፡ ነገር ግን ትዕግስትን ገንዘቤ በማድረግ ይህን ሁሉንም መልእክት በኣነድ ጠራዝ የያዘ የእንግሊዝኛውንም የአማርኛውንም መልእክት ልኬልዎታለሁ፡፡

ባለፈው መልእክት ባይጠቀሙም አሁንም ከዚህ የተለየ ያየደርጋሉ ብዬ አላስብም፡፡ ይሁንና እንደዚች እንደ አገሬ መሪነትዎና ሃላፊነትዎ መጠን አክብሬ ልኬልዎታለሁ፡፡

በአሁኑ መልእክት፣ መልእክት አንድን ፣ መልእክት ሁለትን፣ እናም መልእክት ሶስትን ( የመጨረሻ የአፈጻጸም ውሳኔ ያገኛሉ ) ፡፡ እርሶም የሚመለከታቸው የስራና የሃላፊነት አጋሮችዎ በሙሉ እንደ አገር፣ እነደዘር፣እንደግለሰብ ከበስተትኣለው ሆነው ሁሉን አቀፍ የጥፋት እገዛ የሚያደርጉ ሁሉ እጣቸውን ይዩበት፡፡ እንደ መልእክቱ ትዕዛዝ እንዲትአዙ ዛሬም ባለመሰልቸት እነግረዎታለሁ፡፡

እውቀት፣ ብልጠት፣ ትምክህት፣ ሁሉም በፈጣሪ ፊት ያለብረቱ ቅጣት አይታለፍምና፤ በሽርፍራፊና በተደመደመ ጊዜዎ ጫፍ ላይ ሆነው መውጫ መንገድዎን ያስቡ፡፡

እኔንም ጉአደኞቼንም ቤተሰቦቼንም በተለያየ መንገድ ሲከተሉ የሚውሉ ባለመኪናና እግረኛ የደህንነት ሰራዊቶችን ዛሬም አሰማርተዋል፡፡ ምን እንደሚጠቅምዎት ባይገበኝና ቢገርመኝም ይህ ድርጊት ግን ነገ በሃላፊነት የሚያስጠይቅዎት መሆኑን እንዲረዱት እፈልጋለሁ፡፡

ጊዜ ወስደው ስላነበቡት አመሰግናለሁ፡፡

ከአክብሮት ሰለምታ ጋር

2ኛው ሸኚ ደብዳቤ ነው

ሳይንሳዊ  ምክንያት ሲደረደርበት ይሰማል፡፡ አስተውል የሰው ዘር ገና መደበቂያ ይጠፋል፣ እስከ አሁን ከምልክትነት የዘለለ አይደለምና !

ቁጥር 1፣ 2፣ 3 በያዘው መልአክት እንደተገለጸው ሁሉም የጥፋት አይነቶች መጠነቸውን በመጨመር ላይ ናቸው፡፡ የዘመናችን አዋቂዎች ፣ ጥበበኞች፣የፖለቲካ ትያትረኞችና፣ የዲማጎጂ አርቲስቶች አለምን በረቀቀ የውሸት ብርድ ልብስ ሸፍነው የሚዘልቁ መስሎአቸው አሁንም እየማሰኑና እየዳከሩ ይገኛሉ፡፡

የአየር ንብረት እንቆጣጠራለን፣ የሞቀውን እናቀዘቅዛለን፣ የተቃወሰውን ኢኮኖሚ እናስተካክላለን፣ የሁሉንም ችግር እንፈታለን፣ በጦር በጀት እንከላከላለን፣ሲሉ፣ የሃይማኖት መሪ ነን ባይ የዲያብሎስ አሻንጉሊቶችም እንዲሁ ከፖለቲከኛው ጋር ተባብረን እንፈታዋለን ይሉናል፡፡ ሁለቱም ክፍሎች እንደ አሮጌ ነጠላ እየተቦጨቀ በየቦታው የሚፈነዳውን ችግርና አደጋ በማያልቅ የውሸት ድሪቶ ሊጥፋትና ሊጠግኑት ሲደክሙበት ይታያል፡፡

እርሶም እንደ ገዢነተዎ የዚሁ የመሪዎች መድረክ አባል ነዎት፡፡ የህም ለኔም በኢትዮጵያውነቴ እጅግ አሳፋሪ ነው፡፡ የዚች ታላቅ አገር መሪ ሆነው ሳለ በዚህ መልክ ሲፈረጁና የእግዚአብሄር ጠላቶች መህበርተኛ ሆነው በማየቴ አገሬ በምን የጉዳት መጠን ውስጥ እንዳለች ተረድቼአለሁ፣ ሳስተውልም ኖሬአለሁ፡፡

ከለይ እንደጠቀስከት መንግስታዊ ስርአቶንና አገዛዞን ለመውቀስ ለመምከር ወየም ለመገሰጽ የታሰበ መልእክት የለኝም፡፡ የለኝ መልእክት ስለእድልዎ ስለመንግስትዎ በሰራዊት ጌታ እግዚአብሄር የተወሰነውንና የታዘዘውን ለመግለጽነው፡፡ በሰረዊት ሁሉ ጌታ እግዚአብሄር የተወሰነውንና የታዘዘውን ለመግለጽ ነው፡፡ በሰራዊት ሁሉ ጌታ እግዚአብሄር ፊት ጉዳዩ ታይቶ መንግስትዎ ከነአለቃና ምንዝሩ ተፈትሾ በልዑል የፍርድ ሚዛን ተለክቶ እጅግ ቀሎ ተገኝቶአል፡፡ ይህም ብቻ አይደለም ፈጣሪን ለመውጋት የመቻልን ያህል እጅግ ታብየዋል፡፡ የእግዚአብሄርን ህዝብ እጅግ ጎድተዋል፣ ለመከራ ለስቀይ ዳርገዋል፣  በእምነቱ ዘምተዋል፣ እርስ በእርሱ በዘር እንዲለያይ ዘረኝነትም እንዲነግስ አድርገዋል፣ የኢትዮጵያ ፍቅር የሌላቸውን፣ የተዋህዶ እምነታችንን የሚጠሉ፣ እንዲሁም ለጥፋትዎ የሚሰሩትን አንግሰዋል፡፡ ታይቶ ተሰምቶ የማይታወቅ የዲያብሎስ ስራ እንዲሰፍን አድርገዋል፡፡ ባጠቀለይ የዘረጉት መንግስተዊ ስርአት፣ በፈጣሪ ፊት እጅግ አስቆጪና የእግዚአብሄርንም ቁጣ የቀሰቀሰ ሆኖአል፡፡ ይህም ብቻ አይደለም በተሰጣችሁ ጊዜም የመጸጸት ምልክት አላሳያችሁም፡፡ እንደውም የረቀቀ የጥፋት ድርጅት በመላ አገሪቱ አደራጅተዋል፡፡

በመሆኑም የእግዚአብሄር ጣት በናቡከደነጾር ልጅ በብልጣሶር ለይ ወጥታ የመንግስቱን መቆረጥ እንዳሳወቀች፣ በእርስዎም መንገስት ላይ ይሁችው ታሪካዊ ጣት ወጥታለች፡፡ ሩቅ አሳቢ ቅርብ አዳሪ ሆነዋል፡፡  ጌታ መንግስትዎንም ሆነ በስርአተ መንግስትዎ ውስጥ ያሉትን ተቃዋሚዎ እንዲሁም ማንኛውንም ስርአትዎትን ደግፈው የያዙ ኃይሎችን ሁሉ አሰናብቶአል፡፡ በቦታውም የእግዚአብሄር መንግስት እንዲተካም ታዝዋል፡፡ በመልእክቱ የተጠቀሱት የኢትዮጵያ ወደ ክብርዋ፣ ወደ ብርሃናዊ ጎዳናዋ እንድትወጣና ይህም እውን እንዲሆን ተወስኖአል፡፡ በመሆኑም በእጅዎ ከሚገኘው መልእክት እንደሚረዱት፣ ዓለም በሙሉ ከቅጣት አያመልጥም፤ የተራ ጉዳይ እንጂ፡፡ ሁሉም አገር የተመደበለትን ጽዋ

ይጋታል፡፡ አንዱ በፍጥነት፣ አንዱም በቀጣይነት፣ ሌላውም በረጅም ስቃይ እድል ፈንታውን በድርሻነት ይወስዳል፡፡ ለየሃገሩ የተሰጠው ሸክምና እጣ ፈንታ ይለያያል፡፡ የእርስዎ ግን አልቆአል ተፈጽሞአል፡፡

ቅጣትና ምህረት ሳስተዋሉ ቶሎም ራሳቸውን በእግዚአብሄር እጅ ለሚጥሉ የተሰጠ እድል ነው፡፡ በመጨረሻው ሰአት በዚህ አድል መጠቀም አንዱ መንገድና ብልሃት ነው፡፡ በሌላ በኩል ደግሞ ለሚያፌዙ፣ ለሚንቁ፣ በጥፋት ጎዳና ለሚዘልቁና በኃይላቸው ለሚታበዩ ምህረት የሌለበት ቅጣት ብቻ የእድላቸው ማረፊያ ሆኖአል፡፡ እንግዲህ በዚህ የመጨረሸው ደብዳቤዬ ብታንስም ቁም ነገር ሊያገኙ ይችላሉ ብዬ አሰባለሁ፡፡ ከናቁትም መብትዎ ነው፡፡ የትርፉ ባለቤት መሆንዎ ግን አይቀሬ ነው፡፡ ሳሳውቅ ቆየሁ፡፡ ዛሬም ደግሞ የእርስዎን እድል ፈንታ የሚወስነውን ትዕዛዝ ለመግለጽ እነሆ ታዘዝኩ፡፡

ስለዚህ ከዚህ በታች የምዘረዝራቸው ትእዛዞች በሙሉ ተፈጻሚ እንዲየደርጉ አሳስብዎታለሁ፡፡

1ኛ/ ከዚህ ደብዳቤ መድረስ ጀምሮ የሚወጡ ማናቸውም የተዋህዶ እምነታችንን፣ የአገሪቱን ህልውና፣ ምልክትና (ሰንደቅ አላማ ) የሚነኩ ህጎች፣ ደንቦች እንዳይወጡ፣ የወጡም እንዲታገዱ፡፡

2ኛ/ የሃገሪቱን ሃብት በተለያየ ዘዴ በመዝረፍ በማሸሽ ላይ ያሉ በፍጥነት እንዲገቱ፡፡

3ኛ/ የለበቂ ወቅቱን የተከተለ ካሳና ሃገራዊ ምክንያት ድሆችን ከየቀያቸው ማፈናቀሉና ማባረር በፍጥነት

እንዲቆም፡፡

4ኛ/ በተለየ በተዋህዶ ቤተ ክርስቲያናችን ውስጥ ከለይ እስከታች የኮለኮላቸውን ተኩላዎች ከመድረሴ

በፊት በፍጥነት እንዲያነሱ፡፡

5ኛ/ በየክልሉ የሚካሄዱ ዘረኝነትን መሰረት ያደረገ ሁለንተናዊ እንቅስቃሴና የዘር ልዩነት በፍጥነት እንዲቆም፡፡

6ኛ/ እስከ ያዝነው የ2002 ዓ. ም የአብይ ጾም ፍቺ ድረስ በመንግስትዎ ዙሪያ ሊያጠናቅቁ የሚገባዎትን የመሸጋገሪያ ዝግጅት እንዲየጠናቅቁ፡፡

7ኛ/ ከኔ ጋር ለመነጋገርም ሆነ በውሳኔዎቹ ከተገዙ የተሙአላውን መልአክት ፣ (1.2.3) የያዘውን በሁሉም የመገናኛ መስመር ለህዝብ በተደጋጋሚ የመግለጽ ግዴታ እንዳለብዎት ይወቁ፡፡ ይህን ሳያደርጉ በምንም መልኩ ላናግረዎት በፍጹም አይቻለኝምና !!

ይህንን ትዕዛዝ አምነው ለፈጣሪ ተዕዛዝ ተገዝተው ስልጣንዎን ለማሸጋገር ከወሰኑ ብቻ ነው ከላይ የዘረዘርኩአቸውን ትዕዛዞች የሚፈጽሙት፡፡ ንቀው ከተዉት ደግሞ 4 ገጽ ወረቀቶች ናቸውና ቀደው ይጥሉአቸው ዘንድ መብትዎ ነው፡፡

ከጊዜ ገደቡ በፊት ከ15 ቀን በላይ የማይወስድ የመነጋገሪያ ጊዜ ሰለአሎት በሚሹት ጉዳይ ሊያነጋግሩኝ ይችላሉ፡፡

8ኛ/ ከለይ የተዘረዘሩትን ትዕዛዞች ከፈጸሙ ስልእርስዎም ሆነ አብሮዎት በውሳኔ አሰጣጥ ስለሚሳተፉ ሁሉ እጣ ፈንታ ልገልጽልዎትና ልንነጋገርበትም እንችላለን፡፡

፬ኛ/ ስለኔም ሆነ ወንድሞቼና እህቶቼ ማንነት ከኔ ፈቀድ ከላገኙ መግለጽ አይቻልም፡፡

ባጠቃላይ መንግስትዎ ከነማንኛውም ይዞትና ገጽታው ጋር በቸሩ አምላካችን የማይለወጥ ትዕዛዝ እንዲያከትም የተወሰነ መሆኑን በድጋሚ እያረጋገጥኩልዎት በቦታው ያለምንም እንቅፋት በእግዚአብሄር የተቀቡና የተሾሙ አገልጋዮቹ እንዲረከቡም የልዑል ውሳኔ አርፉአል፡፡

እንግዲህ ለማንበብም ለዚህ በአክብሮት ለተላኩት ደብዳቤ ዋጋ ለመስጠትም ንቆም ወይም ቀዶ ለመጠልም በጥቅሉ ለሁሉም ድርጊት ደግሜ እላለሁ መብትዎ በእጅዎ ነው፡፡ የኔም ትእግስት እስከ ያዝነው አቢይ ጾም ፍቺ ድረስ ብቻ ነው፡፡ ከዚያ በኋላ ሁሉም የሚከናወነው የልዑልን ትዕዛዝ በሚያስፈጽሙ ቅዱሳን መላእክት በመሆኑ የኔም ሆነ የወንድሞቼ ድርሻ አፈጻጸሙን ማየትና ስንታዘዝ ስፍራውን መረከብ ብቻ ይሆናል፡፡ እኔም በፈጣሪ የታዘዝኩትን መፈጸም ብቻ ነው፡፡ ከዚህ ሌላ የምለው የለም፡፡ ከዚህ የመጨረሻው የጨለማው ዘመን ማብቂያ ሰአት ላደረሰን ቸሩ ፈጣሪ የማይቁአረጥ ምስገና ይፍሰስለት ፡፡ አሜን፡፡

ጊዜውን ሰውተው ስለተመለከቱት አመሰግናለሁ፡፡

ከአክብሮት ሰላምታ ጋር

ከታመነው የልዑል ባሪያ አገልጋይ

# ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን

21/01/2004 ዓ.ም.

# አምስተኛ ክፍል

አንባቢዎች ወደ ዋናው መልእክት ከመግባታችሁ በፊት ከዚህ በታች ያሉትን ማሳሰቢያዎች በማስተዋል ያንብቡት !

ማሳሰቢያ፡- ይህ መልዕክት የቀደሙትን መልዕክቶች 1፤ 2፤ 3፤ 4ን ተንተርሶ ከመጀመሪያ ደረጃ ቅጣት ፤ ሁለተኛ ደረጃ ቅጣት ሁሉም የቅጣት አይነቶች በ49 እትፍ ጉልበት አድገው አዲስ ቅጣትንምአካተው የመጡ ናቸውና ! አቅልላችሁ አትመልከቱት !

- በመጀመሪየውም ሆነ በዚህ መልእክት ስርጭት ላይ ዛሬም ለእንቅፋትነት የተሰለፋችሁ ሁሉ፤ በመልእክቱ ውስጥ ከተጠቀሰው ቅጣት ተጨማሪ መግለጫ የማየሰጥበት ቅጣት ታዘባችኋል፡፡

- ይህንን መልእክት ቢያንስ ለ3 ሰው የመስጠት መንፈሳዊ ግዴታ አለብዎት፤ ይህን የማያደርጉ ሰዎች መልእክቱ በእጃቸው ባይገኝ በተሻለ ነበር፡፡

- በነፃ ስጡ አሊያም የኮፒ ወጨአችሁን ብቻ ውሰዱ

! ከገፅ አታጉድሉ፡ ይህ አምስተኛ መልእክት 41 ገፆች አሉት፡፡ ይህ መልእክት በእንግሊዘኛም በአማርኛም ተሰራጭቷል፡፡ ወደውጪም ጭምር አሰራጩት፣ ቢሰሙም ባይሰሙም ይህ መልእክት በዋናነት የሚጠቅመው ለእግዚአብሄር ሕዝቦች ነው፡፡ ለተቀሩት የሞት መርዶ ብቻ ነው፡፡

- በመልእክቱ ተጠቀሙበት እንጂ አትጎዱበት፤ የክርክር ዘመን ስላለፈ አትከራከሩ ቢሻ ያድምጥ ባይሻ አያድምጥ ላበቃ ጉዳይ አትጨነቁ !

- በእያንዳንዱ የመልእክቱ የጀርባ ገጽ ላይ በትልቁ የኔ የልዑል ባሪያ ፊርማ አርፎበታል፡፡

# ለጥፋት ሃይሎች ሁሉ የተሰጠ ማሳሰቢያ

- በብዙ ሃይሎች ዘንድ የሚታሰብ አንድ አስተሳሰብ አለ፡፡ ይኸውም ጊዜው ገና ነው ነገርም እንዲሁ እቀጥላለሁ የሚል ይህ እንደማይሆንና ቀዩን መስመር መርገጥህን እወቀው፡፡
- በግሌ በእኔ ዙሪያ ብዙ የጥፋት ስራ መስራት ሞክራችኋል ! የምትችሉትንም አድርጋቹኋል፤ ይሁንና ሁሉንም ፈቅጄ ስለተውኩት በጉዳት ውስጥ አልወደቃችሁም፤ ዛሬ ግን ይህ አብቅቷል፡፡ ከእንግዲህ ወዲያ የኔን ጎጆ ማእከል አድርጎ በሰባት ኪሎ ሜትር ዲያሜትር ውስጥ በእኔም በወንድሞቼም ሁሉ ላይ አንዳች የቀጥታም ይሁን የተዘዋዋሪ የስለላ የጥቃት እንቅስቃሴአችሁን እንዳይ አልሻም፤ ባትሞክርዋት ይሻላል፡፡ ወደ እናንተ የሚመጣ የለም፤ እናንተው ትለምኑ እንደሁ እንጂ ! ስለዚህ በአንዳች የጠፋት እንቅስቃሴአችሁ ላይ ጥፋት መስሎ ከታየኝ፤ በቀጥታ ለልዑል አቀርበዋለሁ መ-ውንም የምታዩት ይሆናል፡፡
- ጠላት ዲያቢሎስ ከነሰራዊቱ ወደ ሺው ዘመን የገሃነም እስራቱ እንዲወርድ ተወስኖበታል፡፡ ይህ መልእክት ከወጣ ጊዜ ጀምሮ ተፈጻሚ ይሆን ዘንድ፣ የልዑል ሃይላት ይነቃነቃሉ፡፡ የዲያቢሎስና ሰራዊቱ እድላቸው ተከደነ፤ ስለዚህ መርዶአችሁን በመስማታችሁ ለምትደነግጡ፤ /ካላችሁ/ በእግዚአብሄር እጅ መውደቅ ይሻላልና በጥፋታችሁና በሞታችሁ ውስጥም ቢሆን ምርጫችሁ ብታደርጉት ይሻላል፡፡ ላላጋጮች ፌዛችሁ ይታደጋችሁ፡፡
- ዛሬ በአገራችን የሚነገረው ስለልማት፣ ስለ ውሃ መገደብ ነው፡፡ ይሁንና ይህንኑ ቋንቋ የዛሬዎቹ ሰለጠንን ባዮችም ተጠቅመውበታል፡፡ ግን ሌቦች ናቸው፤ ድሃን አደህይተው ጥቂት ቢሊዮነሮችን ፈጥረዋል፡፡ ድሃም የእነሱ እራት --- ነው፡፡

የኛዎቹም የድሃውን ደምና አጥንት ግጠው በውጪ ሃብት አከማችተው፤ ድሃው የተለመደውን የማያልቅበት የውሸት ተስፋቸውን እንዲበላ ይጥራሉ፡፡ ዓለም ከዚህ የሚሻል ለጉስቁል ቦታ የላትም፤ የዲያቢሎስ ስልት ከአያቶቻችን ዘመን ጀምር መልኩን እየቀያየረ የሚተገበር ለባለጸጎችና አገልጋዮቹ የቆመ ስርዓት ነው፡፡ ስለዚህ በምኞት የምትጋልብ ሁሉ፤ ከእንግዲህ ዓለም ሁሉ የልዑል ገንዘብ እንጂ ለተወሰነ ጊዜ በከራይ እንደሚኖር ሰው በውስጧ አዝዞና ፈልጦ ለኖረው ለዲያቢሎስ የሰራት ሃብቱ አይደለችም ! ባለቤቱ ልዑል በቃህ ቤቱን አጥፍተሃል ውጣ ለጥፋትህም ዋጋ ክፈል ብሎ ስለወሰነ የዲያቢሎስ ተስፈኛ ሁሉ ዘመንህ መከደኑን እወቅ !

- **በስተመጨረሻ ለሁሉም የመልእክቱ አንባቢ የምመክረው ፤ አስተውሎ ማንበብና መረዳት የሚገባ ሲሆን ፤ ለሌላውም ለመንገር ፤ ለመምከር ይጠቅማል፡፡ ሁሉንም መልእክቶች አንብበህ ተረዳ !!**

የዘመናችን ፖፖች፤ ፓስተሮች፤ የኛም ጳጳሳት፤ የተረት አምላኪውም ፤ የጣኦት ተገዢውም ሁሉም እስከዛሬ በገዢዎቻችሁ ተወዳችሁ ኖራችኋል ምክንያቱም በርታ ቀጥል የሚነካህ የለም የምትሉ የበአል ነቢያት ናችሁና ! ሚኪያስን በጥፊ የመቱና ያጉላሉ ምድርን የሸፈኑ የኢዮሳፍጥ ነቢያት ናችሁና ! ኤሊያስ በማን ታመነ ሚኪያስስ በማን ፀና ሁለቱም የተወቀሱት ደግ አይናገሩም ከአፋቸው መልካም ነገር አይወጣም ሁሌም ጥፋታችንን ብቻ ይናገራሉ ፤ ተብለው እንደተዘለፉ ኑረዋል፡፡ እኔም የታዘዝኩትን ስለተናገርኩ ክፉ ተናጋሪ ተብዬ እንደተወገዝኩ አለሁ፡፡ ያሻችሁን በሉ የመጨረሻ ፍፃሜያችሁን በማርዳቴ ቅርም አይለኝ የዲያቢሎስ ዘመን ተከድኖአልና !

መልካም ንባብና መረዳት ይሁንላችሁ !

# መልእክት አምስት

## በስመ አብ ወወለወድ ወመንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ አሜን !!

## መግቢያ

የስራዊት ጌታ እግዚአብሄር እንዲህ ይላል ! በዚህ ቃል ተናግራችኋልና እነሆ በአፍህ ውስጥ ቃሌን እሳት ይህንንም ሕዝብ እንጨት አደርገዋለሁ ትበላቸውማለች፡፡ ት/ኤርሚያስ 5 ፡ 14

ልብ በሉ ልዑል በቃሉ ተናገረ፤ በባሪያው በኔ በውዳቂው አፍ ውስጥ ቃሉን አኖረ ! መጭውም እስከ ዛሬእየሆነ ያለውም ውድመታችሁም መጠረጋችሁም ሁሉም እየተከናወነ ያለው ሰአትና ጊዜውን እየጠበቀ የሚሆነውም ከመጀመሪያው መልእክት ጀምሮ እሰከ እዚሁ አምስተኛው መልእክት ድረስ ከላይ እንደ ሰፈረው በልዑል በመመስረት ነው፡፡

የአዳም ዘር በሙሉ ዛሬም ጆሮህን ከፈት አድምጥ

አስተውልም ስማም እጅግ የከበደው ጥፋትህ መጥቷልና !!!

እኔ እጅግ ከሁሉ የማንሰው ሃጢያተኛው የልዑል ባሪያ ለናንተ እብድ ነኝ፤ ለፈጠረኝ አምላኬ ደግሞ ባለ አዕምሮ ነኝና ብትንቁኝም የእሳቱ መለብለብ ከእግራችሁ ጀምሯል፡፡ ዛሬም በትእቢት ተሞልታችሁ በመልእክቱ ባታምኑበትም ብትጠሉትም የሚመርር እውነት ነውና ዛሬም አደምጡ፤ የዘራችሁትንም እጨዱ!! ቀጣዩንም እሳት ካንገታችሁ ሲደርስ፣ ያንጊዜ የናቀችሁትን የእግዚአብሄርን እብድ ምናምንቴውን ትፈልጉታላችሁ፡፡ ተንበርከካችሁም ትለምናላችሁ፡፡ ይህንን ደግሞ ትምክህቴና ጋሻዬ ልዑል አባቴ ያደርገዋል፡፡ እኔ በፈጠረኝ አምላኬና አባቴ ብቻ እመካለሁ፤ ብዙዎች ባላወቁት፤ አንዳንዶች ደግሞ ዲያብሎስ ባሳዘላቸው አጀንዳ እኔን የሚነዱ መስሏቸው ብዙ አይነት የምላስ ጅራፍ ያሰናዳሉ፡፡ ቅዠታም ነው፣ እምሮው የታመመ ተፈላሳፊ ቢጤዬ ነው፤ በዘህ ዘመን እግዚአብሄር የሚልከው ሰው የለም፤ ብዘረዝረው እጅግ ብዙ ነው፤ ይሁን ብቻ ማንም የዘራውን ማጨድ ግዱ እንደሚሆን እንዳይስት፤ መልእክቶቹ ሁሉ በየሰኣታቸው ተፈጻሚ ሲሆኑ እብድና ቅዠታሙ ምን እንደሚሆን እናንተም ምን እንድትሆኑ መልስ ከወዲሁ ብታስቡበት ይጠቅማችኋል፡፡

ይህንን የመጀመሪያ መግቢያ ቃል እንዳትዘነጓት ገና ከመልእክቱ መግቢያ በር ላይ አኖርኩላችሁ፡፡ ከለይ ለተገለጸው ቃል ልዑል በቃሉ እንዲህ ይላል፡፡

እግዚአብሄርን ለሚወዱት እንደሃሳቡም ለተጠሩት ነገር ሁሉ ለበጎ እንዲደረግ እናውቃለን፤ ልጁ በብዙ ወንድሞች መሃከል በኩር ይሆን ዘንድ አስቀድሞ ያወቀቸው የልጁን መልክ እንዲመስሉ ፤ አስቀድሞ ደግሞ ወስኖአልና፤ አስቀድሞ የወሰናቸውን እነዚህን ደግሞ ጠራቸው፤ እነዚህን ደግሞ አጸደቃቸው፤ ያጸደቃቸውን እነዚህን ደግሞ ባረካቸው፡፡ ወደ ሮሜ ሰዎች ፤ ም ፤ 8፡ 28 – 30

ከዚህ በታች ያሉት የልዑል ቃሎች የዚህ መልእክትን ሙሉ ገጽ የያዘውን የቅጣት አመጣጥ የሚያሳዩና አይቀር መሆናቸውን የሚገልጹ ናቸው፡፡

| | |
|---|---|
| እግዚአብሄር የበቀል አምላክ ነው | የእግዚአብሄርን መሰዊያ እንወርሳለን የሚሉትን |
| የበቀል አምላክ ተገለጠ | አምላኬ ሆይ እንደትቢያ በንፋስም ፊት እነደ ገለባ አድርጋቸው |
| የምድር ፈራጅ ሆይ ከምድር ከፍ ከፍ በል | እሳት ዱረን እንደሚያቃጥል ነበልባልም ተራሮችን እንደሚያነድድ |
| ለትእቢተኞች ፍዳቸውን ከፈላቸው | እንዲሁ በቁጣህ አሳድዳቸው በመቅሰፍትህም አስደንግጣቸው |
| የዳዊት መዝ 93 ፡ 1 – 2 | ፊታቸውን እፍረት ሙላው አቤቱ ስምህን ይፈልጋሉ ይፈሩ |
| | ለዘለያለም ይታወኩ ይጎስቁሉ የጥፋት ስምህም እግዚአብሄር እንደሆኑ ይወቁ |
| | የዳዊት መዝ 82 ፡ 12 – 18 |

ለአምልኮቱ የቀናበት፣ የሜዳ ፅብቱን ፈጽሞ ይይዛል፤ ጠላቶቹን ለመበቀል ፍጥረቱን የሜዳ ዐበት ያደርጋታል፡፡ የውነተኛ ጥሩርም ይለብሳል፤ ማድላት የሌለበት ቦርቦርቴን ይደፋል፡፡ የማይሸነፍ የእውነተኛ ጋሻንም ይይዛል፤ የሚቆርጥ መዓቱ ሰይፍን ይስላል፤ ሙሴ ከእግዚአብሄር ጋር ሆኖ ግብጻውያንን ተጠልቶ ይዋጋል፡፡ ፈጥኖ ያገኛቸው ዘንድ በሳቱ ግብጻውያን ላይ የሚያስፈራ መአቱ በደል ነጎድ ቀንቶ ይሄድባቸዋል፡፡ ጻድቃን ግን እንደ አማረ ቀስተ ደመና አከባበብ ከበው ረድኤቱን በማግኛት ያመሰግናሉ፡፡ ከመዓቱም በደል ፣ ነጎድ፣ ደንጊየም፣ ፈጥኖ በረዶ ይወርዳል፡፡የባህሩም ውሃ በላያቸው፤ ይበሳጭባቸዋል፤ ፈሳሾችም ተነዋውጠው ፈጥነው ይከቧቸዋል፡፡ኃይል ያለው ንፋስ ይቀዋወማቸዋል፤ ነፋስ እንደመሆኑ ድርቅ ያደርጋቸዋል፡፡ ሃጢያት ምድሩን ሁሉ ታጠፋለችና፤ ከፉም መስራት የሃያላኑን ዙፋን ያጠፋልና ይበትናቸዋል፡፡

መጽሐፈ ጥበብ ም 15 ፡ 18 - 24

አመፃ ትእቢትን ትቀድማለች፡፡ በትእቢት፣ በነቀት፣ የተሞላችሁ የዘመናችን ገዥዎች አለቃን ጭፍራዎች የልዑልን ምክር፣ ፍርድና እርምጃ ንቃችሁ ፣ ዛሬም አንቋቋመዋለን በሚል የአባታችሁ የዲያብሎስን ምክር ሰንቃችሁ እጅግ ወደ ከበደው እሳትና ጨለማ እየተንደረደራችሁ ትገኛላችሁ፡፡ የእግዚአብሄር እጅ አይዝል አይደክም በከንቱተፍረመረማላችሁ እንጂ፤ እየደቀቃችሁ ከመፈጸም አንዳች የሚታደጋችሁ የለም፡፡ የሰው ዘር ልብ ልትል ሲገበህ በአመፃህ ገፍተህበታል፡፡ በወቀሳው አልተፀጸትክ፤ በፍርዱ አልደነገጥህ፣ የፍርዱ የአፈፃፀም የመጀመሪየ ደረጃ ዓለምን ሲያናውጥ ያንተ ድንጋይ ልብ ግንዛሬም በልዑል ቁጣ ላይ ነዳጅ ያርከፈክፋል፡፡

ልዑል እንዲህ ይላል! ለሞት የሆነ ወደ ሞት፤ ለሰይፍም የሆነ ወደ ሰይፍ፤ ለረብም የሆነ ወደ ርሃብ፤ ለምርኮም የሆነ ወደ ምረኮ ትላቸዋለህ ፤ ስፍን ለመግደል፣ ውሾችንም ለመጎተት፣ የሰማያትንም ወፎች የምድርንም አራዊት፣ ለመብላትና ለመጥፋት፣አራቱን አይነት ጠፉት አዝዝባቸዋለሁ፡፡ ይላል ልዑል ትንቢተ ኤርሚያስ 15 ፡ 2 – 4

ይህ ቃል በናንተ ላይ ተፈጻሚ ይሆናል፡፡ ዛሬ በምናየው ነገ በሌለው ጥበብ፣ በገዥዎችህ ጉልበት

ሃብትና ገደብ በሌለው የውሸት ተስፋቸው ታምነሃል፡፡ የዛሬው መልእክት አዲስ ፍርድ ሊነግርህ አልመጣም፡፡ የተሟለው የፍርድ ቃልና አፈፃፀም ተሟልቶ / ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን በሚል ርስ መልእክቶች 1 ፣ 2 ፣ 3 / በእጅህ ከደረሱ ከ2 አመት በላይ ሆኖአቸዋል፡፡ ይህ መልእክት ደግም የመጣው ካየኸው እያየኸውም ካለው፤ የመጀመሪያ ደረጃ እሳትና በትር ወደ ሁለተኛው የከፋ የእሳት ወንፊት መሸጋገርህን ለማርዳትና ለምን! እንዴት፣ ምንስ ተፈጸመ፣ ምንስ ቀረ፣ ዓለም እንዴት መልክቶቹን ተቀበለች፡፡ በመጀመሪያ እርምጃ ምን ተፈጸመ፣ ያሁኑስ መልእክት ለምን መጣ! ጉዳቱስ ጥቅሙስ የሚለውን ሁሉ አጥርተው እንድታይበት ታስቦ የመጣ ነው፡፡ እሰከ ዛሬ የናቅኸው ሁሉ የዚሁ ሸውራራነትህን ፍሬውንና ቀጣዩን ሸክምህን ታይበታለህ፡፡ በመልእክቶቹ የተደሰትክ ፤ በጊዜው ርዝመት ብቻ የተከፋህ ሁሉ በሰአቱና በጊዜው ልዑል በፈቀደበት ሰአት ተፈጻሚ እንደሚሆን ፤ አነዳችም ከመልእክቶቹ ሳየፈፀም የሚቀር እንደሌለ እንድታረጋግጥና በውስጥህ የገባውን ጠላት የዘራብህን ጥርጣሬ እንድታስወግድ ታስቦ የተዘጋጀ ነው፡፡ የነኖህ፣ የነአብርሃም፣ የነሙሴ የእምነት ልጅ አምላካችን የተናገረውን አያደርግም ብሎ አይጠራጠርምና፡፡

ልዑል እንዲህ ይላል ! ኖህ ገና ስለመይታየው ነገር ተረድቶ እግዚአብሄርን እየፈራ ቤተ ሰዎቹን ለማዳን መረከብን በእምነት አዘጋጀ፤ በዚህም አለምን ኮነነ፤ በእምነት የሚገኘውን ጽድቅ ወራሽ ሆነ፡፡ እብራውያን 11 - 17

ባለመስማትህ፣ ፍርዱንም በማቃለልህ፣ በእውቀትህ፣ በሃብትህ፣ ተመክተህ በመታበይ የመጀመሪየውን የእሳት ወንፊት እያየኸውና በውስጡም ገበተህ እየተበጠርክ ትገኛለህ፡፡ በዋነኞቹ በቀደሙት ሶስት መልእክቶች / 1 ፣ 2 ፣ 3 /የተገለፁትን ፍርዶቹንና አፈፃፀማቸውን እንደተገለጸው ሁሉ የመጀመሪያውን እሳት እያየነው እንገኛለን፡፡ ስለቀጣዩ ምን እንደሚሆን መግለጽ የዚህ መልእክት ተልእኮ ይሆናል፡፡

የሰረዊት ጌታ ልዑልና ቸር ይቅር ባይ መሃሪ፤ ለቁጣው የዘገየ የፍቅር ምንጭና የህይወት ሁሉ ጌታ ስሙ ይክበር ይመስገን አሜን፡፡ ዘመናትን ፍጥረታትን የሚታዩ የማይታዩትን የፈጠረ፤ በእኛ አእምሮ ሚዳሰሰውንም ሆነ ፍጹም ሊታወቅ የማይቻለውን የፈጠረ፤ ልዑል ጌታ ስሙ ይባረክ ይመስገን፡፡ አሜን !! የግለቱ መጠን በምንም መስፈሪያ የማይለካ፤ የብርሃን መጠኑም በምንም መስፈሪያ የማይመዘነውን፤ የእሳት መፍለቂያ ፈጥሮ የሚያዝዝ፣ የሚናዝዝ፣ ከአዕምሮአችንም በላይ ለሆነው ልዑልና ኃያል ጌታ ምስጋና ዘወትር ይፍሰስለት ! እጅግ ከከበሩት ቅዱሳት መላእክት እውቀት፣ ኃይል፣ ማስተዋልና መረዳት በላይ ፍጹም የረቀቀ ድንቅ ጌታን ማንም በምንም መለኪያና አንደበት ገልፆ ሊወስነው የማይቻል አምላካችን ድንቅ ነው፡፡ እንዲሁ ብቻ እንደተሰጠን እውቀት መጠን ስሙ ይባረክ ይመስገን እንላለን፡፡

ዘመንም፣ ጊዜም፣ስፍራም፣ ሁኔታም፣ጨለማም፣ ብረሃንም፣ ሌትም ቀንም፣ ሳይገታው ለሱ ለአብ፣ ለወልድ፣ ለመንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ ከፈጠረው ፍጥረት ሁሉ ሳያቋርጥ እንደ ንጹህ ምንጭ ውሃ፣ እነደ አርሞንኤም ጠል ዘወትር ከዘለአለም እስከዘለአለም ሳይቋረጥ ምስጋና ይፍሰስለት አሜን!!

እኔም እጅግ ታናሽ የምሆን ሃጢያተኛ ባርያው በሃጢያት በጨቀየና ባደፈው እንዲሁም ባልታረመው አንደበቴ አመሰግነዋለሁ፡፡ የተሰበረ ልብን ከንጹህ ህሊና የሚመነጭን ምስጋናና ምልጃን የማይንቅ አምላክ ነውና!! በእናቱ በቅድስተ ቅዱሳን በንጽህተ ንጹሃን ወላዲት አምላክ ምልጃ በፍቅሯ እቅፍ ልጆቹን፤ በደሙ የገዛን እኛን ባርኮ! ለመልካሙ ቀን ለእራቱ ግብዣ የጠበቀን ሁሌም ምስጋናን ለአምላካችንና ለልዑላችን ለሰራዊት ጌታ እግዚአብሄር ልናቀርብለት ይገባል፡፡ እጅግ በሚወዳቸው አልቆ ባከበራቸው የከበሩ ሊቀመላእክቶች /ቅዱስ ሚካኤል፣ ቅዱስ ገብርኤል፣ ቅዱስ ሩፋኤል፣ ቅዱስ ፋኑኤል፣ ቅዱስ ራጉኤል፣ ቅዱስ ሳቱኤል፣ቅዱስ አፍንኒኤል፣ ቅዱስ ሰዳኪያል፣ ቅዱስ ሱርያል፣ ቅዱስ ሰላትያል፣ ቅዱስ ራሙኤል/ ወገኖቹን እረኞቹንና ሕዝቦቹን ሌትም ቀንም በእሳት ከብቦ የሚጠብቅ ሃያል ጌታ አሁንም ሁሌም ከዘለአለም እስከዘለአለሙ ምስጋና ለከበሩት ቅዱሳን መላእክት አክብሮታችን ፍቅራችንና ምስጋናችን ይድረሳቸው፡፡ የኛም የባሮቹና የወገኖቹ አምላክ የከበሩት ቅዱሳተ መላእክትም አምላክ ነውና ምስጋና ዘወተር ለሱ ይፍሰስ አሜን፡፡

በዚህ ከፉ ዘመን ለምንገኝ የእግዚአብሄር ህዝቦች በታላቅ መንፈሳዊ ጀግንነት፣ በጽናተና ሰማእትነት ያለፉትን ስለኛ በልዑል ፊት የሚማልዱትን ሰማእቱ ጊዮርጊስን፣ ሰማእቷ አርሴማን እንዲሁም በቁጥር የበዙትን ሰማእተ ጀግኖችን ቅዱሳንን በልዑል ፊት ልናከበራቸው ልናምሰግናቸው ይገባናል፡፡የምልጃቸው የዘወትርና የጸሎት ድጋፋቸው ባለእዳ ነንና!!

የአዳም ዘር አድምጥ!! መሪ ሆንክ፣ ተመሪም፣ ሃብትም ሰበሰብክ፣ የጦር ክምችትም አደረግህ፣ ታበይክ፣ ተገሰልክ፣ በውሸት ቱልቱላህን አለምን ሸፈንክ፣ በፈለግኸው መንገድና ዘዴ ከነፍክ፣ በረርክ፣ የትም እንደማታመልጥ ገና  በቅንጣቷ እርምጃ ልክህን አውቀሃል ገናም እስከሚያንገሸግሽህ ትጋተዋልህ፡፡ ስለዚህ በጥንቃቄ አንብብ አስተውልም ተረዳ፡፡ መልእክቱን ለህዝብ እንዳይደርስ በማድረግ በስልጣንህ ተመክተህ በጠብመንጃህ ታብየህ የማምልጫ ቀዳዳህን ደፈንክ!!እንግዲህ መጭውን ደገግሞ ስማ!! የደፈርከው የፈጠረህን አምላክ ነውና!!

ይህ ለአምስተኛ ጊዜ የተሰናዳ መልእክት ለምን መጣ የሚል ጥያቄ በሁሉም የመልእክቶቹ ተከታታዮች ዘንድ የሚነሳ ጥያቄን እንደሚያስነሳ  ግልጽ ነው፡፡ የመጀመሪያው ሁለተኛውም ሆነ ሶስተኛው መልእክቶች ከ7/3/1998 ዓ.ም.ጀምሮ የአንድም ሆነ ሁለት አመት ቆይታ እያደረጉ መውጣታቸው በሁሉም ዘንድ የሚታወቅ ነው፡፡ ለ4ኛ ጊዜ የወጣው መልእክት ደግሞ በተለይ ለኢትዮጵያውያን የተዋህዶ እምነት የ..ወጣ ሲሆን በበቂ ሁኔታ የተዳረሰም ነው ተብሎ ይታመናል፡፡ ስለመልእክቱ እንደምታና ትግበራ አግባብ በሆኑ ርእሶች ውስጥ እናየዋለን፡፡

የዚህ መልእክት መውጣት በዋነኛነት የሚያተኩረው፤ ለእግዚአብሄር ህዝቦችም ሆነ በጠላትነት ለቆሙት ሁሉ አለም ያለችበትን ሁኔታና አቅጣጫዋን እግዚአብሄር ቃልና  በመልእክቶቹ ሚዛንነት የምናይበትና የምንረዳበት እንደሚሆን ሁሉም እንዲያውቀው እናስገነዝባልን፡፡ በተጨማሪም በመልእክቶቹ ሚዛንነት ሁሉንም ነገሮች በማስተዋል የምናይበትና የምንገነዘብበት ነው፡፡ በትክክል እየተጓዙ ላሉተ የእግዚአብሄር  ወገኖች ደግሞ እንዲበረቱ፤እንዲሁም የተጣመሙት እንዲቃኑ፣የሳቱትእንዲታረሙ፣የደከሙት እንዲነቁ  እናም የበረቱ ለሌላ ወንድማቸው መንፈሳዊ  ጉልበት እነዲሆኑ ጭምር በመታሰቡ ነው፡፡

ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን በሚለው ሙሉ መልእክቶች መልእክት 3 ገጽ 25 እነዲህ ይላል

በሁለቱም መልእክቶች እንደተገለጸው ዓለም ከ12/12/2000 ዓ.ም. ጀምሮ ወደማበጠሪያው ወፍጮ ገብታለች፡፡ ማበጠሪያው ትልልቁን ቆሻሻ የሚያስወግደው ሰፋ ያለ ቀዳዳዎች ባሉት የመጀመሪያ መሳሪያ ሲሆን፣ ሁለተኛው ከአንደኛው የጠበበ ሶስተኛው ከሁለተኛው እየጠበበ የሚመጣ የእሳት ወንፊት ጀምሮኣል፡፡ አጅግ ከበዶም ይቀጥላል፡፡ ይላል!!

ከመልእክቱ ጭብጥ እንደምንረዳው የእሳት ወንፊቱ ጅምሩን አሳየን እንጂ ገና ሰልፍና ወረፋ ይዞ የሚጠብቀንን የጥፋት ማእበል አላየነውም፡፡ በልዑል ግምጃ ቤት ለጥፋትም ይሁን ለበረከት ምንም ዓይነት መጠንና ልኬት የማይበጅለት በሰውም ይሁን በሌላ ፍጥረት የማይገመት ክምችት አለ፡፡ የምንበጠርበት የእሳት ወንፊት ኩጥር የለሽ ነው፡፡ በቀጣዩ በዝርዝር እንደምናየው የእግዚአብሄር የቁጣ ፍሰት አመጻኞችን፣ ትእቢተኞችን፣ የዲያቢሎስ ደቀመዝሙሮችን፣ ሃሰተኞችን፣ጨካኝ ገዢዎችንና ምንዝሮቻቸውን በቃሉ የሚነግዱ ደፋሮችን አመንዝሪና ግብረ ሰዶሞችን፣ ነፍሰ ገዳዮችን፣ ነጣቂ ዘራፊዎችን፣ በሃበትና በእውቀታቸው የተመኩትን ልዑልንና ቃሉን የካዱና ያቃለሉትን፣ ዘረኞችን በደሙ የገዛቸውን ያስጨነቁ ሁሉ፤ ከምድረ ገጽ እስከሚጠፉ ድረስ፤ እንዲሁም በፍርድ ተጠርገው እስከሚካተቱ፤ እንዲሁም እንደመልእክቱ አሜን ብለው እጃቸውን ለእግዚአብሄር ባሮች እስከሚሰጡና እስከሚንበረከኩ ድረስ የቁጣው ፍሰት መጠኑን እየጨመረ ይሄዳል እንጂ አይቆምም፡፡

ከላይ ስለተጠቀሱት አመጸኞች ልዑል ምን አለ...............

እውነትን በአመጻ በሚከለክሉ ሰዎች በሃጢያተኝነታቸውና በዐመጻቸው ሁሉ ላይ የእግዚአብሄር ቁጣ ከሰማይ ይገለጣልና እግዚአበሄር ሰለገለጠላቸው ስለ እግዚአብሄር ሊታወቅ የሚቻለው በእነርሱ ዘንድ ግልጽ ነውና፡፡ የሚታየው ባህርይ እርሱም የዘለአለም ሃይሉ   ደግሞም አምላክኑ ከአለም ፍጥረት ጀምሮ የተሰሩት ታውቆ ገልጦ ሆኖ ይያልና ስለዚህም እግዚአብሄርን እያወቁ እንደ እግዚአበሄርነቱ መጠን ስለአላከበሩትና ስላላመሰገኑት የሚያመካኙት አጡ፡፡ ነገር ግን በሃሳባቸው ከንቱ ሆኑ የማያስተውለውም ልባቸው ጨለመ፡፡ ጥበበኞች ነን ሲሉ ደንቆሮ ሆኑ የማይጠፋውን የእግዚአብሄርን ክብር በሚጠፋው ሰውና በወፎች አራት እግር ባላቸውም በሚንቀሳቀሱትም መልክ መስለው ለወጡ፡፡

ስለዚህም እርስ በእርሳቸው ስጋቸውን ሊያዋርዱ እግዚአብሄር በልባቸው ፍትወት ወደ እርኩስነት አሳልፎ ሰጣቸው፡፡ ይህም የእግዚአብሄርን እውነት በውሸት ስለለወጡ በፈጣሪም ፈንታ የተፈጠረውን ስላመለኩና ስላገለገሉ ነው፡፡ እርሱም ለዘለአለም የተባረከ ነው፡፡ አሜን፡፡ ስለዚህ እግዚአብሄር ለሚያስነውር ምኞት አሳልፎ ሰጣቸው ሴቶቻቸውም ለባህሪያቸው የሚገባውን ስራ ለባህሪያቸው በማይገባው ለወጡ፤ እንዲሁም ወንዶች ደግሞ ለባህሪያቸው የሚገባውን ሴቶችን መገናኘት ትተው እርስ በርሳቸው በፍትወት ተቃጠሉ ወንዶችም በወንዶች ነውር አድርገው በስህተታቸው  የሚገባውን ብድራት በራሳቸው ተቀበሉ፡፡ እግዚአብሄርን ለማወቅ ባልወደዱት መጠን እግዚአብሄር የማይገባውን ያደርጉ ዘንድ ለማይረባ አእምሮ አሳልፎ ሰጣቸው፡፡ አመጻ ሁሉ፤

ግፍ፤ መመኘት፤ ክፋት ሞላባቸው፡፡ ቅናትን፣ ነፍስ መግደልን፣ ክርክርን፣ ተንኮልን፤ ክፉ ጠባይን ተሞሉ፡፡ የሚያሾከሽኩ ሃሜተኞች፣ አምላክን የሚጠሉ፣ የሚያንገላቱ ትእቢተኞች፣ ትምክህተኞች፣ክፋትን የሚፈላልጉ፣ ለወላጆቻቸው የማይታዘዙ የማያስተውሉ፣ ውል የሚያፈርሱ፣ ፍቅር የሌላቸው፣ ምህረት ያጡ ናቸው፡፡ እንደነዚህ ለሚያደረጉት ሞት ይገባቸዋል፡፡ የሚለውን የእግዚአብሄርን ህግ እያወቁ እነዚህን ከሚያደርጉ ጋር ይስማማሉ እንጂ አድራጊዎች ብቻ አይደሉም፡፡

ወደ ሮሜ ሰዎች ም፤ 1 ፤ 18 – 32

የሰው ዘር ልብ በል ከጠፋህም ምን ይደረግ እያደመጥከው እያየኸው መጥፋት ነው፡፡ ፍርድህን ጉዞህንም እየተመለከትከው መሄድ ነው፡፤

የዚህ መልእክት ዳሰሳ ሰፊና ማስተዋልን፤ ግንዛቤን፤ ትእግስትን፤ የእምነት ጽናትን፣ ለመላው የእግዚአብሄር ህዝብ ለማስጨበጥ እንደታለመ ሁሉ በቃሉም ሆነ በዋናው መልእክት / ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን / በመልእክት 3 ገጽ 3 እንደተገለጸው

የመዋቀሻው ዘመን አልፏል ፡፡ አሁን በይናችሁ እንደምታዩት ፣ በጆሮአችሁም እንደምትሰሙት ዓለም በምጥ ጅማሮ ውስጥ ናት፡፡ ስለሆነም ከእግዚአብሄር አገልጋዮችና ባሮች መንፈሳዊውንም ሆነ ስጋዊውን አመራር፣ እንደ ልዑል ትእዛዝና ፈቃድ መስጠት ግድ ነው፡፡ የኔም ሆነ የወንድሞቼ የሃለፊነት ግዴታም ነው፡፡ ጭንቁም እየበረታ ሲመጣ በጎችን ማረጋጋት፣ መጽናናት፣ ማጽናት ወደ መልካሙ ስፍራ መምራት አለብንና !!

ለመንጋው መሰማሪያ መመሰጊያ፣ መጠለያ ማሳየት ወደዚያም መምራት የእረኞች ግዴታ ነው፡፡ ከበጎቹ መቀላቀል የማይገባቸውን ፍየሎች፣ ተኩላዎች በፍርድ እንዴት እንደሚጠበቁ፣ ማረፊያቸውንም የውቂት ዘነድ ማድረግ የግድ ይላል፡፡ ተግሳጽን ንቀው፣ ትዛዝን አፍርሰው፣ በአመጽ አድገው፣ በክፋት አርጅተው፣ ለመልካሞች እንቅፋትና ጥፋት ሆነው ሁሌም እንደማይቀጥሉ ዳኛው ልዑል በቃሉ መሰረት እንደሚፈርድባቸው ሊያውቁት ይገባል፡፡ ይህንንም ሃላፊነት የተሸከሙ የበጎች እረኞች ከመንጋቸው ተኩለዎችን ማራቅና በጌታ ቅን ፍርድ ስፍራቸውን ማስያዝ ይጠበቅባቸዋል፡፡

ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን መልእክት 3 ፣ ገጽ 3 ይላልና መልእክቱ ሰአቱን ጠብቆ የመጣ ነው፡፡

ስለዚህ ወንድሞችን ብታሳስብ በእምነትና በተከተልከው በመልካም ትምህርት ቃል የምትመግብ የኢየሱስ ክርስቶስ መልካም አገልጋይ ትሆናለህ፡፡ ነገር ግን ለዚህ ዓለም ከሚመችና የአሮጊቶችን ሴቶች ጨዋታ ከሚመስለው ተረት እራቅ፡፡ እግዚአብሄርን ለመምሰል ግን ራስህን አስለምድ፡፡ ሰውነትን ለስጋዊ ነገር ማስለመድ ለጥቂት ይጠቅማልና፡ እግዚአብሄርን መምሰል ግን የአሁንና የሚመጣውን ህይወት ተሰፋ ስለአለው ለነገር ሁሉ ይጠቅማል፡፡

ወደ ጢሞትዮስ 1 ፡ 4፡ 6 – 8

ይህ ዘመን እጅግ ክፉ ዘመን ነው፡፡ በተለይም በአምላካችን የታመኑትን በውጊያው ግንባር

ቀደምት የሆኑትን የልዑል ባሮችና እረኞች በእጅጉ የሚፈተን መሆኑን ልታውቁና ልትረዱ ይገባል፡፡ በጎችን መጠበቅ፣ ግልገሎችንና ጠቦቶችንም ማሰማራት ልዑል የሰጠው ታላቅ ኃላፊነት ነው፡፡ ዘመናችን ካቶሊኮች፣ መናፍቆች ተሃድሶዎች፣ ቅባቶች፣ ተረት አምላኪዎች፣ ጣኦትንና ቀጥታ ዲያብሎስን አምላኪዎችን ከመንጋው አርቆ መጠበቅን የሚሸፍን ታላቅና በልዑል የከበረ ስራ ነው፡፡ ለታመንለት አምላካችን ታዘዝ ለወገኖቻችን ትክክለኛውን መንገድ ልናሳያቸው አስፈላጊና ሁሌም የምንተጋበት ስራችን ሊሆን ይገባል፡፡ ተኩለዎችን ደግሞ በፍረዱ ቃል እንዲገሰጹ፣ ለቅጣቱም እንዲጠበቁ ልዑል በሰጠን መንፈሳዊ ስልጣናችን አስረን ለመጨረሻው የቅጣት ሰአት እንዲጠበቁ ማድረግ ማለት ነው፡፡

ከለይ ለመልእክቱ መግቢያ የሚሆነውን ጥቅል ማገናዘቢያ አሰቀድመናል፡፡ ቀጣዩ በዝርዝር የምናያቸውን ርእሶች እያየን ወደ ትንታኔአቸው በማለፍ በዝርዝር ካስቀመጥን በኋላ መልእክቱን እንደመድማለን፡፡

## የሚተነተኑ ርእሶች

1. ቀደምት መልእክቶችን / 1 ፣ 2 ፣ 3 / እናም መልእክት 4 /በኢትጵያውያን የተዋህዶ ልጆች/ ዓለምም ኢትዮጵያውያንም እንዴት ተቀበሉት፡፡

2. ከመልእክቶችህ መውጣት በኋላ ዓለም ምን ገጠማት፤ አሁንስ በምን ሁኔታ ላይ ትገኛለች፡፡ በመልእክቶቹ አንጻር ቅጣቱ በምን መጠን እየተከናወነ ይገኛል፡፡
3. ከዚህ ሁኔታ በኋላ መጪው ምንድነው
4. ኃያላን መንግስታትና ቀደምት የወጡትን መልእክቶች አቀባበላቸውና እንዲሁም ቀጣዩ እጣ ፈንታቸው
5. የተለያዩ የእምነት ተቋማትና ስለ መልእክቶቹ ያለቸው አሰተያየት፤ በመጪው ቀጣይ 2ኛ ደረጃየእሳት ወንፊት እጣ ፈንታቸው፡፡
6. በዘህ ዘመን በመልእክቶቹ የፍርድ ሚዛን ውስጥ የወደቁት መሪዎችና ጭፍራዎቻቸው በቀጣዩ እርምጃ ምን ገጥሟቸዋል፡፡
7. በመጀመሪያ የእሳት ወንፊት የተደረገ ብጠራና በቀጣዩ የሁለተኛ ደረጅ የእሳት ወንፊት መጪ ሁኔታ በንጽጽር ሲታይ፡፡
8. አገራችን ኢትዮጵያ በመጀመሪየውና በመጪው ወንፊት ውስጥ፤ እንዲሁም ገዥና ምንዝር ሹማምንቶች እጣ ፈንታ

   ሀ/ የተዋህዶ ቤተ ክርስቲያናችን ያለችበት ሁኔታና ቀጣዩ የልዑል እርምጃ ስለመሪዎችዋ፣ ስለካህናቶችዋ፣ ስለወጣቶቹዋ፣ ስለገዳማት፣ስለ መነኮሳት እንዲሁም ስለምእመኖቹ
   ለ/ በአገራችን የተለያዩ እምነቶች ስራና እንድምታው በመልእክቶቹ ሚዛንነት ቀጣዩ እጣቸው፡፡
   ሐ/ የፓለቲካው ስርአት ተጠቃሚና አራማጆች በአገራችን ላይ እየፈጸሙ ያሉት ጥፋትና መላ አገሪቱን የዳሰሰ ወንጀላቸው፡፡ በሁለተኛ ደረጃው የእሳት ወንፍት ውስጥ ዕጣ ፈንታቸው፡፡
   መ/ ኢትዮጵያውን የተዋህዶ ልጆችና በእስካሁን የመጡት ጎዳናና ከጽናታቸው ከልዑል አባታቸው፣ ከእናታችን ደንግል፣ ከቅዱሳን የከበሩ መላእክት የሚፈስላቸው በረከት፡፡
9. አውሮፓና በመልእክቶቹ አንጻር ያለፈችበትና በሁለተኛው የእሳት ወንፊት የሚገጥማት ዕጣ
10. ሰሜን አሜሪካና በመልእክቶቹ አንጻር ያለፈችበትና በ2ኛው የእሳት ወንፊት የሚገጥማት ዕጣ
11. ኤሽያ በመልእክቶቹአንጻር ያለፈችበትና በ2ኛው የእሳት ወንፊት የሚገጥማት ዕጣ
12. አውስትራሊያ በመልእክቶቹ አንጻር ያለፈችበትና በ2ኛው ዙር የእሳት ወንፊት የሚገጥማት ዕጣ
13. ደቡብ አሜሪካ በመልእክቶቹ አንጻር ያለፈችበትና በ2ኛው ዙር የሚገጥማት የእሳት ወንፊት
14. አፍሪካ በመልእክቶቹ ምዘና ያለፈችበትና በመጪው 2ኛው ዙር የሚገጥማት የእሳት ማበጠሪያ
15. የእስካንዲኔቪያ አገሮች በመልእክቶቹ አንጻር በመጪው 2ኛው ዙር የሚገጥማቸው የእሳት ማበጠርያ
16. በተለይ አለምን ለመቆጣጠር በታለመ ንዩክለር፣ ኬሚካል፣ በዬሎጂካል፣ ኒዩትሮን፣ አልፎም በህዋ ላይ የተጠመዱ የጨረር የኒዩክለርም መሳሪያ ለታጠቁ አገሮች እጣ ፈንታ
17. ስለ አባቶች፣ እናቶች፣ ሰለወንድሞች፣እህቶች በጥቅሉ ስለተመረጡ የልዑል ባሮች/ አገልጋዮች/ ላይ የተፈጸመ ጥቃትና በዚህም ላይ ከልዑል የተሰጠ የቅጣት ውሳኔ፣
18. የእምነት መርከባችን /የኖኅ መርከብ/
19. ትንሽ መልእክት ለልኡል ባሮች
20. በመልእክቶቹ ስርጭት ለይ ሰለሚሰሩ ጥፋቶች እና ምጥቀታቸው
21. ሺው ዘመን ም ይላል ምንስ እንደሚሆን ያስረዳናል
22. ማጠቃለያ

# 1/ ቀደምት መልእክቶችን / 1 ፣ 2 ፣ 3፣ / እናም መልእክት 4 / ለኢትዮጵያውያን የተዋህዶ ልጆች/ ( ዓለምም ኢትዮጵያውያንም እንዴት ተቀበሉት )

ሰነፍ በልቡ እግዚአብሄር የለም የላል፡፡ በስራቸው ጎሰቆሉ ረከሱ በጎ ነገርን የሚሰራ የለም የሚያስተውል ልዑልን የሚፈልግ እንዳለ ያይ ዘንድ፣ እግዚአብሄር ከሰማይ የሰውን ልጆች ተመለከተ፣ ሁሉ አመጹ፣ በአንድነትም እረከሱ፣ በጎ ነገርን የሚሰራ የለም፣ አንድም ስንኳ የለም፣ ጉሮሮአቸው የተከፈተ መቃብር ነው በምላሳቸው ሸነገሉ፣ ከከንፈራቸው በታች የእባብ መርዝ አለ፣ አፋቸው መርገምንና መራራን ተሞልቶአል፣ ደምን ለማፍሰስ እግራቸው ፈጣን ነው፣ ጥፋትና ጉስቁልና በመንገዳቸው አለ፣ የሰላምን መንገድ አያውቋትምና፣ እግዚአብሄርን መፍራት በዓይናቸው ፊት የለም፣ ህዝቤን እንደ እንጀራ የሚበሉ፣ ሃጢያት የሚሰሩ ሁሉ በውኑ አያውቁምን! እግዚአብሄርን አይጠሩትም፣ በዚያ በታላቅ ፍርሃት እጅግ ፈሩ፣ እግዚአብሄር በጻድቃን ትውልድ ዘንድ ነውና! የድሆችን ምክር አሳፈራችሁ፣ እግዚአብሄር ግን ተስፋቸው ነው፣ ያእቆብ ደስ ይለዋል፣ እስራኤልም ሃሴት ያደርጋል፡፡ ዳዊት መ. 13(14)

ሁሉን ለናቃችሁ እግዚአብሄር የለም ለምትሉ ምድሪቱን የከደናችሁ ሁሉ አድምጡ!

በ7/3/1998 ዓ. ም. ዓለም ሁሉ ያደምጥ ዘንድ ከሰራዊት ጌታ የተላለፈ / መልእክት አንድ/ ለሁሉም የሰው ዘር የተበተነ ሲሆን፣ በተለይም ለዓለም ሃያላን መንግስታት በየኤንባሲዎቻቸው እንዲደርሱ ተደርጓል፡፡ መልእክቱ በአማርኛና በእጅ ጽሁፍ የተዘጋጀ ነበር፡፡ መልእክት አንድን ሁሉም እድል የገጠመው እያየው እያለ በ27/9/2000 ዓ.ም. 2ኛው መልእክት በአማርኛም በእንግሊዝኛም በኮምፒውተር ሕትመት ተጽፎ በመላው ዓለም ላሉ ሕዝቦችና መሪዎች ደርሶአል፡፡ ከዚህ ክስተት በኋላ ሁለቱም መልእክቶች የልዑልን ፍርድ ያዘሉ ናቸውና ለሁሉም የሰው ዘር እድል በመስጠት ፈጥኖ ንስሓ እንዲገባ በማስጠንቀቅ በጥፋት ጎዳና እየገሰገሰ ያለውን የአዳም ዘር ወደ ፈጣሪው ጉያ እንዲሰበሰብ ለማድረግ የተደከመበት ነበር፡፡ ሆኖም የሰው ልጅ ከመነሻውም የፈጣሪውን ምክር፣ ተግሳጽና አባትነት የናቀ ነበርና ለሺውች ዘመናት የሚፈስለትን የተመለሰ ምክርና ተግሳጽ አይቀበልም፡፡ አልተቀበለምም ምክንያቱ ደግሞ እግዚአብሄርን ለማወቅ የሚፈልገውና የሚደክመው ዓለም ከልጅነቱ ጀምሮ ባስጨበጠችው የእውቀት መነጽር በመሆኑ ሲሆን፣ ዛሬ የምናየው ጥፋትም ሊቃና ያልቻለው ብዙ የዘመኑን ትውልድ በምሁርነትና በእውቀት ካባ ሸፍኖ፣ እንዲመጻደቁና በተንሸዋረረ እይታቸው እየዘበቱና እየተቹ በእውነት እየተሳለቁ ወደ መፈጸማቸው እንዲሄዱ አድርጎአቸዋል፡፡ ልዑል የሰራዊት ጌታ የቅርብ አምላክ እንጂ የሩቅ አምላክ አይደለም፣ ከእውነት ቃል በመስማት እንዲያው በሞኝነት በማመን በዚያም ጸንቶ በተግባር አውሎ በተሰበረ ልብ፤ በቅንነት ተጉዞ ለዛሬው መመረጥ የደርስ ዘንድ ማንም አልወከለውም ነበር፡፡ በየስርቻው የወደቁ ማንም እዚህ ግቡ የማይላቸው ስለ በጎው ቀን በልዑል ጸድቀው ታትመዋል፡፤

እግዚአብሄር አንድ አይደለም ሁለት፤ ከ7  ሺ ዓመቶች በላይ ታገሰ ተሸከመ፣ ወቀሰ፣ገሰጸ፣ቀጣ፣ማረ፣መልሶም መላልሶም የሰውን ልጅ ሁሉ ዓመጻ በምህረት ከደነ፡፡ አያት ቅደም አያቶቻችን አጠፉ፣ ተጸጸቱ፣ ምህረቱን አፈሰሰላቸው፡፡ ዘመኖችን በዚሁ መልክ በምህረቱ ስፋት፣ በቸርነቱ ብዛት፣ በፍቅርነቱ ጽናት መለኪያ ባልተበጀለት ትእግስቱ እስከዚች ሰአት አዘለን፤ ነገር ግን ማን አስተዋለን? ማንም፡፡ ከ1998 ዓ.ም መጀመሪያ ጀምሮ የአለም የአመጽ ጉዞ የሚገታና የልዑል የዘመናት ትእግስት ማለቁንና ወደ ፍርድ ሂደት መግባቱን በማሳወቅ፤ ለአዳም ዘር በሙሉ የመጀመሪያው የፍርድ ውሳኔ አሳወቀ፡፡ ነገር ግን መልእክቱ የደረሳቸው የሚበዙት አቃለሉት በመቀጠል ከ2ዓመት ቆይታ በኋላ በ27/09/2000 ዓ.ም. የመጨረሻ የሆነውን የፍርድ ቃል ገለጸ፡፡ የሰው ትእቢት ማለቂያ የለውምና የልዑልን ፍርድ አቃለለ፣ ናቀ፣ እንኳን ሊተገብረው ሊሰማውም ተጸየፈ፡፤ ይሁንና የእግዚአብሄር ስራ ሰውም ሰማ አልሰማ አይቋረጥመና፤ በስተመጨለሻ ፍርዱን ወደአፈጻጸም የሚያሸጋግረውን ሁሉንም የዓለም አካል የሚዳስሰውን የአፈጻጸም ውሳኔ ከአንድ አመት ተኩል በኋላ በ19/07/2001ዓ.ም. ወጣ፡፡ መልእክቱ በአማርኛም በእንግሊዘኛም የወጣ ሲሆን፤ በዚህ መልእክት መውጣት ሰአት፤ ለየትያለው ነገር ቢኖር፤ ከመጀመሪያው እስከ አፈጻጸም ያሉት መልእክቶች በሙሉ አማርኛውም እንግሊዘኛውም በአንድ ጥራዝ በማተት እንግሊዘኛውን በአንድ ጥራዝ፤ አማርኛውም በአንድ ጥራዝ በማድረግ ለአለም ህዝብና ለኢትዮጵያ ሕዝብም በስፋት ለማዳረስ ተሞክሮአል፡፡

ከዚህ ሁኔታ በኋላ ለኢትዮጵያውያን የተዋህዶ አማኞች ብቻ የተመለከተ 15 ገጽ የያዘ መልእክት በ1/6/2002 ዓ.ም. እንዲወጣ የተደረገ  ሲሆን መልእክቱ በስፋት ሊዳረስ ችሎአል፡፡ ይህ መልእክት ለ3 ጊዜ ያህል ለአገሪቱ መሪ የተጻፈላቸውን  ብርቱ ማሳሰቢያ የያዘ ሲሆን የተቀረው ግን የአገራችንን አገዛዝ ማብቂያ ሰአት መድረሱን በመግለጽ የምህረትና የቅጣት እድልን ለገዢዎቻችን ሰጥቶ ነበር፡፡ ይሁንና በዚህ እድል ሳይጠቀሙበት ቀርተዋል፡፡ ቀጣዩን አጣቸውን በሌሎች ርእስ ውስጥ እናየዋለን፡፡ በጥቅሉም፤ አለምም ሆነች አገራችን እንደየእምነት መሰረታቸው፣ እንደየእውቀት ባለቢትነታቸው፣ ሁሉም የየራሱን ግምት አዘልና በአለም እውቀት በገበያው መነጽር በማየት ሀሳቡን ሲሰነዝር ቆየቷል፡፡

የአለም ህዝብ፣እንዲሁም ኢትዮጵያውን ላስታውሳችዋሁ! መልእክቶቹ ሁሉ/ 1፣ 2፣ 3፣ / ለኢትዮጵያውያን የተዋህዶ እምነት ተከታዮች / 15 ገጽ የያዘ መልእክት / እንደደረሳችሁ ከላይ ላስረዳችሁና ላስታውሳችሁ ሞክሬአለሁ፡፡  እጅግ ውስን ሰዎች ቢያደምጡም 99 ከ100 ወይም ከ10 ዘጠኙ እጅ ንቆ ትቶታል፡፡ እኔንም አጭበርባሪ፣ ቅዠታም፣ ገዢው መንግስት የላከው ሰላይ፤  ሌላም እጅግ ጸያፍ ስሞችን ቢለጥፉብኝም፣ ድርጊቱም፣ ባያመኝም፣ ተደሳቹም ዲያቢሎስ ቢፈነጥዝም፣ ለኔ ለግሌ ሽልማቴ፣ ልዑል የሰጠኝ  ትንሽ የመስቀሌ ሸክም ናት፡፡ አለም የኔን ስብእና ያጠናል፡፡ ከአገሬ መንግስት ጀምሮ የአለም ኃይላት ጭምር የጋራ ጠላታቸው አድርገውኛልና ተባብረው ያልተቋረጠ ክትትል ስልታዊ ጥቃት ሲያከናውኑ ኑረዋል፡፡ ግን ቀድሞም ነግሬአቸዋለሁ አማካሪአቸው ዲያቢሎስም ብልጥ ነው፤ ጥበብን አልተነጠቀምና፡፡ ከቀይ መስመር እንዳያልፉ በማድረጉ እስከአሁን በጠርዝ ቆመዋል፡፡

አቤቱ አንተን ጠርቻለሁና አልፈር፤ ከፉዎች ይፈሩ፤ በሲኦልም ዝም ይበሉ፤ በድፍረትና በትእቢት በመናቅም ፤በጻድቅ ላይ የሚናገሩ፤የሽነገላ ከንፈሮች ድዳ ይሁኑ፤ ባንተ ለሚያምኑ በሰው ልጆች ፊት ያዘጋጀሃት፤ለሚፈሩህም የሰወርሃት ቸርነትህ እንደምን በዛች፤በፊትህ መጋረጃ ከሰው ክርክር ትጋርዳቸዋለህ፡፡ ዳዊት 130 ( 31) ፤ 17 – 20

የሚደረገው ይደረግ ዘንድ ለሁሉም ሰአት ስላለው በዚህ አልገረምም፡፡ የሰው ዘር ብርቱና በቀላሉ የማይሰበር ልብ አለው፡፡ የፈጠረውን አምላክ ክዶ፣ ንቆ፣ ባልሰራው አለም፣ ባልሰራው የራሱ ገላ በስብእናው፣ በተሰጠችው ብናኝ እውቀት፣ በአጭር እድሜው፣ በሰበሰበው ሀብት፣ በያዘው ስልጣን ፍጹም በመታበይ የፈጠረውን አምላክ ምክርና ተግሳጽ  ይንቃል፡፡ መልእክቶቹ ሁሉ የመጡት እሱን እንደ ኖኅ ዘመን ሰዎች  እንዳይጠፉ እንደ ሰዶምና ገሞራው          እሳት እንዳይበላው ነበር፡፡ አልሆነም፡፡ አለምም

ኢትዮጵያውያንም (አለም አንድ መንደር ሆናለችና ) አልሰሙም፡፡ መልእክቶቹንም ናቁት እንጂ አልተቀበሉትም፡፡ ከጥቂቶቹ የታደሉት በስተቀር፡፡ ስለዚህ ያለመስማትን ፍሬ በዚህ የ5ኛው መልእክት ውስጥ ሁልህም የአዳም ዘር በሙሉ ትረደዋለህ፡፡ ሰው በደነገገው ስርአትና ህግ ብታምጽ፤ ሰው ፍጡሩ የሰው ዘር የሰራው ስለሆነ ምደራዊና ፈራሽም በመሆኑ የሁሉም ጌታ በሆነው ልዑል እግዚአብሄር ትዳኛለህ፤ እንደ ፈቃዱ ካደረግህ ታመልጣለህ፤ የራሱን የሁሉ ጌታን ትእዛዝና ፈቃድ ካቃለልህ ደግሞ የሚታደግህ ኃይል ሰማይም ብትወጣ ምድርም ብትገባ ስለሌለ የሚያድንህ የለም፡፡

## 2/ ከመልእክቶቹ በኋላ ዓለም ምን ገጠማት! አሁንስ በምን ሁኔታ ላይ ትገኛለች! በመልእክቶቹ አንጻር ቅጣቱ በምን መጠን እየተከናወነ ይገኛል!

መልእክቶቹ በሙሉ ጊዜ ወስደው ሁሉም ሰው ይረደው ዘንድ በማሰብ፤ በላቻኮለ ሁኔታ ተልእኮአቸውን እያረጋገጡ ይገኛሉ፡፡ ከመልእክቶቹ መከሰት በኋላ አለም ብዙ ጥፋት ገጥሞአታል፡፡ የመጀመሪያውን የእሳት ወንፊት ሁሉም ሰው እያየው ይገኛል፡፡ በአለም ላይ ሁሉ የጫጉላው ዘመን አልፏል፡፡ ዛሪ ስለአንድም ሁለትም ጥፋት ሰምተን ሳናበቃ በሌላ አቅጣጫ ደግሞ የሌላን  አደጋ መከሰት እንሰማለን፡፡

አለም -- የኢኮነሚው ቀውስ ንጧታል /ግሽበት፣ የበጀት ጉድለት፣የገንዘብ ቀውስ፣ የባንኮችና ኢንሹራንሶች ክስረት፣የጅምላ መሸቃቀጫዎች ውዥቀት፣ የመላክና የማስገባት መቀዝቀዝ፣ ጥልቅ የሆነ ኢኮኖሚ መቀዝቀዝ፣ ስራ ማጣት፣ ረሃብ፣ስደት፣የተለያዩ ንግዶች ክስረት፤ መንግስት እንደ መንግስት ያለመሆን፣ በየትኛውም የአለም ክልል በአሁኑ ሰአት ያሉ መሪዎች በሙሉ ማለት ይቻላል፣ ዘራፊዎች፣ አዘራፊዎች፣ ውሽታሞች፣ አመንዛሪዎች፣ ጉቦኞች፣ ጨካኞች፣ አታላዮች መሆን በተለይም እነደ አፍሪካ ባሉ አገሮች ከህዘባቸው ስጋውን በልተው፣ አጥንቱን ቆርጥመው የጨረሱ መሪዎች በስልጣናቸው መቀጠልና የማያፍሩ መሆናቸው፣ በጭካኔ የደሃውን ጉሮሮ ዘግተው በወጭ ባንኮች ብር የሚያጉሩ፡፡ ህዝባቸውን በታንክ በጀት የሚጨርሱ፤ ለስልጣናቸው ሁሉንም ወንጀል የሚፈጽሙ አይን አውጣዎችን  እያየን ነው፡፡/በሁሉም አለም ዙሪያገብ የኑሮ ውድነት ሰፍኖ ኑሮም እጅግ ተመሳቅሎ እናያለን፡፡ አዳዲስ ቀውሶችም ፈጥጠው መጥተዋል፡፡ ምሳሌም የሚሆነን ዛሬ በኃያላኑ ውስጥ አግጦ የመጣው የእዳ ቀውስ ነው፡፡ የአሜሪካ / የባቢሎን የመንግስት እዳ 16 ትሪሊዮን አልፎአል፡፡ የአውሮፓም በቁጥር አይገለጽ እንጂ ብዙ ትሪሊዮን ሆኖአል፡፡ ይህን ተከትሎ ጠንካራ ብራችን የሚሉት የሚወድቅበት ሁኔታ ተፈጥሮአል፡፡ እንደ ቻይናና ጃፓንን የመሳሰሉ አገሮች የጌታቸውን መውደቅ በስጋት አየተጠባበቁ ይግኛሉ፡፡

ይህንን የአለም የጥፋት ጉዞ እያዩ ያሉት የአገራችን መሪዎችና ታዛዦቻቸው በሚጠፉ አገሮች ባንክ ውስጥ ከዚህ ከደሀ ህዝብ ግጠው 8.6 ቢሊዮን የአሜሪካን ዶላር በተለያየ ስፍራ አከማችተዋል፡፡ የተባበሩት መንግስታት አካል የሆነው ዩ.ኤን.ዲ.ፒ     ያወጣው መረጃ ያመለክታል፡፡ በምትጠፋው አለም በዲያቢሎስ አባታቸው በመታመን የሚሰሩት ወንጀል እስከሚደመደመው ድረስ የማይቀም መሆኑን ያሳያል፡፡

የዮሐንስ ራዕይ 18 ፤ከ4 -24 ይመልከቱ፡፡  እንዲሁም ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን መልእክት 1 ገጽ 4-5 ያገናዝቡት፡፡

ዓለም በማህበራዊ ቀውስ እየታመሰች ነው / በየትኛውም የዓለም አካል የእርስ በእርስ ግጭቶች በአብዛኛው ስፍራ የሚታዩት የየእለቱ ክስተት ናቸው፡፤ በእምነት ፍጅት፣ በድንበር ፍጅት፣በስ ልጣን ውጊያ፣ ትራንስፖርት ....ጠና መውደቅ፣ የመንግስት በሕዝብ አመኔታ ማጣትና ሰሚ ማጣት፣ ዘወትር ከተሞች በሕዝብ መተራመስ የባቡር የአውሮፕላን፣ የመኪና አደጋ መብዛት፡፡ በመላው ዓለም የየእለት የኑሮ ወጥቶ የመግባት ዋስትና ማጣት ዓለም ፍጹም ስብእናቸውን በጣሱ፣ ሰው ቅርጽ በያዙ ልቡሰ ኢጋንንት እየተመራች መገኘቷ« ለሰው መብት ለስእብናው፣ ለኑሮው የሚጨነቁ፣ የሚያስቡና የሚተጉ መሪዎች፣ ሙሉ በሙሉ ከዓለም ገጽ መወገድ፡፡ በምትካቸው ፕሮቶኮላቸውን አሳምረው፣ ውሸትን፣ ጨካኝነትን፣ ራስ ወዳድነትን፣ ስለሌላው ደንታቢስነትን፣ የቦዘኔ ተግባርና አንደበትን የያዙ መሪዎች መተካታቸው፡፡ ሰርቀው፣ ዋሽተው፣ ገድለው፣የማያፍሩ ናቸውና ዘወትር ለሕዝብ ጥፋትን፣ጭንቀትን፣ ሞትን፣ረሃብን፣ስደትን፣የሚደግሱለት መሆናቸው፡፡ የራሳቸውን ዲያቢሎሳዊ ምኞት የሚያስፈጽሙበት ሕግ አውጥተው ፍርድ ገምድልነት አጽንተው የሚረግጡንን ማየት ሁሉም ሰው የሚመሰክረው ሆኖአል፡፡ መልእክቶቹ ከዚህ በመለስ የማይባለውን፡ የቅጣት ዓይነት ዓለም እንድታይ አድርገዋል፡፡ የቅጣቱ መጠንም የመጀመሪያ ደረጃ የእሳት ወንፊት መሆኑን የሰው ዘር ልትረዳ ይገባሃል፡፡ መሪዎች በየትኛውም የስልጣን ዘርፍና ዓይነት ይቀመጡ የልኡል ቅጣት ወይም የበረከቱ መሳሪያዎች ናቸው፡፡ ለቅጣት የዋሉትም ከመሰረታቸውም በዲያቢሎስ የተቃኙ ናቸውና፡፡     መልካም የሚባል ነገር በአእምሮአቸው ውስጥ አልተጻፈም፡፡ ለበረከት የዋሉት ድጋጎች፣ አእምሮአቸውም ሆነ ስብእናቸው በልኡል እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ የተቃኘ ስለሆነ ለሰው ዘር በሙሉ ደስታውና እረፍቱ

የሚሳሳላቸው ከልኡል የተሰጡ በረከቱ ናቸው፡፡  እነ ሙሴ፣ እነ ዳዊትን የመሳሰሉትን ማለት ሲሆን፣ በአመጹ ምክንያት ሰው ካጣቸው ሺዎች አመታቶች ተቆጥረዋል፡፡

ዓለም በፖለቲካው ቀውስ ውስጥ ናት፡፡ ሁላችንም ዓይን እንደሚያየው፣ ጆሮአችንም እንደሚሰማው፣ የፖለቲካ ቀውስ ሁሉንም አገር እያመሰ ይገኛል፡፡ ሕዝቦች ገዢዎቻቸውን እጅግ ጠልተዋል፡፡ መሪዎቻቸውም በሕዝብ ፊት የቀለሉ ሆነዋል፡፡ የትኛውም ዓለም አቀፍም ሆነ አገራዊ ውሳኔ አከባሪና አድማጭ የለውም፡፡ የምድሪቱ ገዢዎች ያደራጁዋቸው ሚዲያዎች ሁሉ ቀጣፊ በመሆናቸው አድማጭ አጥተዋል፡፡ ሁሉም ገዢ ሳያጭበረብር ስልጣን ላይ አልወጣም፡፡ የዘመኑ ገዢዎች ፍጹም ዲያቢሎሶች ለመሆናቸው ከዓለም ገጽታ የተረጋጋ ፖለቲካ የሚባል ነገር ከጠፋ ቆየ፡፡ የሕዝብ አመጽም የየእለቱ ተግባርና የማያቋረጥ ክስተትም ሆኖአል፡፡

ለተግሳጽ ለምድሩ ወይም ለምህረት ቢሆን
ሰው በሚኖርበት ዓለም ላይ
ያዘዘውን ሁሉ ያደርግ ዘንድ
ፈቃዱ ወደመራቸው ይዞራል
ኢዮብ ም፤ 37 ፡13

ሰው በልኡል ለመፈራረድ እንዲመጣ ጊዜ
አይወሰንለትም፡፡ ታላላቆችን ያለምርመራ ይሰባብራል
በእነርሱም ፈንታ ሌሎችን ያቆማል፡፡ ስራቸውን ያው
ቃልና፣ እንዲደቁም በሌሊት ይገለባብጣቸዋል፡፡
ኢዮብ ም፤ 34 ፡ 23 – 25

የሰው ዘር ልብ በል ከላይ የሚናገርህን ቃል አስተውል የእግዚአብሄርን ትእዛዝና ፈቃድ ከመፈጸም የሚያግድ ምንም ፍጥረትም ሆነ ሃይል የለም፡፡ ለፍርድ እንድትቀርብና የስራህን ውጤት እንድትቀበል ጊዜ ቀጠሮ የሚሰጥህ ለም! ስራህ በልዑል ይታወቃል፤ ፍርድህም ሳታስበው ይመጣል፡፡ መጥቶልሃልም፡፡

የህያዋን ሁሉ ነፍስ ፤ የሰውም ሁሉ መንፈስ በእጁ ናት፡፡

ኢዮብ  ም፤  12 ፤ 10

ዓለም -- በተፈጥሮ አደጋ መመታቷ / የመሬት  ነውጥ፣ ጎርፍ፣ እሳት፣ የሙቀት መብዛት፣ በረዶ፣ የመሬት መንሸራተት፣ ማእበሎች፣ ቶርኔዶ፣ ሱናሚ፣ ሃሪከን፣ ታይፉን፣ እንዲሁም ዓለም ስም ያላወ ጣችላቸው በሽታዎች ብዙ ዓይነት አደጋዎችን እያየች ሲሆን የመጀመሪያውን ምጥና አሳር እያየች ነው፡፡

ከላይ በክፊል እንደዘረዘርነው ዓለም ከመልእክቶቹ መውጣት በኋላ ዛሬም ያለ ያልተቋረጠ ሁሉን አቀፍ አደጋን፣ ቀውስን፣ ጥፋትን እያስተናገደች ትገኛለች፤፤

በእምነት ዙሪያ አስደንጋጭ ነገሮች እየታዩም ነው፡፡/ በተረት እምነት ተከታይ አገሮች ውስጥ ሙሉ በሙሉ ማለት በሚያስችል ሁኔታ ፍጅትና አመጽ ነግሷል፣ እነ ግብጽ፣ የመን፣ ሶሪያ፣ ሊቢያ፣ ባህራን፣ ቱኒዝያ፣ በመጠኑም ቢሆን አልጀሪያ፣ ሞሮኮ፣ ሳውዲአረቢ እናም ሌሎቹም አገሮች በአመጽ ታምሰዋል፡፡ ይህ ጉዞአቸው ጅምር እንጂ በመልእክቱ የተሰጠው ፍርድ እሰከሚፈጸምና ሁሉም የዓለም አገሮች ትልቅም ሆኑ ትንሽ ተንበርክከው ልካቸውን  አውቀው፣ በልኡል መቀመጫ ኢትዮጵያ ለሚነግሱት የልኡል ባሮች እጃቸውን ካልሰጡ የሚቀጥል ነው፡፡  ምድራቸው የምትረጋጋው ይህ ሲሆን፡፡ ከዚህ ውጪ መፍትሄ ፍለጋ የሚያደርጉት ድካም ከመድቀቅና ውድቀታቸው ከመከፋቱ ውጪ የሚመጣላቸው መፍትሄና መልካም ዘመን የለም፡፡ የገዢዎቻቸውን የጭንቀትና የመፍትሄ አመጠሁ ሩጫና ፕሮፖጋንዳ እንደተሰፋ በመመገብ ለሌላ የከፋ መከራ ከመንደርደር የዘለለ ሌላ የሚገኝ ማምለጫ የለም፡፡

ካቶሊኮችና ውርደታቸው፣ በውኑ ጆሮ አይሰማው የለምና ውድቀት ሲጀምር ውርደት የመጀመሪያው ጉዞ በመሆኑ ከካቶሊኮች እንግራለን፡፡  ሁሉም መሪዎችዋ በፍርሃት የተዋጡበት ፣ ሁሉም የጠለቁበትን የዲያቢሎስ ዋንኛ ስራ ይፋ ሆኖአል፡፡  ግብረ ሶዶምነት የዚችው ቤተ ክርስትያን መለያ ሆኖአል፡፡ ግብረ ሶዶምነት በተለይም እናት አባት የሌላቸውን ህጻናት በመርዳት ስም፣ ሰብስበው ያውም ጳጳሳት፣ አንድ ወይንም ሁለት አይደሉም በተለያዩ አገሮች በብዛት ተገኝተዉ የአለም ሁሉ መሳለቂያ የዜና ሽፋን ማድመቂያ ሆነዋል፡፡ ዲያቢሎስ ያረጋገጠው ነገር ቢኖር፣ ካቶሊኩም፣ መናፍቁም፣ ተረትና ጣኦት አምላኪውም፣ ሁሉም የራሱና ገንዘቡ መሆናቸውን ነው፡፡ በመላው አለም ጥንት የእምነት ቤት የነበሩ ዛሬ ሙዚቃ ቤት፣ ሲኒማ ቤት ሁነዋል፡፡ ከዚያ በዘለለ በአውሮፓም ሆነ

በአሜሪካ እምነት ተረት ሆኖአል፡፡ ስለዚህ ጥፋቱ ከዚህ በመለስ ሳይል ጀምሮአል፡፡ በዚህ መልእክት እንደሚገለጸው በብርቱ ከፍቶ ይመጣል፡፡ ጠላትንም ትቢተኛንም የዲያቢሎስን ልጅ ሁሉ ፍጹም ጠርጎ እስከሚያጠፋና እስከሚያንበረክክ ድረስ የሚቀጥል ይሆናል፡፡ ባጭሩ አለም የገጠማት መከራ መጠኑም አሁን በምናየው በደረጃ አንድ ውስጥ ይገኛል፡፡

ታላቁና ሁሉም ሊያስተውለው የሚገባው ነገር ቢኖር ይህ ነው፡፡ በስካሁኑ የመጀመሪያ ደረጃ እርምጃ ብዙዎች መሪዎች፣ አለምን ያጠፉ የዲያቢሎስ ዋንኛ መሳሪያዎች በዘረፉት ሃብት የሰከሩ ሞኖፓሊስቶች፣ የኢንዱስተሪ የአለም አቀፍ ባንክና ኢንሹራንስ ባለቤቶች፣ የአለምን ምስቅልቅልና ውድመት ከመጋረጃ በስተጀርባ ሆነው የሚያቀናብሩ፣ ጨካኝ ገዥዎች ከነእጅና እግሮቻቸው ገና አልተነኩም፡፡ እግዚአብሄር አምላክ የፍትህ አምላክ ነውና ማንም ከቅን ፍርዱ አያመልጥም፡፡ ቀድሞ ህዝቦቹን ይቀጣል፡፡ ለዚህም ነው ድሆች ሲሙቱ ፣ ሲሰቃዩ፣ ሲያጡ ሲነጡ፣ አደጋ ሁሉ ቀድሞ ሲመጣባቸው የምናየው፡፡ ልዑል የወደደውን ይቀጣል፡፡ በስጋ ይቀጣል፣ በነፍስም በስጋም ይቀጣል፡፡ የህ መረዳት የሌላቸው የዘመኑ መሪዎችና ባለ ሃብቶች ከነ ምንዝሮቻቸው ለምን እንደተጠበቁ አያውቁም፡፡ ልጁን ወደ በጎ ለመመለስ ያለ ርህራሄ የቀጣ ጌታ እኒህን የዲያብሎስ ልጆች ለብርቱ እሳት ማስቀረቱን አይረዱም፡፡ ሞትን እንዲጠሙት አድርጎ ሰው በዘመኑ ያላየውን ብርቱ ጥፋት አዘጋጅቶላቸዋል፡፡ ይህንንም በ2ኛው የእሳት ወንፊት ዝርዝር መግለጫ ውስጥ የምናየው ይሆናል፡፡

## 3 / ከዚህ ሁኔታ በኋላ መጪው ምንድነው !

ከለይ ባነሳናቸው ርእሶች፤ በመጠኑም ቢሆንም ያለውን ሁኔታ ተመልክተነዋል፡፡ የእግዚአብሄር ህዝብ በዚህ ባለው የመጀመሪያ ምት ወይም እንግዳ የሆኑ የአለም ክስተቶች ብዙዎች የመደናገጥ ስሜት ይታይባቸዋል፡፡ ጠላት የሚያርፍበትን በትር ምንም ቢያደቀው አለሁ ይላል እንጂ ተጎዳሁ አይልም፡፡ በመሆኑም ፉከራውና ፕሮፓጋንዳው የሚያስደነግጣቸው በእምነታቸው ብዙም ያልጸኑትን ለመሆኑ ጠንቅቀው የተረዱ ይገነዘቡታል፡፡ ከ1998 ዓ.ም በፊት ዓለም ብዙም የነካት ነገር የለም ነበር፡፡ ከመልእክቱ መውጣት በኋላ ግን ሁሉም ነገር ተቀየረ፡፡ ይህ የሆን ዘንድ ግድ ነው» ጊኤም የተሰጠው፤ በአለም የተተበተቡ ብዙ የእግዚአብሄር ህዝቦች ወደ አባታቸው ጉያ እንዲሰበሰቡ ብቻ ታስቦ እንጂ፤ እንደ አለም ጥጋብ፤ የአንድም ቀን እድሜ መስጠት ባልተገባ ነበር፡፡ አሁን ከምናየው የአለም ሁኔታ በዚሁ ቢቀጥል እንኳን ፤ አለም ! ለረጅም ጊዜ የመቋቋም አቅሙ የላትም፡፡ ይሁንና አመጽን የሚሸከም አነቀልባ ከእንግዲህ ስለሌለ ቀጣዩ ጥፋት ይመጣ ዘንድ እነሆ ግድ ሆኖአል፡፡ የዚህ መልእክት መምታትም ዋነኛው መንስኤ ይኸው ነው፡፡

መጪው ምንድነው፡፡ ከዚህ መልእክት መውታት በኋላ አለም ወደ ከፈውበሰው ህሊና ወደ መይገመተው የአለም ጥፋት ትሸጋገራለች፡፡ ዝርዝሩን በመጪዎቹ ረእሶች ውስጥ ታገኙታላችሁ፡፡

## 4/ ሃያላን መንግስታትና ቀደምት የወጡትን መልእክቶች አቀባበላቸው፤ እንዲሁም ቀጣዩ እጣ ፈንታቸው፡፡

-ትንቢተ ሕዝቅኤል ምእራፍ 26፤ እንዲሁም ምእራፍ 27ን ከዚህ በታች ለተጠቀሱት አገሮች በሙሉና አጃቢ  አገሮች በሙሉ በሁለተኛው የእሳት ወንፊት ውስጥ ከታዘዙት ቅጣቶች በተጨማሪ የሚፈጸምባቸው ይሆናሉና

-በማስተዋል ያንብቡት፡፡

በዚህ ርእስ ስር የምናያቸው የዓለም ሃያላንን መንግስታት እነማናቸው!

1/ አሜሪካን /ባቢሎን/  2/ ራሽያ 3/ እንግሊዝ 4/ ፈረንሳይ 5/ ቻይና 6/ ሕንድ 7/ ጀርመን

8/ ጃፓን 9/ ካናዳ 10/ አውስትራሊያ 11/ በራዚል 12/ ስዊድን 13/ ስፔይን 14/ ሆላንድ 15/ ጣሊያን

16/ ኢራን 17/ እስራኤል 18/ ኖርዌይ 19/ ግሪክ 20/ቱርክ 21/ ሳውዲ አረቢያ 22/ ግብጽ 23/ ኮርያ / ሁለቱም እነዚህ በቅደም ተከተላቸው የተቀመጡ አቅም አለን የሚሉ ናቸው፡፡ ከነዝህ የሚያንሱት ደግሞ በአመጻቸውም ሆነ በሃጢያት በተነከረ ተግባራቸው ከበኩሮቻቸው የማይተናነሱ ናቸው፡፡

እነዚህ አገሮች በሙሉ የተሟላው መልእክት በእንግሊዘኛ ተዘጋጅቶ የደረሳቸው ሲሆን ለሕዝባቸው እንዲገልጹ ማሳሰቢያ የተሰጣቸው ናቸው፡፡ ይህ ብቻ ሳይሆን በየአገሮቻቸው ያሉ ዩኒቨርስቲዎችና ሚዲያዎች ደርሶአቸዋል፡፡

ታዋቂ የሚባሉ ሚዲያዎች ሲ ኤን ኤን፣ አልጀዚራ፣ ፕሬስ፣ ቢቢሲ፣ ከደረሳቸው ዋንኞች ሚዲያዎች ናቸው፡፡ ከመጽሄቶች እነ ኒውስ ዊክ፣ ዘ ኢኮኖሚስት፣ ታይም ሁሉ ደርሶአቸው የተነፈሱት ትንፋሽ የለም፡፡

እነሀ ሁሉ ሰምተው፤ በእጃቸው ይዘው ለገዛ ሕዝባቸው የደበቁ የዲያቢሎስ ሰራተኞች ከምንላቸው ውጪ ሌላ ማን ሊባሉ ይገባል! ዛሬም እየሞቱና እየደቀቁ፣ እያዩት እኔ ከሞትኩ ሰርዶ አይብቀል እንዳለች አህያ ራሳቸውንም ሕዝባቸውንም ይዘው ሊጠፉ የቆረጡ ይመስላል፡፡ መሰላቸው እንጂ ከነሱ እውቀትና ብልጠት ይልቅ የእግዚአብሄር ሞኝነት ይጠበባል፡፡

መጪው እጅግ የበረታ ጥፋት በነዚህ መልእክቶቹን ባፈኑና በንቀትና በትእቢት በተጀሉ የዓለም ጉዶች ላይ ያነጣጠረ ይሆናል፡፡ ሞትን እንዲፈልጉት የሚያስገድድ ስፍር ቁጥር የሌለው በርባሪና አጥፊ እሳት ይላክላቸዋል፡፡ መልእክቶቹንም ቀንም ሌሊትም ባላቸው ሚዲያ ሁሉ ለፍልፈው ምህረት እንዲለምኑ ያደርጋቸዋል፡፡

መጪው በትርና እሳት ዛሬ ከሚያዩትና ካካለለው ስፋት በላይ፤ በማከል  መከራቸው 7 ጊዜ 7 ተባዝቶ 49 ጊዜ እጥፍ ጉልበት አምጥቶ ከምድር ሊጠርጋቸው ይመጣል፡፡ ትርጉሙንም በምሳሌ በሌላ ርእስ እናየዋለን፡፡

አልሰማ ላላችሁት ለእናንተ ምድሪቱንና የአዳምን ዘር ያሳታችሁና ለአባታችሁ ለዲያቢሎስ እንደመስዋእት የቀረባችሁ፡፡ ከመምህሩ ደቀመዝሙሩ እንዲሉ፤ ከአባታቸው ከዲያቢሎስ የበለጣችሁ ደቀ መዝሙሮቹ ናችሁ፡፡

ስለዚህም ጥፋታችሁ ምንም አይነት ጥበብና ብልሃት የማይከላከለው እስትንፋስ የማይሰጥ የትም ብትሸሹ የማታመልጡት እሳት ታዘላችኋል፡፡ በተለይ በፖለቲካውም፣ በእምነቱም፣ በፍርዱም፣ በሃይል ስምሪቱም፣ በመረጃ ስብሰባውም፣ በሃብት ማካበቱም፣ በጥንቆላውም፣ በምንዝርናውም፣በጭፍጨፋውም በጥቅሉ ልዑል ባወገዘው የአመጽ የኃጢያትና የትእቢት ስራ በግንባር ቀደምትነት የተሰለፋችሁ በየትኛውም ደረጃ ያላችሁ መሪ ተዋናዮቹ ትካተታላችሁ፡፡  የጥፋቱን የሃይል መጠን ዝርዝር በሌላኛው ርእስ ስር ታዩታላችሁ፡፡

## በሙሉው መልእክት / ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን መልእክት 3 ገጽ 83 /ይህን ይላል

ይህ የውሳኔ አፈጻጸም ከወጣና ከተፈለገው አቅጣጫ መሄድ ከጀመረ ከመጀመሪያው የመድረሻ ቀን ጀምሮ ዓለም የጠረጋውን ምንነት በሁሉም የዓለም ገጽታ፣ በሁሉም የሰው ዘር ኑሮ ዙሪያ ታያለች፡፡ ከዚች እለት ጀምሮ በቁጥር 1 በቁጥር 2 መልእክቶች የተጠቀሱት የቅጣት አይነቶች ይፈሳሉ፡፡ ማቆሚያ የላቸውም የትኛውም ብልሃትና ዘዴ አያቆማቸውም፡፡ እንዲያውም የሰው ልጅ ትእቢቱን ካጸና እጅግ ታየቶ የማይታወቅ ጥፋት በአለም ሁሉ ላይ ይሆናል፡፡

በዚህ ሰአት በአለም ሁሉ ያሉ የአገር መሪዎች፣ አለም አቀፍ ድርጅቶች ከነሹሞቻቸው፣ ከነአገልጋያቸው ግንባር ቀደም ተጠራጊ ይሆናሉ፡፡

ይህ ሊሆን ይህ መልእክት መጥቶልሃል፡፡

## 5/ የተለያዩ የእምነት ተቋማትና ስለመልእክቶቹ ያላቸው አተያይ

## በመጪው ቀጣይ የ2ኛ ደረጃ የእሳት ማበጠሪያ እጣ ፈንታቸው፡፡

ሁሉም የመላው ዓለም ሕዝብ እንደሚያውቀው፣ ምድራችን ስፍር ቁጥር በሌላቸው የእምነት ዓይነቶች የተሞላች ናት፡፡ ሁሉም እውነት ከኔ ጋር ናት ይላል፡፡ በጥበብ በሃብት በቁጥር ብዛት መስፈሪያ ራሱን ለማጽናት ሲደክምም ኖሮአል፡፡ እውነት አንድ ናት፡፡ ስለ እምነት ያለውም እውነት አንድ ብቻ ነው፡፡ እሱም ልዑል ዋጋ የከፈለባት የተዋህዶ እምነት ናት፡፡ ሌላ እምነትና እውነት የለም፡፡ ከሷ ውጪ ያለው ሁሉ ዲያቢሎስ ያደራጀው የአምልኮት መልክ ያለው፣ በቁጥርም በዝቶ አለምን የሸፈነው ወደ ጨለማ የሚወስድ እየወሰደም ያለ የጥፋት መንገድ ብቻ ነው፡፡  እስኪ እነዚህን ዋና ዋናዎቹን  ሕዝብን ይዘው እየጠፉ ያሉትን በአጭር በአጭሩ እንያቸው፡፡

እኔ የቅርብ አምላክ ነኝ እንጂ የሩቅ አምላክ አይደለሁም ፡፡ ሰው በስውር ቢሸሸግ አላየውምን? ሰማይንና ምድርን የሞላሁ እኔ አይደለሁምን ? ይላል እግዚአብሄር፡፡ ት.ኤርሚያስ 23፤ 23 – 24

የማሰማሪያየን በጎች ለሚያጠፉና ለሚበትኑ እረኞች ወዮላቸው፡፡ ት.ኤርሚያስ 23፤ 1

ሀ/ ካቶሊክ- ይህች እምነት ምን ትመስላለች እጣዋስ! በሙሉው መልእክት ውስጥ በመልእክት 3 ገጽ 26 – 30 ተበራርቶ የተገለጸ ሲሆን በአጭሩ በክርስትና ካባ ፣ በፍልስፍናና በእውቀት ተሞልታ ብዙ በእውቀት እምነት የተሞሉ ልዑልን በጥበባቸው ስለው የሚያመልኩ ሕይወት አልባ የሆኑ፣ ከእውነተኛው አስተምህሮ ከተዋህዶነት ቀድመው ተገንጥለው የወጡ ዛሬ በቢሊዮን የተቆጠሩ ሕዝቦችን ለዲያቢሎስ ምርኮ የሰጡ የልዑልን ሃይል ሰዎች የተሰባሰበባት ናት፡፡ በ431 ዓ.ም. የተፈጠረችው ካቶሊክ ዛሬ ልትከፍለው ግድ የሚሆንባት የብዙ በጎች --- ለሀሰተኛ ትምህርቷ ስትል ያፈሰሰች ናት፡፡ እንደምንሰማው ውርደቷ ቀድሞአል፡፡ ግብረ ሶዶም አለም --- የተዋህዶን እምነት ለማጥፋት በረቀቀ ስልት ዛሬም የምትደከም ናት፡፡ በተለይ በኢትዮጵያ ከመናፍቃን ጋር አብራ የተዋህዶ እምነትን በጥበብ፣ በአስተምህሮ ስም በእርዳታ ስም ለማጥፋት እየጣረች ያለች ናት፡፡ በኢትዮጵያ መንግስት ልዩ ድጋፍ ከሚደረግላቸው ከመናፍቃን ቀጥሎ ካቶሊክ ዋናዋ ናት፡፡ ይህች የእምነት ተቋም ከመጀመሪያው ጀምሮ የመልእክቶቹን መውጣት ተከትሎ ስውር አፍራሽ የዲያቢሎስ ስራ ስትሰራ ቆይታለች፡፡ መልእክቱም እንዳይሰራጭ ከሚደክሙት አንዷም ናት፡፡ መልእክቱ በይፋ በሚዲያ ከወጣ በቢሊዮኖች የተገነባው ቁጥር ቁጥር ብቻ ሆኖ እንደሚቀር በሚገባ ታውቃለች፡፡ ይሁን እንጂ ልዑል በሷ እስር ቤት ከታጎረው በቢሊዮን የተቆጠረ ሕዝብ በህይወት መዝገቡ ቀድሞም ያሰፈራቸው፣ እጅግ ጥቂት ወገኖች ስላሉ በንስሃ እንዲመለሱ እስከ አሁን ጠብቆአቸዋል፡፡ የዚህን ዘመን ሕይወት አድን እምነት መርከብ / የኖህ መርከብ/ የተሳፈሩትን የተገባቸውን ነጩን ልብስ የለበሱትን አሳፍራ ጉዞ የጀመረች በመሆኑ፣ የአሁኑ ቀጣዩ የከፋው ጥፋት ሲመጣ ግን ያልሰሙት በልዑል እርዳታ፣ ሰምተው በመርከቧ ተንጠላጥለው፣ ይተርፋሉ ተብሎ ይታመናል፡፡ የጭንቅ መዳን ልንለው እንችላለን፡፡ ከዚህ በተረፈ ካቶሊክ የዘራችውን ታጭድ ዘንድ፣ እጅግ ብዙ ሚሊዮኖቹአንና መሪዎችዋን ገብራ ስም አጠራሯ ሳይቀር ከምድር ፊት ይጠረጋል፡፡ በጭንቅ የሚተረፉም ካሉ ትቢያ ነስንሰው ራሳቸውን ፈጭተው በታመነበት ንስሃ ለአንዲቷ የኢትዮጵያ ተዋህዶ እምነት እጃቸውን ከሰጡ ብቻ ነው በምድሪቱ ማረፊያ የሚያገኙት፡፡ የዚህች እምነት ውስጥ በተለይ በአለሙ ሁሉ ያሉት መሪዎቿ እምነቱን በጥበብ በፍልስፍና ይዘው ያሉ ናቸው፡፡ ብዙ የቲኦሎጂ ኮሌጆች ያላትና በዚያም የሚበዙት አገልጋዮቿ፣ ቀሚስ ለባሽ ዲያቢሎሶች፣ቃሉን በፍልስፍና በጥበብ ሰንጥቀው፣ በይደውና ደርተው የተሸከሙ ናቸው፡፡እኒህን እየፈለፈለች ያለች ናት፡፡ የኛው አገር የተዋህዶ እምነታችን መሪ ጳጳሳት ዲግሪ ተቀብለናል፣ ዶክተር ሆነናል፣እያሉ እንደመልካም ዝና በአውሮፓና በአሜሪካ በሩስያና በአጎራባቾች ካሉ ቲኦሎጂ ዩኒቨርስቲዎች፣ የለቃቀሙትን ፍልስፍና ለበስ እምነት ተሸክመው መጥተው ለህዝብ መልካም ነገር ገብይተው እንደመጡ ሳያፍሩ ይናገራሉ፡፡ ልዑል በየትኛውም ትእዛዙ በጥበብ፣ በፍልስፍና ስበኩኝ አላለም፡፡ ሁሉም ሃዋርያት ሁሉም ነበያት ከፍልስፍናና ከጥበብ ትምህርት ቤት አልወጡም፡፡በፍልስፍና ትምህርት ቤት መግባት አላስመረጣቸውም፡፡ የእምነት ጀግኖቹ እነአብረሃም፤ እነጴጥሮስ፣እነኤሊያስ፣ እነዮሃንስ እንደምሳሌ ስናያቸው፤ ከየትኛው ኮሌጅ ወጡ! ዓለምን ያስደመሙ የእምነት ጀግኖች ዛሬም ላሉት የእውነት ምልክቶች ናቸው፡፡ ስለዚህ ካቶሊክ ከነምናምንሽ ከነዝግንትልሽ በበርባሪና በአውዳሚ እሳት ፍጹም ትጠረጊና ምልክትሽ እንኳን እንዳይገኝ ሆኖ፣ በሁለተኛው የእሳት ወንፊት መበጠራችሁ ይፈጸም ዘንድ፣ በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል ትእዛዙ ወጥቶአል፡፡

በዚህ ርእስ ስር ማስታወስ የሚሻን ነጥብ ቢኖር፤- ለኢትዮጵያ መባረክም ሆነ መመረጥ እንደምልክትም ሆነ እንደበረከት የሚታዩት በየገደሉ፣ በየመቃብሩ፣በየዱሩ ወንበር ዘርግተው፣ ቅጠል ቀልሰው፣ ዜማውን፣ ቅኔ ውን፣ ድጓውን፣ መጻህፍቱን በወጣቱ አእምሮ ውስጥ አፍስሰው መተኪያ የሌለውን እድሜያቸውን በሙሉ ለዚሁ ጌታ ለወደደው ስራ አውለው ዛሬ አለፈው አልፈው የሚታዩትን የአብነት ትምህርት ቤቶችን ተክለው አልፈዋል፡፡ ምትክ የማይገኝለትን የተዋህዶ እምነታችንን በአለቱ ላይ መስርተው ሄደዋል፡፡ ይህንን ንቀው ነው የዛሬዎቹ ዲያቢሎሶች የበግ ለምድ ከለበሰች ተኩላ ሳይንሳዊ እምነት ያመጡልን፡፡ ሁላችንም እንደምናውቀው ድንቅ የሆኑ ሊቃውንተ ቤተክርስቲያንን ፣ ጳጳሳትን፣ መምህራንን ለተዋህዶ እምነት በጽናት በመቆማቸው ሰርገው ገብተው ጠመንጃን ይዘው የተዋህዶ እምነታችንን ከሚያጠፉት ጋር ግልጥ ውጊያ ውስጥ በመግባታቸው በተለያየ ዘዴ / በተቀናበረ የመኪና አደጋ፣ በመርዝ/ እንዲወገዱ ተደርገዋል፡፡ በምትካቸውም የዲያቢሎስ የመናፍቅ፣ የካቶሊክ ምልምሎች እንዲተኩ ተደርጓአል፡፡ ስለዚህ ካቶሊክ የዲያቢሎስ መሳሪያ ናትና ፍርዱም ይገባታል፡፡

የጴጥሮስ መልእክት ሁለተኛው፤- ምእራፍ ሁለትን በሙሉ ጠንቅቀው ይመልከቱ ስለ መናፍቅም ሆነ ስለካቶሊኮች ምንነት በግልጽ የሚረዱበት የልዑል ቃል ነውና! ፍርዱም በዚሁ ቃል ተመስርቶ የወጣ ነው፡፡

## ለ/ ፕሮቴስታንት / መናፍቃን /

ይህ እምነት በስም አጠራሩም እንደሚታወቀው አመጽን እንደመንገድ የሚያዩ፣ በአመጽ የተጠነሰሱ፣ ዛሬም በአመጽ በሴራ የዲያቢሎስ ድርጅታቸውን እያስፋፉ ያሉ ናቸው፡፡ በመልእክቶቹ / ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን / በሚለው መልእክት 3 ገጽ 30 – 32 እንደተገለጸው ከካቶሊክ የተገነጠሉ ዘመናቸውን ሁሉ እንደአሜባ እየተገነጠሉ የሚባዙ እምነታቸውን ልክ እንደፖለቲካ አደረጃጀት አጭበርብረውና አታለው በመላው አለም እራሳቸውን ያስፋፉ የዲያቢሎስ የዘመኑ ድርጅቶች ናቸው፡፡ከካቶሊኮች በሚበልጥ ድርጅታዊ አሰራር ፖለቲካውንም ተላብሰው ገንዘብን ሰንቀው በመላው አለም ለሰዎች ጥፋትን ለዲያቢሎስ ግዳይን ዘወትር የሚያቀርቡ ናቸው፡፡

ከነዚህ ጋር መጨቃጨቅ ከዲያቢሎስ ጋር በአካል የመዋጋት ያህል ነው፡፡ መልእክቱንም ሁሉ በሹፈትና በፌዝ የተመለከቱ ናቸው፡፡ የልዑል፣ የድንግል፣ የቅዱሳን መላእክት፣ የሰማእታትና የነቢያት የሃዋሪያት መሰረታዊ ጠላቶች በመሆናቸው ከነሱ ውስጥ አንድም ሰው በምህረት መዝገብ አይታሰብም፡፡ በራሴም በተሰጠኝ ስልጣን በታመንኩለትና ባሪያውም ልጁም ሆኜ በማገለግለው እግዚአብሄር አብ፣ እግዚአብሄር ወልድ፣ እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ ስምና በእናቴ በወላዲት አምላክ ስም በወዳጆቼ በገበርኤል፣ በሚካኤል፣ በሩፋኤል፣ በፋኑኤል ስም ቃሌን አጸናለሁ ከምድሪቱ ሁሉ ካልጠፉ እኔ ለነሱ በፍጹም የማልተኛ መሆኔን አረጋግጥላችኋለሁ፡፡ ያውም በኢትዮጵያ ምድር በልዑል መናገሻ፣ እንኳን እነርሱ በአካል ቀርቶ ምልክታቸውም ሆነ ስም አጠራራቸውም አይታሰብም፡፡ ስለዚህ ከነዚህ ጋር በማንኛውም መልኩ ማህበራዊ፣ ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊ ትስስር ያለህ ሁሉ ! አብረህ በእሳቱ ትበላለህና ሰከንድ ሳታጠፋ አምልጥ ሌላ የምልህ የለም፡፡ ለነሱ የተደገሰው የሰው ልጅ ያላየው ጥፋት ነውና፡፡ እነዚህን የምትቀበል የተዋህዶ አገር የለችም፡፡ በነዚህ የአገራችንም የአለምም ተዋህዶ እምነታችንም ጠላቶች የየትኛውም የአለም ዜጋ የሁኑ የአገራችን ! መናፍቃን እስከ ሆኑ ድረስ ምንም አይነት ዘር ምልክት ሳይተውለቸው ፍጹም ከምድሪቱ ይጠረጋሉ፡፡ ያሳደጓቸውም እንስሶች ጭምር በኢትዮጵ ውስጥ እንዲኖሩ አይፈቀድም፡፡ አይደረግምም፡፡ ስለሆነም በየትኛውም አለም ስፍራ ሁሉ መናፍቃን ሁሉ በዚህ መልእክት በተጠቀሱ መቅሰፍቶች ሁሉ ይጠረጉ ዘንድ በልዑል ፈቀድና ትእዛዝ በካዱአት በእናቴ በድንግል ትእዛዝ በኔም በልዑል ባሪያ ተፈጻሚ ይሆን ዘንድ ታዞአል፡፡ እጅም መስጠት፣ እስትንፋስም ለናንተ የለም፡፡ በምንም የሚተው ቀዳዳ አይኖርም፡፡

*ቀዳዳ ለነዳታን እንዳልተተወ ሁሉ ፤ የልዑል ቃል እንዲህ ይላል ! ሙሴንም፤ እግዚአብሄር የቀደሰውንም አሮንን በሰፈር ተመቀኙአቸው፤ ምድርም ተከፈተች ዳታንንም ዋጠችው፤ የአቤሮንንም ወገን ደፈነች፤ በማህበራቸውም እሳት ነደደች፤ ነበልባልም ኃጥአንን አቃጠላቸው፡፡ መ. ዳዊት 105 ( 106 ) ፡ 16 -18 መናፍቃን የናንት እጣ ፈንታ ይህ ከላይ ያለው ቃል ነው፡፡*

**ሐ / እስልምና** ይህንን እምነት በተመለከተ ፤ በሙሉው መልእክት ፤ መል፡ 3 ገጽ 32 – 33 በዝርዝር ምታገኙት ሲሆን፤ ይህ እምነት በተረት ዓለም የሚዳክር በመሆኑ፤ ለብዙዎችም፣ ለራሱም ሰዎች ጥፋትን ደግሶ ውድመትን አንግሶ ራሱንም የነገሰበትንም ምድር ጭምር እያጠፋ ያለ እምነት ነው፡፡

ስለዚህ እምነት በመልእክት 1 ገጽ 7 ላይ እንደተመለከተው፤ ፍጹም ከምድር የሚጠረግ የጥፋት እምነት ነው፡፡ ይህ ጅምሩ ዛሬ በመላው አለም ላይ ጎልቶ ቢታይም ከዚህ መልእክት መውጣት በኋላ ፤ በ49 ጊዜ እጥፍ ጨምሮ ሰምተን የማናውቀው የእሳት ማእበል የሚጠርገው ነው፡፡ ከዚህም እምነት እግዚአብሄር የመረጣቸው ከማእበሉ ሾልከው የሚወጡ አሉ፡፡ ራሳቸውን በመጸጸት ወደ እውነተኛይቱ እምነት ወደ ተዋህዶ ይመለሳሉ፡፡ እጅግ በቁጥር ያነሱ ናቸው፡፡ ካሁኑ ብዛታቸው አንጻር ምንም አልተረፉም፡፡ የሚያስብላቸው ናቸው፡፡ የተረፉትም ለአንዲቷ የኢትዮጵያ ተዋህዶ እምነት እጃቸውን ከሰጡ ብቻ ነው በምድራቸው የሚኖሩት፡፡

በዚህ መልእክት በትእዛዞቹ ውስጥ የተጠቀሱት መቅሰፍቶችና ሁለተኛው የእሳት መጥረጊያዎች በሙሉ ይጠርጓቸው ዘንድ በልዑል ፈቃድ በኔ በባሪያው በኩል ትእዛዙ እነሆ ተገልጾአል፡፡

አቤቱ ጋሻዬ በሃይልህ በትናቸው አውርዳቸውም፣ ስለአፋቸው ኃጢያት ስለ ከንፈራቸውም ቃል መርገምንና ሃሰትን ስለሚናገሩ፣ በትእቢታቸው ይጠመዱ፣ በቁጣ አጥፋቸው፣ እንደይኖሩም አጥፋቸው፣ መ፣ ዳዊት 108 ( 109) ፤ 11 – 13

መ/ ቡዲሂዝም፤ ታኦይዝም፣ ሺንቶይዝም፣ ቡድሂዝም እና መሰሎቹ በሙሉ በግልጽ ጣኦትን የሚያመልኩ ናቸው፡፡ በነዚህም ሙሉ ጥፋትን የምናይ ሲሆን ስፍር ቁጥር የሌለውን ሕዝባቸውን የሚያጡና፣ ካላቸው ሕዝባቸው ከ20 እጅ 19 ኙን አጥተው የተረፉትም ቢሆን፤ለኢትዮጵያ ተዋህዶ እምነትና በዚችው የድንግል አገር ለሚጠናው የልዑል ዙፋን ሲንበረከኩ ብቻ ነው በምድራቸው በሰላም የሚኖሩት፡፡ አለበለዚያ ግን ጉልበቱን ከቀን ወደ ቀን እየጨመረ የሚሄደውን ጠረጋ እስከሚፈጽም ድረስ ያዩታል፡፡የሁለተኛ ደረጃው የእሳት ወንፊት በብርቱ ከሚፈስባቸው አገሮች ግንባር ቀደምም ናቸውና! ጥፋታቸው የአለምን ሕዝብ በብርቱ ያስደነግጣል፡፡ በኤሽያ ያሉ አገሮች ናቸውና መልእክቶቹ ለመንግስቶቻቸውና ለሚዲያዎቻቸው ደርሰዋል፡፡ በመሆኑም በዚህ መልእክት ውስጥ የተጠቀሱት ሁለተኛው የእሳት ወንፊትና ሌሎችም መቅሰፍቶች በሙሉ፤ ይፈስሱና ያጠፏቸው ዘንድ በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል እነሆ ታዞአል፡፡

ት. ኢሳኢያስ ም. 2፤ 12 --- 22፤ ት. ኢሳኢያስ ም. 24 ፤ 1 – 13፤ ትንቢተ ኤርምያስ ም.8፤2-3

ሠ/ በዚህ ርእስ ከአባሎቻቸው ቁጥር ማነስ አንጻር ባናነሳቸውም የተለያየ ስምና ዓላማ ያዘሉ፤ እምነት መሰል የዲያቢሎስ መሳሪያዎች ከላይ ከተጠቀሱት የተለየ እጣ የላቸውም ታላላቆቻቸው በእሳቱ ሲበጠሩና ሲጠፉ እነዚሁ አብረው ይጠፋሉ፡፡ በነዚህም ላይ የቅጣት ትእዛዞች ሁሉ ተፈጻሚ ይሆናሉ፡፡

ረ/ በመላው አለም ያሉ የተዋህዶ እምነት ተከታዮችን በተመለከተ - ዛሬ እንደምናየው በመላው አለም ጎልተው ስማቸው የሚጠቀስ ተዋህዶ እምነት አማኞች ግብጽ ካሉት በቀር የሉም ማለት ይቻላል፡፡ ከእውነተኛይቱ ተዋህዶነት ሸሽተው በተለያየ የዲያቢሎስ ትብታብ ተጠልፈው ስሙን ብቻ ያዘሉ እርግጥ ብዙ አሉ፡፡ ስሙን ማንጠልጠል ብቻውን አያድንም በምግባር በትክክለኛውና በቀጥተኛው የተዋህዶ እምነት ሲጸኑ እንጂ፡፡

ሁላችሁም ልታውቁት የሚገባው ዋናው ቁም ነገር ይህ ነው፡፡ በእምነቲቱ መርከብ የተሳፈሩ፤ የትኛውም የዓለም ክልል የሚኖሩ ኢትዮጵያውያንም ሆኑ የሌሎች አገሮች ዜጎች የተገባቸው ስለሆነ፤ የጽድቁን ነጩን ልብስ ለብሰዋል፡፡ በእምነቲቱ የእምነት መረከብ / የኖህ መርከብ / ተሳፍረዋል፡፡ ቀድመው እንደነዚህ ሊሳፈሩ የተገባቸው አንዳንዶች ደግሞ በተለያየ የአለም ትርፍ ስብሰባ ተሰማርተው ኮልኮሌአቸው በዝቶ ታንቀውና ታግተው ያሉ በተለይም ለዘመኑ የጥፋት አለቆች በእንጀራ ስም እያገለገሉ ያሉ ሁሉ የሰበሰቡት ጠፍቶ፤ ውድ ዋጋ ከፍለው የሚወዱአቸውን አጥተው እየተጎዱ በጥፋታቸው ሂደት ውስጥ ብርቱ ስብራትን እያዩ ንስሃቸውን ጨርሰው በመርከቢቱ ውጪ አካል ተንጠልጥለው በታላቅ ጭንቅ የሚድኑ ናቸው፡፡ ይህ ሁሉ መልእክት ሲፈስ በቸልታ በንቀት በጥርጥርም መንፈስ በመሞላት በያዙት ሃብትና ውዳቂ ስልጣን በመታመን፤ ጊዜአቸውን ስለጨረሱ ነው፡፡ ሁሉን አጥተው በስጋቸው ውድ ዋጋ ከፍለው በጭንቅ የሚድኑትም ለዚህ ነው፡፡ ከአለም ጥበብና ፍልስፍናን ሲቀላውጡ፤ በእጃቸው የነበረውን እንቁአቸውን ስለጣሉም ነው፤ ይህ ፈተና የሚያገኛቸው፡፡ መጻጸታቸውና ሃፍረታቸው ለረጅም ጊዜ አንገታቸውን እንዲደፉም ያደርጋቸዋል፡፡

ትንቢተ ህዝቅኤል ምእራፍ 8 ፡ ምእራፍ 9 አስተውለው ያንቡ ! የእግዚአብሄር ሕዝቦች ምልክት በግንባራቸው ላይ ተደርጓል፡፡ የልተደረገባቸው ደግሞ ማንም ለማያስቀረው ለታላቁ እሳት ይጣሉና ይጠረጉ ዘንድ ተወስኖባቸዋል፡፡ ይህም ተፈጻሚ ይሆናል፡፡

የመጀመሪው የእሳት ወንፊት ከመፍሰሱ በፊት የተገባቸው ለሁኑ ሁሉ በየትም የአለም ስፍራ ቢሆኑም በግንባራቸው ላይ የልዑል ማህተም፤ በቤተሰባቸውና እንዲድኑላቸው ለወደዱአቸው ሁሉ የእመቤታችንን የድንግልን ማህተም ተደርጎባቸዋል፡፡ ሙሉ ለሆነው ጥበቃ ለራሳቸውም ለቤተሰባቸውም ወደው ላስጠለሏቸውም በአስራ ሁለቱም ሊቃነ መላእክት፤ በሚካኤል፣ በገብርኤል፣ በሩፋኤል፣ በፋኑኤል፣ ግንባር ቀደምትነት በብርቱ እሳትና ጥበቃ ታጥረዋል፡፡ የልዑል፣ የድንግል፣ እጅግ የከበሩት የቅዱሳን መለእክት እንቁና የክብሩ ጌጥ ናቸውና፡፡ አንዳችም የሚነካቸው ቀርቶ ባለፉበት በረገጡበት መድረስ አይቻልም፡፡ በእነዚህ የእግዚአብሄር እንቁዎች ላይ እስከ ዛሬ ግፍ ለሰሩባቸው ዋጋቸውን ባደባባይ እንዲከፍሉ ይደረጋል፡፤ ዛሬም በሞቱባቸው ቀን ከከፋት የማይመለሱ ቢያንስ ለነፍሳቸው መጠለያ ለማግኘት እንኳን የመለመን እስትንፋስ እንዳያገኙ የለመዱትን ክፋት ሲያስቡና የሚያስቡ ሲከሰቱ ወዲያው በብርቱ ኃይል ይጠፈራሉ፡፡ ወደ ሞት ልመናም ይሸጋገራሉ፡፡ ሞት ከተቸራቸው ደግሞ እድለኞች ናቸው፡፡

ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን መለእክት 1 ገጽ 7 – 8 ፤ መልእክት 2 ገጽ 14 – 15 ፤ መልእክት 3 ገጽ 35 – 36 ፤ ገጽ 61 – 64 በጥንቃቄ አንብብና ተረዳ !!

## 6 / በዚህ ዘመን በመልእክቶቹ የፍርድ ሚዛን ውስጥ የወደቁት መሪዎችና ጭፍሮቻቸው በቀጣዩ እርምጃ ምን ይገጥማቸዋል !

ቢመከር ያልሰማ መከራ ይምከረው ይላል የአባቶች ብሂል፡፡ በዚህ ዘመን ያሉ መሪዎች ሙሉ በሙሉ ማለት ይቻላል ፍጹም አውሬነትን የተላበሱ፣ በግልጽም ዲያብሎስን የሚያመልኩና የሚታዘዙ የዘመኑ ጉዶች ናቸው፡፡ መልእክቶቹ ደግመው ደጋግመው መዘኑአቸው፤ እጅግ ቀለውም አገኙአቸው፡፡ ድሃ ሲመታ፣ በጎርፍ ሲጠረግ ፣ በማእበል ሲፈራርስ፣ እነደ ሃይቲ ከግማሽ ሚሊዮን በለይ ሕዝብ ሲበላ፣ በመሬት ርእደት ሲፈርስ አለም በኢኮኖሚ ቀውስ ስትታመስ፣ ደሃ በረሃብ ሲረግፍ፣ ሲሰደድ፣ ድሀው ወደ ሞት፣ መካከለኛው ወደ ድህነት ሲቀላቀል ፣ በከፍታ ያለው ወደ መካከለኛው እያለ ሲወርድ፣ ውሃ ሲወስድ አሳስቆ እንደሚባለው ጉደኛ መሪዎች ( የፖለቲካውም የሃይማኖቱም ) ከነጭፍሮቻቸው፣ ከነአገልጋያቸው፣በመጀመሪው በትር ስላልተጎዱ፣ በዘራፍ፣ ተሞልተው ለጥፋታቸው ዛሬም በትእቢት ሲፈነጩ ይታያሉ፡፡

ቀጣዩ እርምጃ ኃይልና ጉልበቱ ሁሉ አሁን ከምናየው በ49 እጥፍ ጨምሮ ተጭኖ መጥቷል፡፡ በተለይም እስከ አሁን እያላገጡ ባሉ መሪዎች ( የፖለቲካውም፣ የሃይማኖቱም፣ የጦሩም፣ የጸጥታውም፣ የሃብቱም ) አዛዥ ናዛዦች ከነጭፍሮቻቸው የትም ቦታ ቢወተፉ በማያመልጡበት እሳት ይጠረጋሉ፡፡ ሞትን ይራቧታል፣ ይጠሟታል አየገኙአትም፡፡ ሞት ይሸሻቸዋል፡፡ ከተገኘላቸውም ብርቱ ስቃይን አሳይቶ ይወስዳቸዋል፡፡ ሞትን ስላገኙት እድለኞች ናቸው ብለው የቀሩት አምሳዮቻቸው ይቀኑባቸዋል፡፡ የሰበሰቡት ሃብታቸው ይጠፋል፡፡ ቤተሰቦቻቸውም አብረው ይጠረጋሉ፡፡ ለምልክት የሚተውላቸው ነገር በፍጹም አይኖርም፡፡ የገነቡትም ይፈርሳል፡፡ የሰበሰቡትም ይበተናል፡፡ ወለዱ ዘርም አበዙ፤ ወገን የጎተ አምሳያቸውንም አደራጁ፤ ያመልጣል ብለው ባሰቡበት የአለም አካል ሁሉ ሸሽጉ የሚያመልጥ የለም እያዩት በብርቱ እሳት ይበላል፡፡ ሁሉንም ጥፋት በቁማቸው ያዩታል፡፡ በስተመጨረሻ እነሱ

ዘራቸውም የጥፋቱ መደምደሚያ ይሆናሉ፡፡ እነሱ ጠፍተው ፍሬዎቻቸውም ተጠርገው የዲያብሎስ ምልክቱም ሳይቀር ሁሉም በቁማቸው ወደ ምድሪቱ የእሳት ባህር ይገባሉ፡፡ እንደ ዳተን ምድር ተከፍታ ጉያዋ ትከታቸዋለች፡፡ ምልክትም ታሪክም የማያነሳቸው ይሆናሉ፡፡ በዚህ ጥፋታቸው መፈጸም ነፍሳቸው ወደ ሲኦል ለዘለአለሙ እሳት ወደምትጠበቅበት ትገባለች፡፡ ይህ ይፈጸምባቸው ዘንድ በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል በዚሁ መልእክት እንዲገለጽ ተደርጓል፡፡

## 7/ በመጀመሪያ ደረጃ የእሳት ወንፊት የተደረገ ብጠራና በቀጣዩ ሁለተኛ ደረጃ የእሳት ወንፊት መጪ ሁኔታ በንጽጽር ሲታይ

ዓለም የመጀመሪያውን የእሳት ወንፊት ከመልአክቶቹ መውጣት ጀምሮ በየጊዜው እያደገ በሚሄደው ምት እያየችው ትገኛለች፡፡ የመጀመሪያው እሳት በሁሉም አለም ገጽታ በትሩን እያሳረፈ ይገኛል፡፡ በመጠኑም ለማየት ያህል

- ርእደ መሬት ፡- ቢያንስ በወር አሊያም በሳምንት እየተከሰተ ይገኛል፡፡ ሃይቲን፣ ጃፓንን፣ ኒውዚላንድን፣ ቺሊን፣ ጣሊያንን፣ ኢንዶኔዢያን፣ እና ሌሎችንም እየመታ ይገኛል፡፡ ይቀጥላልም፡፡
- ጎርፍና እሳት፡- በተጣመረ አሜሪካንን ( ባቢሎንን )፣ አውስትራሊያን፣ ሜክሲኮን፣ አውሮፓን እየመታ ነው ይቀጥላልም፡፡
- ቶርኔዶ፣ ታይፈን፣ ሁሪኬን፣ ሱናሚ፣ ካተሪና እና ሌሎችም ስም የለሽ ማዕበሎች ኤሽያን፣ አሜሪካንን፣ ደቡብ አሜሪካንን፣ አውስትራሊያን በመጠኑም አውሮፓን እየመታ ሲሆን የማያቋርጥም ሆኖ ይቀጥላል፡፡
- እሳተ ጎሞራዎች፡- የተኙ ነቅተዋል፡፡ ሰው ያላየውንም ጥፋት ያመጣሉ፡፡ አሁንም እያጠፉ ይገኛሉ፡፡
- ርሃብ፣ ጦርነትና ፍጅት፣ ለአፍሪካ፣ ለነፓኪስታን፣ ለነአፍጋኒስታን ፣ ለነህንድ ተሰጥቶ እየሰራ ሲሆን በቀጣዩም ያልተካተቱ ተደምረው በብርቱ ከፍቶ ይቀጥላል፡፡
- በሽታ ፤- በመጠኑም እያጠፋ ቢሆንም እጅግ ታይቶ በመይታወቅ ኃይልና አይነት ሲመጣ ምልክት እየሰጠ ይገኛል፡፡ ትራንስፖረት በሁሉም አለም አደጋ በዝቶታል፡፡
- ኢኮኖሚ ተመሰቃቅሎአል፣ የገንዘብ ቀውስ፣ የባንክና የኢንሹራንስ መውደቅ፣ የበጀት ጉድለት፣ ግሽበት፣ ሪሴሽን፣ ስራ ማጣት፣ የኑሮ ውድነት፣ የየእለቱ ክስተት ሆኖአል፡፡ ይቀጥላልም፡፡
- የህዝብ አመጽ ከፍቷል፣ ያልደረሳቸውን ጨምሮ ከፍቶ ይቀጥላል፡፤
- የእምነት ግጭት፣ የዘር ግጭት፣ የድንበር ግጭት ሁሉም አሁን ካሉት ከፍተው ይቀጥላሉ፡፡
- መንግስትን እንደ መንግስት የቆሙ ኃይሎች፣ ወታደራዊ ኃይል፣ የጸጥታ ኃይል የማይታዘዝ ወደ መሆን እየገሰገሰ ይገኛል፡፡ ይሆናልም፡፡
- የኒዩክሊየር ቀውሰ መታየት ጀምሮአል፡፡ ይቀጥላልም፡፡
- የሙቀት መጠን እጅግ ከፍቶ ታይቷል፡፡ በሪኮርድም ያልታየ ሆኖአል፡፡ በአሜሪካ 35 ሰው ገድሎአል ከፍቶ ይቀጥላል፡፡ በዚህ ጽሁፍ ያልተዳሰሱ ብዙ አደጋዎች እየተከናወኑ ይገኛሉ፡፡
  በተለይም የዘመኑ ሚዲያ ለወሬው ማድመቅ የጎሉትንና ገዢዎቹን የማያጋልጥና የማይጎዳውን ብቻ

ስለሚዘግብ እንጂ ጥፋቱ ማንንም ያልዳሰሰበት አገር የለም፡፡ ምሳሌን ብናነሳ ስለኢኮኖሚ የትኛውም ሚዲያ የሚያነሳው ስለታላላቆቹ አገራት መክሰር መውደቅ እንጂ፣ ስለ ትንንሾቹ ማለተም እንደኛ አይነቱ አገር ቦታ ተሰጥቶት አይዘገብም፡፡ ሞቱም ተነሱም በቀበሌ ልክ የሚታዩ በጌቶቻቸው ተደግፈው ያሉ ስለሆነ ማንም ቦታ አይቸራቸውም በመሆኑም ስለ ቅጣቱ መጠንና መንስኤ የአዳም ዘር እንዳይረዳው የዘመኑ የዲያቢሎስ ልጆች ማንኛውንም የመረጃ መንገድ አጥረው በመያዛቸው እንዲያውም ከነአካቴው በውኑም ይሁን በህልሙ ያላየው ጥፋት መጥቶለታል፡፡ የሚበዛው ህዝበ ዓለም / 99 ከመቶ የሚሆነው/ ከአያት ቅድመ አያቶቹ ጀምሮ የተሸከመውንና እሱም ከደረሰበት ዲያቢሎስ ካስጨበጠው ጥበብ ጋር አዳምሮ፤ በዘመን ሂደት የልዑልን ህግና ትእዛዙን ሽሮ በስፍራውም የጠላት ዲያቢሎስን መመሪያ የህይወቱ መንገድ አድርጎ በመያዙ፤ ቢመከርም ቢገሰጽም በትእግስት ቢሸከሙትም እንኳን ሊሰማ አልቻለምና፡፡ ሙልጭ ብሎ የፈጠረውን አምላክ ክዶ፤ ተረት ነው፤ ፈጣሪ የለም በሚል አቋሙ ጸንቶአል፡፡ በመሆኑም የሁሉም ፍጥረት ባለቤት ልዑልና ሃያል ጌታ ፍርዱን እንደጸሐይ አውጥቶታል፡፡

አመጸኛው፤ ከሃዲው፤ አመንዝሪው፣ቀጣፊው፣ ትዕቢተኛው፣ ዘራፊውና ጨካኝ አመጸኛ ትውልድ የሚፈጭበትና የሚጠረግበት እሳት ውስጥ ገብቶአል፡፡ የታመነበት ዲያቢሎስ፤ የተሸከመው እውቀትና ቁሳቁስ ኒዩክለር፣ ጀት፣ ታንክ፣ ሚሳየል ሲታደጉት ልናይለትም ነው፡፡

2ኛው ዙር የእሳት ወንፊት ከመጀመሪያው ጋር ሲነጻጸር ምን ይመስላል፡፡

- የሁለተኛው ዙር የእሳት ወንፊት ይመጣ ዘንድ ግድ የሆነው፤ ይህ አመጸኛ ትውልድ፤ በመጀመሪያው ወንፊት ሲበጠር፤ ሊያደምጥም ሊሰማም ስላልቻለና፤ እንዲያውም ለሕዝቡ ከመንገር ይልቅ አፍኖ በመያዝ፤ በተለይ በገዢነቱ ወንበር ላይ የተቀመጡት፤ ቁብም ስላልሰጣቸው ሁለተኛው የእሳት ወንፊት ታዞላቸዋል፡፤ ይህ ማበጠሪያ ምን ይመስላል ? ማንን ይጠርጋል ? እስከምን እርቀት ይሄዳል ? ጉልበቱስ ማን ይቋቋመዋል ? ይህንን እናያለን፡፡
- ከእንግዲህ የሚመጣው የእሳት ማበጠሪያ፤ ማንም የፍጠረት ሃይል፣ በየትኛውም ጥበብና ኃይሉ የማያቆመው ሞካሪውንም የታለመለትንም ሳያጠናቅቅና ሳይደመድም የማይመለስ ነው፡፡
- ልዑልም ልዑል፤ የፍጥረት ሁሉ ጌታና ፈጣሪ፣ ሊመለክ፣ ሊመሰገን፣ የሚገባው መሆኑን ምድሪቱም ሰማዩም ገንዘቡ ሰውም የራሱ የእጅ ስራ እንደሆነ ማረጋገጥ ስለተገባና ላመኑት ለወደዳቸው ለወደዱት በጥፋት ጎዳና ላልሄዱት፣ ትእዛዙን ለወደዱት፣ በፍቃዱም በፍቅሩም ለተደሰቱት፣ ዋጋቸውን መክፈል አለበትና ይህ ይደረጋል፡፡ የጥፋት ልጅ ሁሉ ደግሞ በጥፋቱ ውስጥ እየተጠረገ በፀፀት ያየዋል፣ ይሄዳልም፡፡ እግዚአብሄር ለልጆቹ የሚያፈሰውን ምድር ከተፈጠረች ጀምሮ ያላየችውን ፀጋውን ሲያድላቸውም፣ በግልፅም ይታያል፡፡ እርጉሞች ደግሞ በአፀደ ነፍስ በሲኦላቸው ወድቀው በአካለ ስጋ የቀሩም የጥፋት ልጆች ካሉ በስቃይ ማጥ ውስጥ ወድቀው በእሳት እየተበጠሩ እስከሚሄዱ ድረስ ይመለከቱት ዘንድ የግድ ሆኖአል፡፡
- የልዑልን፤ ሃይሉንም ለካዱ፣ የለምም ለሚሉ፣ ዲያብሎስንም ለሚያመልኩ፣ማንም አይደፍረንም ብለው በሃይላቸውና በጉልበታቸው እንዲሁም በሃብታቸው ተመክተው ለሚገለሉ ሁሉ፣ የፈጣሪንም ትእግስት እንደቂልነት እንደከንቱነት በመቁጠር ለተከፈሉ፣ ጥበብ ልብሳችን፣ ዲያቢሎስ ጋሻችን ብለው ለተቀመጡት ለአንዴም ለሁሌም መዝገባቸው ተዘግቶ ከአባታቸው ጋር ወደ እሳት መውረድ አለባቸው ይህም ይሆን ዘንድ በልዑል ታዞአል፡፡ ማንም ሳያግደው ተፈጻሚ ይሆናል፡፡
- ታሪካቸውም፣ ዝክራቸውም ፣ ቅሬታአቸውም፣ ዘራቸውም፣ከምድረ ገጽ ይጠረግ ዘንድ ታዞአል፡፡

ስለሆነም ይህ የሁለተኛው ይእሳት ወንፊት፤ በመጀመሪያው የእሳት ወንፊት ያለተዳረሰውን ሽፍኖ በተለይም የአመጽ መሪዎችንና የእነሱ ተዋረድ ናዛዥ አዛዥ ታዛዦችን ኢላማው አድርጎ የሚመጣ ያህል፡፡ ሕዝባቸው እንዳይሰማ እንደይጸጸት እንቅፋት የሆኑ ገዥዎችም ፣ የሚዲያ ሰዎችም፣ በተለይ በዚህ ጉዳይ ውሳኔ ሰጭዎች የሆኑ ሁሉ፣ ሙለውን መልእክቶች ለህዝብ እንዳይደርሱ፤ አቅማቸው የፈቀደውን ሁሉ መሰናከል በማድረጋቸው የማይወጡት ፍጹም ያልገመቱት ፤ ሞትን እንዲለምኑት እያደረገ የሚፈጫቸው እሳት ታዞላቸዋል፡፡ ከህዝቡም መሃል እየለዩ የሚበሏቸው ዓለም ያላያቸው በምንም መሳሪያ የማይቋቋሙት የአውሬ አይነቶች ይፈሱባቸዋል፡፡ በአሰቃቂ ሁኔታም ምልክት አልባ የሆነውን የአዳም ዘር በሙሉ ይቆረጥሙታል፡፡

- ርእደ መሬት ዛሬ ከምናየው በለይ ከሰባት እጥፍ ጀምሮ እስከ 49 እጥፍ ድረስ ጨምሮ ይመጣል፡፡ ከተከሰተበት ስፍራ አገርም ከሆነ አንድ አገር አይኖርም፡፡ አካባቢም ከሆነ በላዩ ላይ የሰውም ሆነ የሌላ ምልክት አይኖርም፡፡ በአንድ ጊዜ በሚሊዮኖች የሚቆጠሩ ሕዝቦች መሰናበት የተለመደ ክስተት ይሆናል፡፡
- የኒዩክሊየር ፍጹም ጥፋት፡- በጨበጡት አገሮች ሁሉ ላይ ይሆናል፡፡ በጃፓን ከተከሰተው አደጋ ከሚመጣው ጋር ሲነጻጸር አደጋና ጥፋት እንዳልሆነ ይታመናል፡፡
- ማእበሎች ሁሉ ስም የወጣችሁላቸውም ሆኑ፤ እስከ አሁን ካያችኋቸው በለይ ከሰባት እጥፍ ጨምሮ እስከ 49 እጥፍ ጎልብተው ይመጣሉ፡፡ ማንም በእርዳ ተረዳዳ አያመልጣቸውም፡፡
- አውሎ ነፋሶች ሰው አይቶም በማያወቀው ፍጥነትና ጉልበት ይመጣሉ፡፡ ጠርገውም ያለምልክት ያጠፋሉ፡፡ ጉልበታቸውም በ49 እጥፍ ያድጋል፡፡
- በረዶዎች እሰከ ዛሬ ከምናውቃቸው የአንድ ግራም ክብደታቸው በለይ እሰከ 50 ኪሎ በሚሆን ክብደት በተለያየ ቅረጽ ፍጹም ያጠፉ ዘንድ ፤ በተመረጡ ቦታዎችና ሰዎች ላይ ይወድቃሉ፡፡ ቤትንም መሸሸጊያንም ያወድማሉ፡፡
- ማህበራዊ ፣ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊ ቀውሶች ሁሉ አሁን ከምናየው ሰፍተው ፤ ሁሉንም የምድር አካል ሸፍነው ከሰባት እጥፍ ተነስተው 49 እጥፍ በሆነ የጥፋት ኃይል ምድርን ይከድናል፡፡ ገዥና ባለ ሃብት ነኝ፣ የሚልና የነዚህ ጋሻ ጃግሬ ሁሉ፣ ከምድር ገጽ የሚያጠፋቸው በርባሪና ጠራጊ እሳት ታዞላቸዋል፡፡
- በሽታዎች እጅግ አደገኛ በሆኑ ቫይረሶች እየፈሉ ይመጣሉ፡፡ በሚሊዮኖች የሚቆጠሩትን የአዳም ዘር ምልክት አልባ የሆኑትን ሁሉ ያጠፋሉ፡፤ ለረሃብተኞች ደራሽ ስለማይኖር ሚሊዮኖችን መውሰድ ስራቸው ይሆናል፡፡ ምልክት አልባው ሁሉ የጥፋቶቹ ሁሉ ኢላማ ይሆናል፡፡
- ዓለም ለዘመናት ያደራጀችው መመኪያ ሁሉ ከንቱ ሆኖ ከነ ምልክቱ ይጠፋል፡፡ ባጠቃላይ በሙሉው መልእክት ( ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን ) በሚለው የአፈጻጸም መልእክት 3 ገጽ 83 -87 የመጨረሻ ማሰሪ ቃልና ትእዛዞች የሚገልጽ ሲሆን ፤ እነዚህ የመጨረሻ ትእዛዞች ዓለም በመጀመሪያው የእሳት ወንፊት ሲበጠሩ እንድናይ አድርጎናል፡፡ ዛሬም በዚህ ሁለተኛው የእሳት ወንፊት በትእዛዞቹ ውስጥ የተጠቀሱትን ቅጣቶች ሁሉ፤ በሰባት ጊዜ ሰባት እጥፍ አብዝቶ ይጠርግ ዘንድ በልዑል ፈቃድ በኔም በባሪያው በኩል እነሆ ታዞአል፡፡
- ምልክት አልባው፤ ተወህዶ እምነትህን ንቀህ፤ ከንቱን የተከተልህ በጥበብህ በጉልበትህ በሃብትህ የታመንክ የልዑል ጠላት፤ የእናቴ የድንግል ጠላት፣ የተወዳጆቼ የተከበሩት ቅዱሳን መላእክት ጠላት፤ የተዋህዶ እምነት ጠላት የት ትደበቃለህ ?

ወዴትስ ትሸሸጋለህ ? እንግዲህ ዛሬም መርዶህን ስማ አብቅተሃል፡፡ መጭውን ጥፋትህን በምን ጊዜ በምንም መንገድ አታልፈውም፡፡ መልካም ሰንበት !!

- እንዲሁም የየክፍለ አህጉሮችን የሁለተኛው ዙር የእሳት ወንፊት እጣ ፈንታውን በየራሳቸው ገጽ ማብራሪያ ይሰጥበታል፡፡ ይህች ከእግዚአብሄር ዘንድ የበደለኛ እድል ፈንታ፤ ግፈኛም ሁሉን ከሚችል አምልክ ዘንድ የሚቀበላት ርስት ናት፤ ልጆቹ ቢበዙ ለሰይፍ ይሆናሉ፤ ዘሩም እንጀራን አይጠግብም፤ ለእርሱም የቀሩት በቸነፈር ይቀበራሉ፤ መበለቶቻቸውም አያለቅሱም፤ እርሱ ብርን እንደ አፈር ቢከምር ፤ ልብስንም እንደ ጭቃ ቢያዘጋጅ፤ እርሱ ያዘጋጀው ይሆናል፡፡ ነገር ግን ጻድቅ ይለብሰዋል፡፡ ብሩንም ንጹሃን ይከፋፈሉታል፡፡ የሚሰራው ቤት እንደ ሸረሪት ድር ይሰራል፡፡ ጠባቂም እንደሚሰራው ጎጆ ነው፡፡ ባለጠጋ ሆኖ ይተኛል፤ ዐይኑን ይከፍታል እርሱ የለም፤ ድንጋጤ እንደ ጎርፍ ታገኘዋለች፤ በሌሊትም አውሎ ንፋስ ትነጥቀዋለች፤ የምስራቅ ነፋስ ያነሳዋል፤ እርሱም ይሄዳል ፤ ከቦታውም ይጠርገዋል፤ እርሱ ይጥልበታል አይራራለትም፤ ከእጁም ፈጥኖ መሸሽ ይወዳል፤ ሰው በእጁ ያጨበጭብበታል፤ ከስፍራውም በፉጨት የስወጡታል፡፡ መጽ. ኢዮብ 27፡ 13 – 23

በመጀመሪያው የእሳት ወንፊት እያበጠረህ አሁንም ስላልተመለስክ ከላይ በቃሉ እንደምትረዳው ሁለተኛው እሳት ወንፊት ታዞልሃል፡፡

# 8 / አገራችን ኢትዮጵያ በመጀመሪያው የእሳት ወንፊትና በመጭው ሁለተኛው የእሳት ወንፊት ውስጥ

ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን !! የኢትዮጵያ ህዝብ የወደደህን አምላክ በመናቀህ ከአባቶችህ ብርቱ ዋጋ ተከፍሎበት የተሰጠህን እንቁ እምነት ጥለህ የባእዳን እምነትና ውዳቂ እምነት ተሸክመህ ላልተቋረጠ ጉዳት ተዳረግህ፡፡ ይህ ብቻ ሳይሆን ዛሬ ምታየውን መጠነ ሰፊ ጉዳት እያየኸው ትገኛለህ፡፡የልዑልን ሁሉንም ህጎች ጣስክ፤ በባእዳን ባህል እምነት አኗኗር ተጠመድክ፡፡ አባቶችህ የገነቧትን ተዋህዶ እምነትህን ጣልክ፤ በምትኩ የዲያብሎስን እምነቱንና ስርአቱን አነገስህ፡፡ ጥንቆላን ፤ አምልኮ ባእድን አነገስህ፡፡ የመናፍቃንና ወላጆቻቸው ፤ እንዲሁም የተረት አምለኪዎች መዘባበቻ ሆንክ፤ እምነቱን ተዋህዶን፣ ዜግነቱን ኢትዮያዊነትን ካፈረባት ዜጋ ምንም ይመጣብናል ብለው ስላልሰጉ ገዥዎችህም ጭምር አላገጡብህ፤ ፈነጩብህ፣ የወደቅህበትን እስቲ እየው፡፡

ስለዚህ እስከ ዛሬ እያየኸው ያለው ጥፋት እንደ ካንሰር ጠፍሮ ይዞሃል፡፡ ይህች ምድር የድንግል ምድር ናት፡፡ አመጸኛን የሚሸከም አንቀልባ የላትም፡፡ ከተዋህዶ እምነት ውጭ ለሆነ ሁሉ ምድሪቱ አትሸከምም፡፡ ሁሉንም በረከቷን ትነፍግሃለች፡፡ ዛሬም እንደምናየው ለከፉ ችግር፣ ለረሃብ፣ ለበሽታ፣ ለድህነት፣ ለጨካኝ አገዛዝ ተጥለሃል፡፡

የመጀመሪያው የእሳት ወንፊት ሁለመናህን አበጥሮሃል ፡፡ እንደ ውጪው አገር ያልተጠረገኸው በኢትዮጵያ ምድር እውነተኛ የልዑል ህዝቦች ፣ የድንግል ወገኖች፣ የከበሩ የቅዱሳን መላእክት ወዳጆች፤ በጥቅሉ የአንዲቱ የእውነተኛይቱ ተዋህዶ ልጆች እንደ ቁሻሻ በየስርቻው ወድቀው በጨካኝ አረመኔ ገዥዎች ተሳደውና ተረግጠው በልመናቸው ቁጣውን ስለተከላከሉልህ እንጂ እስከ አሁን የሳብካትን አየር አትተነፍሳትም ነበር፡፡ ይሁንና በነሱ ልመና ብቃት እያላገጥህ አገሪቱንም ተወህዶ ቤተ ክርስቲያንንም እያጠፋህ መቀጠል ስለማይቻል የተሰጠውን እድልህን ስላላመንከው ወደ ሁለተኛው የእሳት ወንፊት እንድትሸጋገር ታዞብሃል፡፡ ተወስኖብሃል፡፡

በሁለተኛው የእሳት ወንፊት አገራችን ኢትዮጵያ ምን ይገጥማታል ለሚለው መልሱ ቅርብ ነው፡፡ በየመልክቶቹ ሁሉ ስለ ኢትዮጵያ እጣ ፈንታ በሚገባ ተገልጾአል፤ ያንን ደጋግመህ ማየት ይገባል፡፡ በመጀመሪያ ነጻ የምትወጣ አገር ኢትዮጵያ መሆንዋን ተረጋግጦ ተገልጾአል፡፡ አሁን በሁለተኛው እሳት ማንም አለቃና ምንዝር፣ ዘራፊና አዘራፊ፣ ዘረኛ፣ መናፍቅ፣ ተረት አምላኪ፣ ባእድ አምልኮ ተከታይ፣ ኢትዮጵያዊነትን ንቆ ዛሬ ደግሞ ለዘረፋ በአገሪቱ የተሰማራ፣ አገሪቱን፣ ሕዝቧንም፣ እምነቷንም፣ ታሪኳንም የማያውቁትን አውቀውም የካዱትን ፣በሕዝብ ላይ ሆኖ የሚገዛ፣ የድሃውን ጎጆ በአለማለሁ ስም የሚያፈርስ፣ ሰርቶ የደከሙትን በተለያየ የቀረጥና የህግ ሽፋን የሚዘርፍ በጥቅሉ በአገሪቱ ያለ ጠማማ፣ ወልጋዳ፤ እንቅፋት በሙሉ፣ ገዥና አለቃም ሆነ ምንዝር የሚጠርግ ይሆናል፡፡

ሁለተኛው የእሳት ወንፊት፣ ምድርም ሆነች በላይዋ የሚኖረው ሰው፤ የሚቋቋመው አይደለም፡፡ በእዚህ በሁለተኛው የእሳት ወንፊት የሚያልፍ በልዑል የታመኑ በግንባራቸው ምልክት ያላቸው ብቻ ናቸው፡፡ የተቀሩት ከመርከቢቱ ውጪ በተጨማሪም ምልክት አልባ የሆኑ እንደ ኖህ ዘመንና እንደ ሰዶምና ገሞራ መጠረግ ብቻ ነው፡፡ የተተወላቸው እጣ ፈንታም ይኸው ነው፡፡ በዘመናት እድሜአቸው የደከሙት፣ ኢትዮጵያንና እምነቷን ተዋህዶ ኦርቶዶክስን ለማጥፋት ነበርና፤ በአለም ሁሉ ፈሰው ካሉት የዲያብሎስ ልጆች ወንድሞቻቸው ጋር የዚህ ፍርድ አፈጻጸም ያርፍባቸው ዘንድ ግድ ይሆናል፡፡ ከልዑልም ትእዛዙ ወጥቶአል፡፡

1 ሀ / የተዋህዶ ቤተ ክርስቲያናችን ያለችበት ሁኔታና በሁለተኛው የእሳት ወንፊት እጣዋ

ኢትዮጵያ ሃገራችን በልዑል ምርጫ የታደለች፣ የተባረከች ለድንግልና ለቅዱሳን መላእክት በበረከት የተሰጠች የሰው ልጅ ጠላት በሆነው ዲያብሎስ ደግሞ ቁጥር አንድ ጠላቱና የረገማት፤ ሊያጠፋት ሌትም ቀንም  የሚደክምባት ናት፡፡ በመሆኑም ይህችው አንዷ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያናችን በጨለማው ገዥና በብርሃን ገዥ የሁሉም ጌታ በሆነው ፈጣሪያችን መሃከል ታላቅ ውጊያ የሚደረግባት የጦር አውድማ ናት፡፡ የሰው አእምሮ ታላቁ የውጊያ መድረክ ነው፡፡ የሰው ልጅ እንደምርጫው ራሱንም እንደአመነበት ላስገዘው ነገር እራሱን መስዋእት አድርጎ ያቀርባል፡፡ ልዑል እንዳስቀመጠለት ወይ ለክፉ ወይም ደግሞ ለደግ ( ለጨለማ ወይም ለብርሃን ) ራሱን ይሰጣል፡፡ በዚሁ መሰረት በአለም ሁሉ እንደሚታየው ለጨለማው የተገዙ በዛሬው ሰዓት ለታላቁ የቁጣ እሳት ፍሪዳ ሆነው የቀረቡ፤ ለዘመናት ከአያት ቅድመ አያቶቻቸው ጀምረው እውነትን ተጻረው ፤ የሥጋ ሃሳብን ፍላጎታቸውን በማራመድ፤ የዲያብሎስ መሳሪያ ሆነው፤ እስከ አሁን በአባታቸው በዲያብሎስ መሪነት፤ ለጥፋትና ለመጠፋታቸው እየደከሙ ይገኛሉ፡፡

ከነሱ በተጻራሪ ለብርሃን ለእውነት ለፈጠሪያቸው ፈቃድና ትእዛዝ ራሳቸውን ሰጥተው በሰራዊት ጌታ ግንባር ቀደምትነት እስከ ዛሬ ያልተቋረጠ ውጊየ እያካሄዱ ይገኛሉ፡፡ የተዋህዶ ቤተ ክርስቲያናችን ከመሰረቱ እግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ የተከለውን እውነት ጨብጣ በአባቶቿ ደም አጽንታ በብርቱ የጠላት ውጊያ እዚህ ደርሳለች፡፡ የኢትዮጵያ ተወህዶ ቤተ ክርስቲያን የዲያብሎስ ቁጥር አንድ ጠላት በመሆኗ ከውስጧም ከውጪም አፍራሽ ኃይል ተሰማርቶባት በታላቅ ውጊያ ውስጥ ትገኛለች፡፡

ዘመኑ እስከ አሁን የዲያብሎስ ለሱም የተፈቀደ ስለነበር ጠለት የበላይነቱን ጨብጦ በቤተክርስቲያናችን በአንዲቷ የተዋህዶ ቤታችን፣ ከአናቷ እስከ እግር ጥፍርዋ ወሮአት ይገኛል፡፡ እናቷ በዲያብሎስ የጠመንጃ ኃይል፣ በድርጅታዊ አሰራር፣ በካቶሊኮች ብርቱ ድጋፍ፣ በመናፈቃን ጋሻ ጃግሬነት፣ በገዥው ቀጥተኛ ጣልቃ ገብነት የተቀመጠ ፍጹም የተዋህዶ ጠላት፤ የአለም አቀፍ የመናፍቃንና የካቶሊኮች አባልና መሪ፣ የሆነ ቤተ ክርስቲያኗን ለመናድ ሲባል በአናቷ ላይ ከተቀመጠባት ሁለት አስርትን አስቆጥሯል፡፡ ዲያብሎስ የብሉይንም፣ የሃዲስንም ዘመን የምድር ገዥ ሆኖ እስከተፈቀደለት እስከዛሬ በሁሉም አዛዥ ናዛዥ ሆኖ አየፈጫት አየቆላት ይገኛል፡፡ ይህ ዘመኑ መልእክት ሁለት ከወጣ ( ማለትም ከ2000 ዓ.ም ) ጀምሮ ወደተዘጋጀለት ወደ ሲኦሉ ( ወደ እሳቱ ) እንዲወርድ በመወሰኑ ጉዞውን ጀምሮአል፡፡

ገና እንደበፊቱ እንፈልጣለን እንቆርጣለን የሚሉ የነጋባቸው የኢ/ ተወህዶ ቤ/ክ ውስጧንም ሆነ ውጪዋንም ወረው በረከቷን በመጋጥ ፣ ምእመኖቿን በመበተን፣ ቀይዶና አስሮ ለመናፍቃን መሰሎቻቸው ተኩላዎች በመስጠት የገዥው ሰራተኛና አገልጋይ የሆኑ እምነቱም የሌላቸው አገሪቱን በመዝረፍ ስራ ላይ የተሰማሩትን በቤተ ክርስቲያኗ አካል ውስጥ በመሰግሰግ ሽባ እንድትሆን አድርገዋታል፡፡ የዚህ ጥፋት ዋነኛ ሞተሮች ደግሞ ከፓትርያርኩ ጀምሮ ለሱ የታመኑትን ጳጳሳት አካቶ በየደረጃው ያሉ የየአድባራቱን አስተዳዳሪዎችንም ሆነ አገልጋዮችን ፍጹም የተዋህዶ ጠላት የሆኑትን ሁሉ የሚያቅፍ ሆኖአል፡፡ በአብነት ት/ቤቶች፤ ቁልፍ ቁልፍ ቦታ ላይ ሰላይ የስርአቱ አገልጋዮችን ሰግስጎአል፡፡ በስብከተ ወንጌሉ ከአናቱ እሰከ ስሩ ድረስ ስውር መናፈቃንን አሰማርቷል፡፡ ተሃድሶ፣ ቅባት፣ የሆኑ ጳጳሳት፣ ካህናት፣ ዲያቆናት በሁሉም ስፍራ የበላይነቱን ይዘው በማጥፋት ላይ ይገኛሉ፡፡

እውነተኞች የተዋህዶ ልጆች እንኳን በየቤተ ክርስቲያኑና አድባራቱ ሊኖሩ እስከ ሸሹበት እሩቅ ገዳማት ጭምር በመዝመት ማገኛውንም የተዋህዶነት ምልክት የጨበጡትን ለማጠፋት እየሰሩ ይገኛሉ፡፡

ማህበረ ቅዱሳንን በተመለከተ ቀደም በመልእክት 4 ( ብዛቱ 15 ገጽ በሆነ )እንደተብራራው ማህበረ ቅዱሳን በውስጡ ቅኖችና ለተወህዶ እምነታቸው የቀኑ እንዳሉ ሁሉ ፤ ጠላት ያሰረጋቸው እምነት ለበስ የሆኑ ፍጹም የገዥውና የቤተ ክርስትያኗ አፍራሽ ኃይል ሊያፈርሱት እያደቡ ይገኛሉ፡፡ በውስጡም ራሳቸውን የቀበሩም ሰአት ጠባቂዎችም ናቸው፡፡

በዚህ ብቻ አልተገቱም ገገርውም ሆነ የተዋህዶ እምነት ጠላቶች አንድ ያደረጋቸውና ያሰማራቸው መሰረታቸው ነው፡፡ የአለሙ ገገር ዲያብሎስ ሁሉም የአለም መሪዎች በዋንኛነት የኛም፣ በአለም ሁሉ ያሉ እምነቶች ማለትም ከተዋህዶ እምነት ውጪ የሆኑ ሁሉ ገንዘቡ ናቸው፡፡  ስምሪቱም የሚከናወነው ከአለም አቀፍ ካቶሊክ፣ ከአለም አቀፍ መናፍቃን፣ እንዲሁም ከተረት አምላኪዎች ጭምር ተቀናብሮ፣ በሚያዝዛቸው ገገሮቹ የሃይል ስምሪት ተደግፎ ነው፡፡  መልእክቶቹም ሁሉንም የአለም አካል የዳሰሱት ጠላት ዲያብሎስም በሁሉም የአለም አካል ስለተንሰራፉ ነው፡፡

የአዳም ዘር በተለይም ኢትዮጵያውያን ልብ ልትሉ የሚገባው ትልቁ ነገር ይህ ነው፡፡ የአለም ጸሐፍት ሁሉ ይጽፋሉ፣ ስለስጋው አለም ነው፡፡ ይህ የዲያቢሎስ ችግር አይደለም፡፡ እንዲሁም ስለእምነት ብዙዎች የእምነትም የጥበብም ሰዎች ይጽፋሉ፡፡ በራሱ የእምነት ክልል ውስጥ እስካሉ ድረስ ለዲያቢሎስ አይገደውም፡፡የሱ ጭንቀት ስለተዋህዶ እምነት የሚጽፉ በተለይም በእምነቱ የፀኑ ከሆኑ ብቻ ነው፡፡ ስለ ዲሞክራሲ ተጻፈ፣ ስለኢኮኖሚ ተጻፈ፣ ስለአገር ድንበር ተጻፈ፣ስለፖለቲካው ተፃፈ፣ይህ ሁሉ ለዲያቢሎስ ችግሩ አይደለም፡፡ የሱ ችግር ተዋህዶ እምነትን የሚያጸና ተግባሩም ፅሁፉም እንዲሁም ፅናቱም ሲሰምሩ ካየ ነው፡፡

የእምነቱን መሰረት ጠንቅቀው ያወቁትን አገራችን ኢትዮጵያና እምነቷ ተዋህዶ አምጠው የወለዱአቸውን ብዙ መምህራን፣ ብዙ ዲያቆናት፣ ብዙ መነኮሳት፣ ብዙ ባሕታውያን ፣ ብዙ ጳጳሳት በስውርና በቀጥታ በተለያየ የአደጋ ቅንብር በራሱ ቤተ

ክህነት ውስጥ በተደራጀ ቡድንና በገዢውም የፀጥታ ሃይል እንዲወገዱ ተደርጓል፡፡ ይህ ድርጊታቸውን ደግሞ እኛ የእግዚአብሄር ሕዝቦች ጠንቅቀን እናውቃለን፡፡ በሌላው ርእስ የተወሰነባቸውን እናያለን፡፡

የሁለተኛው የእሳት ወንፊት በኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ውስጥ ምን ይፈጸማል የሚለው ዋናው ጥያቄ ነው፡፡ ለዚህ ዛሬ የልኡልን ቤት እያጠፉ ያሉ በውስጧም በውጭም ሆነው ለተዋህዶ እምነት መጥፋት እየሰሩ ላሉ ሁሉ ከዚህ የሚከተለው ቅጣትና መጠረግ ታዞላቸዋል፡፡ ይህ ትእዛዝ የኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ፀድታ በልዑል እግዚአብሄር መንፈስ የተቀቡት እውነተኛ እረኞቿ እስከሚረከቧት ድረስ የፀና ይሆናል፡፡ ስለዚህ የሰራዊት ጌታ እግዚአብሄር እንዲህ ይላል፤- በጠላቶቼ ላይ ቁጣየን እፈጽማለሁ፤ የሚቋቋሙኝንም እበቀላለሁ፣ እጄንም ባንቺ ላይ አመጣለሁ ዝገትሽንም በጣም አነጻለሁ፣ ቆርቆሮሽንም ሁሉ አወጣለሁ፣ ፈራጆችሽንም እንደ ቀድሞው፣ አማካሪዎችሽንም እንደ መጀመሪያው ጊዜ መልሼ አስነሳለሁ፣ ከዚያም በኋላ የጽድቅ ከተማ የታመነችም ከተማ ተብለሽ ትጠሪያለሽ፤ጽዮን በፍርድ ከሷም የሚመለሱ በጽድቅ ይድናሉ፣ በደለኞችና ሃጢአተኞች ግን በአንድነት ይሰበራሉ፤ እግዚአብሄርንም የሚተው ይጠፋሉ፤ በወደዳችኋት የአድባር ዛፍ ታፍራላችሁና ስለመረጣችኋትም አትክልት ይዛችኋልና፤ ቅጠሏ እንደረገፈ ዛፍ፤ ውሃም እንደሌለባት አትክልት፤ ትሆናላችሁና፤ የኋለኛውም እንደተልባ ጭረት ስራውም እንደጥላሸት ይሆናል፤ አብረውም ይቃጠላሉ፤ እነርሱንም የሚያጠፋ የለም፡፡ ኢሳኢያስ 1 ፤ 24 – 31 ቃሉን የሚነግረን ትእዛዞቹ ተፈጻሚ ይሆናሉ የሚተርፉ ለመልካም፤ የሚጠረጉ ለሲኦል ይሆናሉ

## ትእዛዞች፤

ሀ/ በኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤ/ክ አመራሩ ላይ ላሉት፣ የመናፍቅና የካቶሊክ ጉዳይ ፈጻሚ ለሆኑት፡፡ ተዋህዶ እምነትን ለማጥፋት መድከም ታላቅና ይቅር የማይባል ወንጀል ነው፡፡ ያውም የበግ ለምድ ለብሶ በቤተክርስቲያና እናት ላይ ፊጥ ብሎ፤ በጎችን መበተን፤ ማጥፋት፤ ማረድ፤ መግደል፣ የሚያስከትለው ምን እንደሆነ ሕዝቅኤል 34 ይነግረናል ስለዚህ ሞትን ለናንተ መስጠት ሽልማት ነው፡፡ ስለሆነም ሞትን የምትለምኑበት በሁለመናችሁ ላይ የሚሰለጥን በርባሪ እሳት ታዞአል፡፡ ለጥፋት የምትገለገሉበት እጅ፣ አይን፤ ጆሮ፣ እግር፣ አእምሮአችሁ የማታዙት፣ የማይታዘዝላችሁ ይሆናል፡፡ እንቅልፍ የሚባል እንዳታገኙአት ታዞአል፡፡ ሞት ያባርራችኋል ስትገኙለት ይሸሻችኋል፡፡ ሌትም ቀንም የአካልም የኅሊና እረፍት ታጣላችሁ፡፡ ልትቀምሱ፣ ልትጠጡ፣ የወደዳችሁት ሁሉ መርዝ ሆኖ ያሰቃያችኋል፡፡ ስቃያችሁ ጋብ የሚለው ለጥቂት ደቂቃዎችም ቢሆን እንቅልፍ የሚያሸልበው፤ በኔ በልኡል ባሪያ የተላለፉትን መልእክቶች፤ ከአንድ ጀምሮ እስከ አሁኑ ሰአት የወጡትን መልእክቶች በሙሉ፤ በይፋና በአደባባይ፤ በማስሚዲያ ስታነቧት፤ ሕዝብም ሰምቶ ሲጠግባት ብቻ ነው ፤ በመኝታ ላይ ማረፍ የሚቻለው፡፡ ብዙ መሰሎቻችሁ በሚያዩበት ስፍራ በኔ በልዑል ባሪያ የተላለፈውን ሙሉ መልእክት ( ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን ቁጥር 1 ፤ 2፤ 3 ፤) የያዘውን ጥራዝ፤ ደረታችሁ ላይ በግልጽ በማስቀመጥ ነው፡፡

ከላይ በተዘረዘረው መልኩ የምታገኙዋት እንቅልፍ ከአንድ ሰዓት በፍጹም አትበልጥም፡፡ ይህም እድል የሚሰጠው በልባችሁም በአደባባይ ተናግራችሁ የሰራችሁትን ስትናገሩ ብቻ ነው፡፡ እንዲሁም ያሰራችኋቸውን የእግዚአብሄር ሕዝቦች ከነካሳቸው ስትለቁ፤ በየገዳሙ፣ በየቤተክርስትያኑ፣ በየገዳማቱ የወተፋችኋቸውን አጥፊዎች ስታነሱ ብቻ ነው፡፡ የአንድ ሰዓቷም እንቅልፍ በቀን አንዴ የምትሰጣችሁ እንጂ ከዛ ውጪ ያለም፡፡ ከውስጣችሁ ለታደሉት ሞት አሰቃይቶ ይወስዳል፡፡ ይህ እድል ለዲያቢሎስና ከእምነታችን ቤት እናት ላይ ለተቀመጠው ፓትሪያርክ፤ ከሲኖዶሱ ጀምሮ እስከስር አጥቢያ ቤተክርስቲያንና ገዳማት ድረስ በመሰግሰግ ለዚህ ሰው ቅስትና ማገር ሆናችሁ፤ ከእግዚአብሄር ይልቅ ለአንድ ሰውና መሰሎቹ ተኩላዎች ታምናችሁ ላለችሁ ሁሉ፤ ለሱ የታዘዘው ታይቶም ተሰምቶም የማይታወቅ ስቃይ ለናንተም ታዞአል፡፡

ከዚሁ በተረፈ ከላይ እንደታዘዘው የልዑል ልጆች ቦታውን ሲረከቡት ከስቃያችሁ የሚገላግላችሁ ክፉም ይሁን ደግ ውሳኔ በሰዓቱ ታውቁታላችሁ፡፡እዚሁ የምትደርሱት ግን እጅግ ጥቂቶች ናችሁ፡፡ በዚሁ ቅጣት ከነትእቢታችሁ ለመቀጠል ከዳከራችሁ ቅጣቱ በ49 እጥፍ እንዲያድግ ተወስኖአል፡፡

ለ/ ከስር ለተኮለኮላችሁ በአስተዳደሩም በአገልግሎቱም ላይ ላላችሁ የተዋህዶ እምነትን ታፔላ ለለጠፋችሁ፡፡ ከላይ ላመራሮቻችሁ እንደታዘዘው በእናንተ ላይ ተፈፃሚ ይሆናል፡፡ ከእግዚአብሄር ይልቅ በነሱ ታምናችኋልና፤ የነሱ መዝገብ ሲዘጋ የናንተም አብሮ ይከደናል፡፡ ይህ ሁሉ እየሆነ፤ ከነድንጊያ ልባችሁ ከጸናችሁ፤ ይኸው ቅጣት በ7 እጥፍ ያድጋል፡፡ በዚህ ካልተረዳችሁ 7 ጊዜ 7 እጥፍ 49 ጊዜ እጥፍ ሆኖ ጨምሮ ያጠናቅቃችኋል፡፡

ሐ/ ዲያቢሎስ ሁሉንም የአለም አካሎቹን አስተሳስሮ ስለመግዛቱና የየተዋረድ ትእዛዝና ቅንብሮቹ በአለም ሁሉ ያሉ ገዢዎች በዲያቢሎስ መለኪያ ስልጣን ላይ ይወጣሉ፡፡ ካልታዘዙት ይወርዳሉ፡፡ ከታዘዙት ደግሞ ይቆያሉ፡፡ የሱ አሰራር የሚሰበረው ከላይ የልዑል ትእዛዝ ሲያርፍበት ብቻ ነው፡፡ እግዚአብሄርን እንደ እግዚአብርነቱ የሚያከብሩ ሕዝቦች ወይም ግለሰብ ላይ፤ የዲያቢሎስ ህግ አይሰራም፡፡ ነገር ግን ከእግዚአብሄ ህግ ሲወጡ እስራኤላውያን ይገጥማቸው እንደነበረው ውጣ ውረድ

ዛሬም ላሉ ሁሉ ይሰራል፡፡ ( ዛሬም እንደ ህዝብ ለልዑል የሚገዛ ባናይም፤ እንደ ግለሰብ ግን ስላሉ ዲያቢሎስ ይፈትናቸዋል እንጂ ሊያዛቸው ሊገዛቸው አይችልም) የተቀረው ግን ፈጣሪውን በራሱ ምርጫና ውሳኔ የካደና በመምሰል የቆመ፤ በመሆኑ ለዲያቢሎስ አገዛዝ የተተወ ነው፡፡ ማንኛውም ሰው በምርጫው የዚህን አለም ደስታና ፈንጠዝያ ከመረጠ የአምላኩን የፍቅር፣ የጽድቅ ትእዛዝ ከናቀ፣ ከካደ፣ ዲያቢሎስ የዚች ምድር ጊዜያዊ አዛዥና ፈታኝም ነውና ይረከበዋል፡፡ ለዚህም ነው የሚበዛው የሰው ዘር በጉያው የተወሸቀው፡፡ አለምን ንቀው፤ ዲያቢሎስን ክደው በልባቸው፣ በነፍሳቸው፣ በስጋቸውም የሰራዊት ጌታን ያነገሱ፤ ምንም ፈተናቸው ቢበዛ በረከታቸውና ተስፋቸው የጸና ነው፡፡ ከውጣ ውረዱ ጋር ዘወትር በአምላካቸው ይጠበቃሉና ከዚህ ውጭ ያለው የሰው ዘር ግን በጨለማ ኃይል ተተብትቦ፤ ለዲያቢሎስ ፍርፋሪ፣ ለግበፅ ሽንኩርት ተገዝቶ ይኖራል፡፡ ዲያቢሎስ የተገዙለትን በስልጣን፣ በሃብት እንዲጠልቁ ያደረጋቸዋል፡፡ ከዚያ የሚያንሱትንም በእለት ተእለት ሕይወታቸውና በትርፍ ፍሊጋቸው በመግባት የራሱ ተገዢ ያደርገቸዋል፡፡ ዛሬ የምናየው እውነት በዚህ መስፈሪያ የመጣ ነው፡፡ የሃይማኖቱም መሪዎች አድርጉ የተባሉትን ያደርጋሉ፡፡ የእምነቱ ህግ ፈቀደም አልፈቀደም፤ ምሳሌ እንይ፤ የአገራችን የተዋህዶ እምነታችን መሪ ( በባለ ጠብመንጃው ድጋፍ ተቀመጠ፤ ወይም በዲያቢሎስ የተመደበ) ከተዋህዶ እምነታችን ጋር ምንም የማያገናኛቸውን በመሰረታዊ የእምነታችን መመሪያ የተወገዙትን ተቀብሎ የአለም አቀፍ ቤተ ክርስቲያን ህብረት በሚል ስብስብ ውስጥ በመታቀፍ፤ የክብር ፕሬዘዳንት የሚል ሹመት መጠሪያ ሆኖ ዘወትር እንሰማለን፡፡ ይህ ህብረት የአለም አቀፍ መናፍቃንን፣ ካቶሊኮችን፣ በዋናነት የያዘ ነው፡፡

እንዲሁም በአገራችን መናፍቁንም ካቶሊኩንም እስላሙንም በመሰብሰብ ለሰላም የሚል የእምነት ጥርቅም ፈጥረው የዚሁ ሰብሳቢ ሁነዋል፡፡ ሰላም በተዋህዶነት በመጽናት እንጂ በእምነት ካባ የገዢው የፖለቲካ ድራማ ሰራተኛ በመሆን የሚመጣ አልነበረም፡፡ ለዚህም ነው በቤተ ክርስቲያናችን በተዋህዶ እምነታችን ቤት አናት ላይ ዲያቢሎስ ተቀምጦአል የምንለው፡፡ ዲያቢሎስ ያዛል፤ ጳጳስ ሆነ ፕሬዘዳንት ይታዘዛል፡፡ ፈቅደው የተገዙለት አባታቸው ነውና፡፡

*መ/ በቤተ ክርስቲያናችን በተዋህዶ እምነታችን ላይ ለሰራችሁት ወሰን የለሽ ወንጀል፤ ከላይ በ፣ ሀ/ሀ እና በ፣ ሀ/ ለ ለተጠቀሳችሁት፣ በእምነታችን ላይ ለሰራችሁት ቅጣት፤ በትእዛዞቹ እንዳለ ሆኖ በስጋው በገዢው መንግስት ውስጥ እንደ ተሳትፎአችሁ መጠን ለገዢው ስርአት የሚታዘዘው ቅጣት ማለትም የሁለተኛ ደረጃ የእሳት ወንፊት በተጨማሪ በእናንተ ላይ ተፈጻሚ ይሆናል፡፡*

## በአገራችን ያሉ የተለያዩ እምነቶች በሁለተኛው የእሳት ወንፊት የሚጠብቃቸው እጣቸው፡፡

በአገራችን ኢትዮጵያ የተንሰራፉ እምነቶች ብዙ ናቸው፡፡ ካቶሊክ፣ መናፍቅ፣ ተረት አምላኪ /ሙስሊም/ ሌሎችም እኒህ ሁሉ ታዲያ ሲደክሙ የኖሩትም ልፋታቸውም አንዲቷን የቀናች በልዑል የተወደደችና የተመሰረተች ተዋህዶ እምነትን ማጥፋት ግንባር ቀደም ስራቸው ነበር፡፡ ዛሬም ሁሉም እንደሚረዳውና እንደሚያየው፤ ገዢውም፤ መናፍቁም፣ ተረት አምላኪውም፤ ካቶሊኩም፤ በቅንብርና በስልት በቤተክርስቲያናችን ቁልፍ ቦታ ሁሉ መሽገው በተቀመጡት ተልእኮ ፈጻሚ መናፍቃን፤ ተሃድሶ፤ቅባት፤በሚባሉ በመታገዝ የጥፋት ስራቸውን ያለከልካይ እያከናወኑ ይገኛሉ፡፡

እኒህን የጥፋት ሰዎችና የእምነት ድርጅቶች ምን ይገጥማቸዋል፡፡ ሁለተኛው የእሳት ወንፊት ለነሱ ምን ይመስላል!

ከእንግዲህ ሁልህም የዲያቢሎስ ልጅ በሺዎች ዘመናት ስትፈጭ፣ ስትቆላን ኖረሃል፡፡ ያዘመንህ አብቅቶአል፡፡ ከዚህ በኋላ ጉዞህ ወደሲኦልና ወደጥልቁ እሳት ብቻ ሆኖአል፡፡ ከዚህ በኋላ ላንተ ከተገዙ ዝግንትሎችህ ጋራ በማያቋርጠው የእሳት ወንፊት እየተበጠርክ ትሄዳለህ፡፡ ጅማሮውም ታይቶአል! ቀጣዩም በ49 እጥፍ አድጎ ይቀጥላል፡፡ የአሁኑን አታልፈውም እንጂ በሺዎች በሚሊዮኖች እጥፍ ማብዛት የልዑል ችግር አይደለም፡፡ የልዑልን ቁጣ ቀስቅሰህ ካነደድክ ቆይተሃል፡፡ ትእግስት የሆነውን ላንተ እድሜ አይደለም በጥፋት ሂደት ውስጥ ይድኑ ዘንድ እጣቸው ለሆነ ሲባል እንጂ፡፡ በየጠረጋው ማእበል ውስጥ በምልክቱ መዝገብ ውስጥ የሰፈሩ ነገር ግን በተዋህዶ የእምነት መርከብ ውስጥ ያልተሳፈሩ ዲያቢሎስና ዓለም ያሳዘለቻቸውን ሸክማቸውን ዝግንትል ሁሉ በየቁጣው ሂደት ውስጥ እያራገፉ ከወደቁበት በታላቅ ስብራትና በመጸጸት እንዲሰበሰቡ ታስቦ መሆኑን ሁሉም ሊያውቀውና ሊረዳው ይገባል፡፡

በዋናነት ከሚመጡት ጥፋቶች በተጨማሪ በዚህ ርእስ ለተጠቀሳችሁም ሆነ በሁሉም ርእስ ስር ተጠቅሳችሁ፤ በመላው አለም ጭምር ላላችሁ ምልክት አልባ የአዳም ዘር በሙሉ ከዚህ የሚከተለው ታዞባችኋል፡፡

1/ ከተፈጥሮ አደጋው፤ ከማህበራዊ ቀውሱ፤ ከፖለቲካው ትርምስ፤ከኢኮኖሚውጥፋትና ቀውስ በተጨማሪ በተለምዶ ከምናውቃቸው መባርቅት ከንዋኔ ውጭ ፍፁም ታይቶም ተሰምቶ በማይታወቅ ጉልበት በብዙ ሙቶዎች ጉልበት ጨምረው በማያቋርጥ ፍሰት ምልክት አልባ የአዳም ዘርን ይፈጫሉ፡፡ መባርቅቱም በጠራራማ ፀሐይ ይሁን በደመና ቀንም ይሁን ሌት ጊዜንም ሆነ ሰዓት ሳይመርጡ፤ የተፈለገውን ስፍራ ለማጥፋት ይወርዳሉ፡፡ በተለይም የዘመኑ ገዢዎች፤ የጦርና የጸጥታ ሃላፊና ሰራተኞች፤ ሞኖፖሊስቶች፤ የተዋህዶ እምነት ጠላቶች ሁሉ ግንባር ቀደም ተመቺ ይሆናሉ፡፡ በዚህ የቁጣ በትር የሚሙቱ ሞት ከወሰዳቸው እድለኞች ናቸው፡፡ ካልወሰዳቸው ግን የነሱን ስቃይ ማየት ደግሞ ለተመልካቹ ለራሱ እጅግ ጭንቀት የሚፈጥር ይሆናል፡፡ በብዙ ሀገሮች እንደሚታዩት ሙብረቅ ከዝናብ ጋር፤ ከከባድ መእበሎች፤ እንደ ቶርኔዶ ከመሳሰሉ ጋር የሚከሰቱ ቢሆንም መጪዎቹ የተለዩ ናቸው፡፡ በአገራችን የ2003 ዓ. ም. የክረምት መግቢያ ላይ በመላው ሃገሪቱ የተከሰቱት ሙብረቆች ብዙ ከብትን፤ ብዙ የኤሌክትሪክ ተሸካሚና ትራንስፎርመሮችና እንዲሁም ሰዎችን በዝናብና በደመና ወቅትም አልፎም በደረቅ ፀሐይም በመውረድ ጉዳት አድርሰዋል፡፡ እነዚህ መጪውን ለማመላከት የ ተከናወኑ ምልክቶች ናቸው፡፡ መጪው በጋ ክረምት መፀው የማይል ነው፡፡

እነዚህ መባርቅት ሰውን ለመምታት ብቻ አይደለም የሚመጡት፤ ከዚህም ውጪ ማንኛውንም የዲያቢሎስ መጠቀሚያ ያጠፋሉ፡፡ ጦራቸውን ፤ ክምችታቸውን የማደራጃ፤ የመፈብረኪያ ስፍራቸውን ድሃን ለመፍጀትና ለመግዛት የሚጠቀሙበትን የጸጥታም ሆነ የማፈኛ ተቋም ሁሉ ይጠርጋሉ፡፡ መባርቅት ቅዱሳን መላእክት ከጨበጡት ቁጥር የለሽ ሃይል ውስጥ አንዱ ናቸው፡፡ እኒህ መባርቅት በተለምዶ ከምናየው የመባርቅት ሃይል በ49 እጥፍ ጉልበት የማውደም ሃይል ይዘው ይመጣሉ፡፡

2/ የአዳም ዘር! እስካሁን የምታውቀው የቅጣት ማእበል ሁሉ ከብዶ ቢመጣም በታሪክም በማየትም በመስማትም ታውቀዋለህ የማታውቀው ፍጥረቱን ምን እንደሆነ የማትለየው የአውሬ አይነት ምድሪቱን ይከድናል፡፡ ከፊል ሰው፤ ከፊል አውሬ፤አውሬ መሰል ኢጋንንት፤ የተለየዩ አውሬዎችን መልክ የቀላቀለ አውሬ ሌትም ቀንም ምልክት አልባውን ለመብላት ይዘምታል፡፡ የሰው ልጅ የያደራጀው ማንኛውም መሳሪያ እያጠፋቸውም ለቅጣቱ የላካቸው የሰራዊት ጌታ እስካላነሳቸው ድረስ! ይህ የሚሆነው ደግሞ የታዘዙትን አጠናቀው ሲጨርሱና የዑል ህዝቦች ሁሉን ተረክበው ሲደላደሉ ብቻ ይሆናል፡፡

የልዑል ሕዝቦች በተወሰነላቸው በየመኖሪያቸው ላይ ምልክትና ጥበቃ ስለሚኖር መግባት አይቻልም፡፡ ፈቅደው ከሚያስጠልሉት በስተቀር፡፡

3/ የሰው ዘር ሰምቶትም አይቶትም ወይም ይሆናል ብሎ ገምቶት የማያውቀው ብዙ ሚሊዮኖችን የሚየጠፋ የበሽታ ዓይነት ይከሰታል፡፡ ያለከልካይም ይጠርጋል፡፡

## 2/ሐ የአገራችን ኢትዮጵያ ገዢዎችና ምንዝሮቻቸው በ2ኛው የእሳት ወንፊት ውስጥ /የነሱ ድጋፍ ሰጪ አዛዥ መካሪዎችም/ እጣቸው፡፡

የሃጢያተኞችም ወገናቸው እንደ ገለባ ክምር ነው፡፡ ፍጻሚያቸውም ለገሃነም ይሆናል፡፡ የሃጢያተኞች ስራቸው ክፉ ነው ፍጻሜዋም ገሃነም ነው፡፡ መጽኃፈ ሲራክ ም፤ 21 ፡ 9 – 10

ስለ ኢትዮጵያ እጣ ፈንታ እሰከዛሬ በወጡት መልእክቶች ውስጥ በሰፊው ተገልጦአል፡፡ ይህ ርእስ የሚዳስሰው ገዢዎቻችን ምን እየሰሩ ነው! ለስራቸውስ ምን ይገባቸዋል! የሚለውን ሲሆን፤ ስለ አገዛዛቸው በአገራችንና፤ በሕዝባችን፤ በእምነታችን፤ በታሪካችንም ላይ የሰሩትን በጥቅሉ በመዳሰስ፤ መጪው እጣቸውንም የምናይበት ርእስ ነው፡፡

አገራችን ኢትዮጵያ በዘመኗ ሁሉ ስትፈተን ኖራለች፤- ነገር ግን ያለፍንበትን የ20 ዓመታትን የሚመስል የጉዳት ዘመን የለም፡፡ የዛሬው ገዢዎቻችን እነማን ናቸው ? እነዚህ እጅግ የከፉ ሕዝብን፤ አገርን፣ እምነትን ለማጥፋት ተማምለው የተነሱና ጠፍተውም አጥፍተውም እዚህ የደረሱ ናቸው፡፡ ገዢዎቻችን ለራሳቸው ብቻ አልተፈጠሩም፤ እዚህ ድረስ ለመድረስም ብቻቸውን አልተጓዙም፤ ዛሬም ብቻቸውን አልቆሙም፡፡ እነዚህ ገዢዎቻችን በአገራችን በኢትዮጵያ ላይና በተለይም በተዋህዶ እምነታችን ላይም ፍፁም በደማቸው የተዋህዶ በዘራቸው ጭምር የተላለፈ ጥላቻን የተሞሉ ናቸው፡፡ ሕዝቡን በጥቅሉ በተለይም ደግሞ ተዋህዶነትንና ኢትዮጵያዊነትን በጥቅሉ የያዘውን የሰሜኑን ሕዝብ እጅግ ይጠላሉ፡፡ ቢቻላቸው እንደ ሕዝብ ሙሉ በሙሉ ቢጠፋላቸው ደስታቸው ነው፡፡ ይህም ሲባል የትግራይ ሕዝብ የሰሜ ን ሰው አይደለም ወይ በሱስ አጥደለም ወይ የሚገለገሉትና የሚታገዙት የሚል ስሜት ይጭራል፡፡ አዎን ተጠቅመውበታል፡፡ አሁንም በጥቂቱ በግሉ በራሱ በብዙው በስሙ እየተጠቀሙበት ይገኛሉ፡፡ ይህም ሲባል አገርን፣

እምነትን አልበደሉም ማለት አየደለም በተለይ ወጣቱ ለዚህ ጥፋት የሚዘርፉና የሚያሰቃዩ አሉ፡፡ ነገር ግን የወደቁትን ሴትና ወንድ መነኮሳትን ለማየት እንደ ማስረጃ የሚሆኑአችሁ ድንግልን ለመሳለም 15 ቀን በእግራቸው ተጉዘዉ ግሸን የሚመጡትን ብታዩአቸውና ብትጠይቁአቸው በቂ ነው፡፡ በትግራይ ሁለት ገጽታን ትመለከታላችሁ፡- አንደኛ በረሃብ ውስጥ ሆኖ እምነቱን ተዋህዶነቱን አጥብቆ የሚኖርበትን፣ ሁለተኛው በገዢዎቹ ተመክቶ በታጋይነት ተኩራርቶ በወገኖቹ ደም፣ በኢትዮጵያውያን ርሃብና ጭንቅ እየተሳለቀ የመጣና አሁንም በዛው ጥፋት ውስጥ ያለው ብዙ ነው፡፡ በተጻራሪው በተዋህዶ እምነታቸው ጸንተው፣ በትግራይ በረሃ የወደቁ ብዙ አባቶች መነኮሳት እንዳሉ ሁሉም የሚያውቀው ነው፡፡ የዛሬዎቹ ገዢዎቻችን የዛሬው ትውልድ ታሪኩንና ተዋህዶ እምነቱን እንዲያውቅ የመጀመሪያውን የማጥፋት ስራ የሰሩት በዚሁ በትግራይ ውስጥ ነው፡፡ በቁጥረ ከ80 የማያንሱ በእምነታቸው በኢትዮጵያዊነታቸው የሚታወቁትን፤ በሃገሬው ሕዝብ ከበሬታ የነበራቸውን፤ ኋላ ቀር ናቸውበሚል ዲያቢሎሳዊ ፍልስፍና፣ የትግራይ ወጣት በድርጅታዊ አሰራር እንዲቀበል በማድረግ፣ ታሪኩንና ተዋህዶ እምነቱን የሚነግረውና የሚያስጨብጠው እንዲያጣ ለማድረግ እንዲወገዱ አድርገዋል፡፡ የጨለማ ሸራ ተሸፍኖ አይቀርም፡፡ ዛሬ ስለነሱ ወደር የሌለው የሃገር ጥፋት አብረዋቸው ውለው የነበሩ ለጠላታቸው መጠቀሚያ መሆናቸውን የተረዱ የተፈጸመውን እየተፈጸመም ያለውን የሃገር ማጥፋት ወንጀል እየነገሩን ይገኛሉ፡፡

ገዢዎቻችን ዛሬ ሙሉ በሙሉ የባህረ ነጋሽ /ኤርትራ/ ተወላጆች ናቸው፡፡ ይህ ደግሞ ዛሬ የአደባባይ ሚስጥር ሆኖአል፡፡ ምን ቢሸፍኑ ልዑል አምላካችን ወደ አደባባይ ወደብርሃን ማንኛውንም የጥፋት ስራ ያወጣዋል፡፡ አገሪቷን ጠልተው ከሄዱ በኋላ አለም አቀፍ ቅንብር በተደረገበት እርዳ ተረዳዳ የአገሪቱን ሀብት እየዘረፉ ይገኛሉ፡፡ መንግስት የራሳቸው፣ ደኅንነቱ፣ ወታደሩ፣ ሚኒስቴሩ፣ ኮምሽነሩ፣ ሁሉም ስልጣን የተባለች በሙሉ በራሳቸው ተጠቃሎ ተይዞአል፡፡ የሃገሪቱ ባንክ፤ ኢንሹራንስ፣ ግንባታ፣ ኢንቨስትመንት፣ አስመጪ ላኪነት ሁሉም የኢኮኖሚ እንቅስቃሴ በነዚሁ ሰዎች ተይዞ ሕዝቡ በሙሉ በሕግ ሽፋን በልማት ሽፋን በሚወጡ መመሪያዎችና ማስገደጃዎች እየተነጠቀና እየተዘረፈ ይገኛል፡፡

የነዚህ ደጋፊዎች ደግሞ ካናት ካለችው ባቢሎን ጀምሮ የተወሰኑ የአረብ ሃገራትን አካቶ እንደ ቻይናና ህንድ የመሳሰሉትን የአጋንንትና ጣኦት አምላኪዎች ጨምሮ ይህቺን አንዲት የተዋህዶ እምነት ሃገር ለማጥፋት እስከዛሬ እየደከሙ አሉ፡፡ ሕዝቡን በዘር ከፋፍለዋል! ኢኮኖሚውን ወርሰዋል፤ ቤቱን አፍርሰዋል፤ በቦታው የራሳቸውን ህንጻ ገንብተዋል፤ በግብር ስም ያላፈራውን ያላገኘውን ውለድ ብለው ኑሮውን አፍርሰው ለረሃብ ሰጥተውታል፡፡ በአገሪቱ ለነሱ የታመኑ፣ በሆዳቸው የሚያስቡ፣ ሰለአገር፣ ስለእምነት ቦታ የሌላቸውን መልምለው በመላ አገሪቱ ፈሰው ለነሱ እንዲሰልሉ የነሱን አገዛዝ እንዲጠብቁ አድርገዋል፡፡

የአገሪቱን ታሪክ የተዋህዶ እምነቱን የአባቶቹን መሰረቱን ለማጥፋት ቅርሱን ይዘርፋሉ፣ በርዘው ከልሰው ስለተዋህዶ እምነቱ ስለአገሩ ታሪክ ምንም እንዳያውቅ በሁሉም ሕይወቱ ዙሪያ የተደራጀ መምሪያ አደራጅተው እያጠፉት ይገኛሉ፡፡የተለያየ የተበረዘ ስለታሪካችንም፣ ስለተዋህዶ እምነታችንም የተደለዘ ጽሁፍ ይበትናሉ፡፡

አገራችንን በማጥፋቱ ስራና ውጥን ውስጥ እነግብፅ፣ እነባሕረ ነጋሽ፣ እነሱዳን፣እነጅቡቲ፣እኒህ ሁሉ ኢትዮጵያን የማጥፋቱ አካሎች ናቸው፡፡ ትላንት ደግሞ የኛው ግዛት የነበሩ ናቸው፡፡

በኢትዮጵያ ላይ የሚካሄደው ዘመቻ በዋናነት እነአሜሪካ፣ ከአውሮፓ፣ እነእንግሊዝ፣ እነፈረንሳይ፤ ከኤስያ እነሕንድ፣ እነቻይና፣ ከአረብ አገራት የሆኑም የሚሳተፉበት ነው፡፡ ስለነዚህ አገራትም ሁሉ ስለሁሉም የቀደሙትን መልእክቶች ማየት እጅግ ጠቃሚ ነው፡፡ ምክንያቱም የሁሉም አገሮች ስራቸው የተመዘነበት ፍርዳቸው ሰፍሮ ይገኛልና፡፤ ለመንደርደረያ ያህል ይህን ካልን በመጪው የሁለተኛው የእሳት ማበጠሪያ ገዢዎቻችንና ምንዝሮቻቸው እንዲሁም በዙሪያችን ያሉ ለጥፋታችን እየሰሩ ያሉ አገሮችስ በ2ኛው የእሳት ማበጠሪያ እጣቸው ምንድነው ?

በገዢዎቻችንና ቁጥራቸው በሚሊዮን የሚቆጠር አገልጋዮቻቸው ላይ የተወሰነ ፍርድ በቀደሙት መልእክቶች እንዳለ ሆኖ በሁለተኛው እሳት ይበጠሩ ዘንድ ይህ ትእዛዝ በልዑል ፈቃድ ወጥቶአል፡፡

አምስተኛውም መላክ ነፋ፣ ከሰማይ ወደምድር ወድቆ የነበረ ኮከብ አየሁ፤ የጥልቁም ጉድጓድ መክፈቻ ተሰጠው የጥልቁን ጉድጓድ ከፈተው፣ ጢስም ከተላቅ እቶን እንደሚወጣ ጢስ ሆኖ ከጉድጓድ ወጣ፤ ፀሀይና አየርም በጉድጓዱ ጭስ ጨለሙ፤ ከጢሱም አንበጣዎች ወደ ምድር ወጡ፤ የምድርም ጊንጦች ስልጣን እንዳላቸው ስልጣን ተሰጣቸው፤ የእግዚአብሄር ማህተም በግምባራቸው ከሌለባቸው ሰዎች በቀር በምድር ያለውን ሳር፣ ቢሆን ወይም ማናቸውንም የለመለመ ነገር ወይም ማናቸውንም ዛፍ እንደይጎዱ ተባለላቸው፣ አምስት ወርም ሊያሰቃዩአቸው ተሰጣቸው እንጂ ሊገድሉአቸው አይደለም፣ እነርሱም የሚያሰቃዩት ስቃይ ጊንጥ ሰውን ነድፎ እንደሚያሰቃይ ነው በዚህም ወራት ሰዎች ሞትን ይፈልጋሉ አያገኙትምም፣ ሊሞቱም ይመኛሉ ሞትም ከነርሱ ይሸሻል፣ የአንበጣዎችም መልክ ለጦርነት እንደተዘጋጁ ፈረሶች ነው፣ በራሳቸውም ላይ ወርቅ እንደሚመስሉ አክሊሎች ነበሩአቸው፣ ፊታቸውም እንደ ሰው ፊት ነበረ፣ የሴቶቹን ጠጉር የሚመስል ጠጉር ነበራቸው፣ ጥርሳቸውም እንደ አንበሳ ጥርስ ነበረ፣ የብረት ጥሩር የሚመስልም ጥሩር ነበራቸው፣የክንፋቸውም ድምጽ ወደጦርነት እንደሚጋልቡ እንደ ብዙ ፈረሶች ሰረገላዎች ድምጽ ነበረ፣ እንደ ጊንጥም ጅራት ያለ ጅራት አላቸው፣ በጅራታቸውም መውጊያ አለ፤ ሰዎችንም

አምስት ወር እንዲጎዱ ስልጣን አላቸው፣ በእነርሱም ላይ ንጉስ አላቸው፣ እርሱም የጥልቅ መልአክ ነው፣ ስሙም በእብራይስጥ አብዶን በግሪክ አጶልዮን ይባላል፣ የዮሃንስ ረእይ ም. 9 ፤ 1 – 11

ስለሚመጡት ጠራጊዎች ታውቁ ዘንድ እኒህም ጠራጊዎች ከሌሎች ጋር ሆነው ሁሉንም የሰው ዘር ምልክት የሌለውን ሁሉ ሊያጳዱ፣ ሊያሰቃዩ፣ ሊገሉ፣ሊቆረጥሙ ስልጣን አላቸው ከዚህ በታች ያለው ትእዛዝም እነዚህን መቅሰፍቶች ያካተተና የልዑልን ትእዛዝ ለመፈጸም በተጠንቀቅ የቆመ ነው:: የሚጠብቀውም የዚህን መልእክት መውጣት ብቻ ነው:: የቅጣት ትእዛዝም በወጣባቸው ሁሉ ላይ ትእዛዙን ተከትለው ለአፈጻጸሙ በምድሪቱ ሁሉ ላይ የሚዘምቱ ሃይሎች ናቸው::

# ትእዛዞች

- አገራችንን ኢትዮጵያን ባሁኑ ጊዜ በመግዛት ላይ የሚገኙት፡- ጠቅላይ ሚኒስትር፣ ፕሬዚዳንት፣ በጠቅላይ ሚኒስትሩ የሚመሩ ሚኒስትሮች፣ ም/ሚኒስተሮች፣ ሚኒስትር ደኤታዎች፣ ኮምሽነሮች፣ የፌደራል ሃላፊዎች፣ የየክልሉ የፀጥታ አስተዳደር፣ የፍትህ መሪዎች፣ ስርአቱን በሃይልነት ደግፈው የቆሙ ሃይላት /ፖሊስ፣ ወታደር፣ መረጃ/ እንዲሁም ስርዓቱ ላቆመው መንግስት በአባልነት ቅጽ ተሞልተው ላሉ ሁሉ፣ በስወርና በግልጽ በተቃዋሚነት ስም የቆሙ መስለው ለስርአቱ ታማኝ አገልጋይ ለሆኑ፣ በየቀበሌው ፈሰው ለአገዛዙ በታማኝነት ቆመው የሕዝቡን የየእለት ሕይወቱን ጭምር ለገገርው ስርዓት እንዲገብር የሚያደርጉ፣ በተለያየ ምክንያት ከራሱም ከልጆቹም አፍ እየነጠቁ የሚወስዱ ሁሉ፣ እንደ ህዝብ ተደራጅተው የኢትዮጵያን ህዝብ እንደ መሰረታዊ ጠላት ቆጥረው ለዘመቱበት ሁሉ፡-
- ተዋህዶ እምነታችንን ለማዳከም ከመናፍቃን፣ ከተረት አምላኪዎች፣ ከካቶሊኮች፣ ከጥንቆላና አምልኮ ባእድ አምላኪዎች ጋር በመመሳጠር፣ ስልጣናቸውን በመመካት ለተዋህዶ ቤተ ክርስቲያናችን መጥፋት ለሚሰሩ ሁሉ፤
- ኢትዮጵያዊነትን ክደው፣ ከአካልነታቸው ተገንጥለው፤ ተመልሰው በስርአቱ አጋፋሪነት አገሪቱን ተዋህዶ እምነት፣ ለማጥፋት ለሚሰሩ፣ በአገሪቱ ኢኮኖሚውን ተቆጣጥረው የሚዘርፉ፣ በዘረኛነት ተቧድነው የሌላውን ኢትዮጵያዊ ወገናቸውን አገለለው፣ የዘር ቀጠና ፈጥረው ምድሪቱንም ለዘር ቡድናቸው የሚሸነሽኑ፣ ለስርአቱ ከፋፍለህ ግዛ ፖሊሲ አስፈፃሚ የሆኑ፣ በዚህም የበለፀጉ ንብረት ሃብት በውጭ ያከማቹ፣ ይኸንኑ የአገርና የተዋህዶ እምነት ጥፋት ከውጭ ሆነው የሚያበረታቱ፣ የሚደግፉ፣ በድርጊቱም የሚሳተፉ ሁሉ፤
- አገሪቱንና የጸና ተዋህዶ እምነቷን ለማጥፋት፤ ከአገሪቱ አናት፣ እጅ፣ አግርና መላ አካሉዋን ወረው እያጠፉ ላሉ ከበስተጀርባ ሆነው፤ በአገርም በውጪም በጨበጡት የዳቢሎስ ስልጣን ተመክተው አመራርና፤ የሁሉን አቀፍ እገዛ ለሚያደርጉ ሁሉ
- በማዘዙ በመወሰኑ ላሉት ከዋናው መሪ ጀምሮ እስከ ስር ድረስ፤ ከዚህ የሚከተለው ቅጣት በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል ተፈጻሚ ይሆን ዘንድ ታዞአል::

ሀ/ ሞት እረፍት ነው:: ለአገሪቱ 20 ዓመታትን ሙሉ ለሞቷ ስትደክሙ ኖራችኋል:: ስለሆነም ሞት አይሰጣችሁም:: ሞትን ትለምናላችሁ አይሰጣችሁም፤ ትፈልጉታላችሁ አታገኙትም፤ ይቀርባችኋል፤ ነገር ግን ካልታዘዘ አይወስዳችሁም፤ ይህንንም ሁሉ የሚያስመኛችሁ በርባሪ እሳት ታዞባችኋል:: እንቅልፍም በአይናችሁ አይዞርም:: መኝታችሁ እሳት ሆኖ ይበላችኋል:: እራሳችሁን ለማጥፋት ትሻላችሁ አይቻልም:: ማረፍ ትፈልጋላችሁ አይታሰብም:: ለመደበቅ፣ ለመሸሽ ትደከማላችሁ በፍጹም አይቻልም:: የትኛውም ያደራጃችሁት ሃብት ንብረት፣ ሃይል በሙሉ ይጠፋል፤ ዘራችሁ ከናንተ የመነጨ ነውና አይቀጥልም:: ያለውም እጣው በናንተው ስራ ይወሰናል:: ከዚህ በፊት ያልታዩ ሰምታችሁትም የማታውቁ የተቀላቀለ ገጽታና አካል ያላቸው አውሬዎች ምልክት አልባውን ለመቆረጣጠም በመላው አለም በኛም አገር ይፈሳሉ:: በምንም አይነት ሃይል አይጠፉም:: ሌትም ቀንም ይሰማራሉ:: ምንም ምሽግ ምንም አይነት ቤት፤ አጥር አያግዳቸውም:: በወላዲት አምላክ፣ በከበሩት ቅዱሳን መላእክት፣ በቤታቸው ላይ ምልክት ( መሃተም) ያረፈባቸውን አይደፍሩም:: ቤቱም ድንግል ባሰማራቻቸው ቅዱሳን የብርሃን መላእክት ይጠበቃሉና:: ገዳማት፣ አድባራትም እንዲሁም በልዑል ሰራዊት በቅዱሳን መላእክት ይጠበቃሉ::ማንም ወደ ተጠበቁት ቤቶች መግባት አይችሉም:: ካልተፈቀደለት በስተቀር፤ በኃይል የሚሞክሩ ይመታሉ:: በገዳማትም ለመግባት ፍጹም አይቻልም በውስጣቸው ያሉ ምልክት አልባዎችም ይጠረጋሉ፤ በገዳማት የቀራችሁት የእግዚአብሄር ሕዝቦች ስርአቱ ሳይጎድል በቀራችሁት ቁጥር አገልግሎታችሁን መቀጠል አለባችሁ

ለ/ መባርቅት በ49 እጥፍ ጉልበት ይመጡባችኋል፤ የትኛውም ምሽግ ውስጥ ተወተፉ ያጠፉአችኋል:: ከመሃላችሁ በመባርቅት ሞትን ያገኘውን እድለኛ ነው ብላችሁ ትቀኑበታላችሁ:: በአመጽ አድጋችሁ በአመጽ ላረጃችሁ ለናንተ ሲኦልንና ገሃነምን በህይወት ቆማችሁ ትለማመኑታላችሁ:: ወደ ውጭ እሸሻለሁ የለም እዚያም ይኸው ትእዛዝ በብዙ እጥፍ ኃይል የጸና ነው:: መሸሸጊያ የሚባል በምድር ላይ የለም ሁሉም የልዑል ገንዘቡ የእጁም ስራና ታዛዦችም ናቸውና:: ሽባና ምናምንቴ የሚያደርጉ ሰምታችሁ የማታውቋቸው መድሃኒት አልባ በሽታዎች ይይዟችኋል::ምንጫቸውም በምንም ዘዴ አይታወቅም::መዳኛም የላቸውም:: በስልጣናችሁ ተ መኪታችሁ፤ የድሃውን ሕዝብ ስጋውን በልታችሁ፤ አጥንቱን በመቆርጠም ላይ ያላችሁ፤ ይህም አንሶአችሁ በባእድ

ሃገር ሃበት ያከማቻችሁ ሁሉ፤ የናንተም ተባባሪ ሸሻጊ የሆኑ መንግስትና ድርጅቶች ሁሉ ከላይ የተጠቀሰው ቅጣት ተፈጻሚ ይሆንባችኋል፡፡

ሐ/ ለአለም ሕዝብ የታዘዘው ( በመልእክቶች 1፤ 2፤ 3 ) የተጠቀሰው ቅጣት በአገራችንም በማንም ሰው በልኩ ልብስ እንደሚያሰፋለት ለኢትዮጵያ አገራችንም በጥቅሉ በአቅሟ ቅጣቱ ይፈሱባታል፡፡

መ/ በመልእክት 4 የታዘዙ ትእዛዞች እንዳሉ ሆነው ያገራችን መሪ የጊዜ ገደብ ተደርጎ ስልጣናቸውን እንዲያስረክቡ ተነግሮአቸው ነበር፡፡ በዚህ እድል ሳይጠቀሙ ቀርተዋል፡፡ እግዚአብሄር አምላካችን ማንም ሰው በሃጢያቱ እንዲጠፋ ፈልጎ አያውቅም ሰው በራሱ ምርጫ ከዲያቢሎስ ጋር ሁኖ ይጠፋል እንጂ፡፡ ይህን ሁሉ ወንጀል በአገራችን፣ በእምነታችን፣ በህይወታችን፣ በንብረታችን ላይ የፈጸመ ያስፈጸሙ መሪና ምንዝሩ የንስሃና የመጸጸቻ እድል ተሰጠው ናቀ፤ ተሳለቀ፤ በጥፋቱም በማንአለብኝነት እነሆ ገፋበት፡፡ መልእክት 4 የጊዜውን ማለቅ አብስሮአል ይህ ከተገለጸም አመት ከስድስት ወር ሆነው፡፡ ጊዜው የረዘመ ሊመስለን ይችላል፡፡ ይሰሩ ዘንድ የሚገባቸው ስራዎች እየተከናወኑ ይገኛሉ፡፡ በራስህ ሕይወት ዙሪያ ያለውን እሳት እይ፣ ኑሮህን መርምረው፣ መንገዱ እየተጠረገ ነው፣ አንዳች ሳየፈጸም የሚቀር የለም፡፡ ልዑል በወሰናት ሰዓት ትከናወናለች፡፡ መሪዎቻችንም ትእቢታቸው የወለደላቸውን ብርቱ ጥቃት በዚህ መልእክት መታዘዙን ከላይ ባሉት ርእሶች መስፈራቸውን ተረጋግጦአልና ይወቁት፡፡

መልእክት 4ን በትክክል ሊረዱት ያልቻሉ ቅን ወገኖች እንዳሉ ሁሉ አንዳንዶች የመልእክቱን አንድ አንድ አካል ባልተባለ ባእድ ቃል የመልእክቱን አቅጣጫ ሊያስቱ ሞክረዋል፡፡ ለነዚህ የሚታዘዘው ቅጣት ታዞላቸዋል በየግላቸው ያገኙታል፡፡ መልእክት 4 የሚያሳየን ገጽታ ሙሴ እስራኤላውያንን ነጻ የማውጣት ስራውን ሊያከናውን በፈርኦንና በመሰሎቹ የታየን ሁኔታ የሚመሳሰል መልክ ይታይበታል፡፡ፈርኦን የእስራኤልን ሕዝብ እንዲለቅ ሙሴ ሲጠይቀው መልሱ የትእቢት፣ የንቀት ነበር ከ7 ያላነሱ ቅጣቶች ሲፈሱ በትእቢት ፀንቶ ነበር፡፡ ሁዋላ ላይ የታመነበትን ሰራዊት ሲያጣ ግን የእግዚአብሄርን ምንነት አወቀ፡፡ የኛ መንግስት ተነገረው ናቀ፤ በሁሉም ዘርፍ በኢኮኖሚውም፣ ፖለቲካውም፣ ማህበራዊ ሕይወቱም ተመታ ደቀቀ አልሰማም፡፡ ስለሆነም እነሆ ዛሬ ብርቱ ቅጣት በራሱም በሁሉም መገልገያው ላይ ታዞአል፡፡ የዛሬው ከፈርኦን ዘመን በላይ እንደ ተጨማሪ የሚወሰደው ቅጣት አለ፡፡ ያኔ ፈርኦን የእግዚአብሄርን ምንነት አይቶ አምኖአል፡፡ በራሱ ላይ በደረሰው ጥፋት ከቀድሞውም እምነት ባይኖረውም የፈጣሪውን ያህል አምኖ ተቀበለ፡፡ የዛሬዎቹ የኛው ሸከሞች ግን የፈርኦንን ታሪክ ያውቃሉ፡፡ በራሳቸውም በደረሰባቸውም ያለውን ያያሉ፡፡ ገናም እሳቱን ተግተው ይደመድማሉ፡፡

ፈረኦን ሶካር! ዛሬ ለእነሱ ስሙን በቀየረው በትላንቱም ያው፣ በዛሬውም ያው የሆነውን ዲያቢሎስ ወይም የዘመኑን ሶካር ያምናሉ ይታመናሉ፡፡ ሶካር ድረስልን፣ ፍጭልን፣ ቁላልን እያሉት ነው፡፡ በዚህ ልንደነቅ አይገባንም፡፡ ሙሴ የእግዚአብሄርን ጸጋና ጉልበት ለብሶ ከፈርኦን ጋር የነበረውን ትግል በድል አጠናቋል፡፡ የፈጀውን ጊዜ ይፍጅ ታሪኩ ከፈርኦን ጋር የተካሄደውን ትግል ምን ያህል ጊዜ እንደከደነ ባይነግረንም፤ ድል ግን የእግዚአብሄር ሕዝብ ትሆናለች፡፡ ስለዚህም በጥርጥር የተሞላህ ወገኔ ጠላት የዘራብህን አረም ከልብህ ንቀልና አውጣ በፈጣሪህ አምላክ በገባልህም የማይናወጥ ቃል ኪዳን ታመን፡፡ እግዚአበሄርን ማስደሰት የሚቻለው በእምነት ብቻ ነው፡፡ እምነትም ያላየነውን ነገር ግን እንደእግዚአብሄር ፈቀድና ቃል ይሆናል ብለን፤ በተስፋው ጸንተን የምንቀበለው ማለት ነው፡፡

ስለኢትዮጵያ የቅጣት ፍሰትና ስለ ትእዛዞቹ ማጠቃለያ፡-

በዚህ የሁለተኛው የእሳት ወንፊት የሚወርዱት ቅጣቶች ሁሉ፤ የቀደሙት መልእክቶች ሁሉ (1፤ 2፤ 3፤ ) እንዲሁም በመልእክት 4 ውስጥ የተጠቀሱት ፍርድና አፈጻጸማቸው እንደሚያረጋግጡት፤ የአዳም ዘር በሙሉ ከጥቅቶቹ በስተቀር፤ ንቆ ዛሬም እያፌዘ ስላለና በልዑል ትእግስትም በማላገጡ፤ ይህ የሁለተኛው የእሳት ወንፊት በልዑል ፈቃድ በኔ በባሪያው በኩል ትእዛዙ እነሆ ተገልጾአል፡፡

በአሁኑ እሳት ውስጥ ማንም ምልክት አልባ አያልፍበትም፡፡ ሁሉንም ወንጀላቸውን፣ ስራቸውን በአደባባይ በማናቸውም የዜና ማሰራጫ፤ በጋዜጣ፤ በመጽሔት፣ በሬዲዮና በቴሌቪዥን ሳያቋርጡ መናዘዝን፣ ሙሉውን መልእክት የኽንንም 5ኛውን መልእክት ጨምሮ በሁሉም መገናኛ ብዙሃን፤ ቀንም ማታም አንዲት ቃል ሳትጎድል መግለፅ አለባቸው፡፡ ከሚፈስባቸውም እሳት የአንዲት ሰዓት እረፍት ለማግኘት፣ የነሱ ስቃይ ከታዘዘው የእሳት ወንፊት ወጥቶ ወደ መደበኛ የቅጣት ዓለም መሸጋገር የሚቻለው፤ የእግዚአብሄር መንግስት ጸንቶ፤ ባሮቹ ልዑል ባዘጋጀላቸው ዙፋን ላይ አርፈው የፍርድ ውሳኔአቸውን ሲያጸኑ ብቻ ነው፡፡ ከዚህ ሂደት ቀድሞ ማንኛውም የአለም ሃገራት መሪና ምንዝሮቹ፤ እጃቸውን በኢትዮጵያ ለሚጸናው በአንዲት ተዋህዶ እምነት ለጸና መንግስት መስጠትና በፍርድ መካተት ይጠበቅባቸዋል፡፡ ተጨማሪና ተከታታይ ትእዛዞችን መፈጸምም ግድ ይላቸዋል፡፡ ከዚህ ውጪ ማንኛውም አገር፣ ሕዝብ፣ ግለሰብ፣ ድርጅት፣ ቡድን፣ መፍትሄ አገኛለሁ ብሎ ማሰብ የለበትም፡፡ ቢታሰብም ሰሚ የለውም፤ ለአሳቢውም ከንቱ የሆነ፣ የራሱንም፣ የወገኑንም፣ የሕዝቡንም መከራና የእሳት ፍም መጋምና ማጋል ብቻ ይሆናል፡፡

በቅጣቱ የወደቁ ሁሉ ዛሬም ስለዋናው ጉዳይ ስለገጠማቸው ፍርድ አምነውበት ቢድኑም ባይድኑም በፈጣሪያችን በሰራዊት ሁሉ ጌታ ፊት ወድቀው ፍርዱን በፀጋ ቢቀበሉ በተሻላቸው ነበር፡፡ ምንም ይሁን ምን በልዑል እጅ መውደቅ የተሻለ ነውና እኔ እንደራሴ አምላኬና እናቴ ወዳጆች የከበሩት መላእክት እንዳስተማሩኝ፣ እንደመከሩኝ እንደአሁኑ ከአቅም በላይ / በትእግስት ከሚታለፈው/ ፍፁም ባለፈ ባይሆን ኖሮ እስካሁንም ልዑል እንደሰጠኝ ትእግስት ባያቆየኝ ኖሮ አይቻልም ነበር፡፡ የሆነ ሆኖ ዛሬ የልዑልም፣ የድንግልም፣ የከበሩት ቅዱሳን መላእክትም ትእግስት ተጠናቆ ካበቃ ቆየ፡፡

የአዳም ዘር አድምጥ፣ ስማ ጆሮህን ጭው የሚያደርግ፣ በድንጋጤም ልብህን የሚሰነጥቅ እንኳን ወደ ሁለተኛው ወፍጮ መግባት ገና ጅምሩን ስታየው እምትደርስበት ይጠፋሃል፡፡ የትኛውም ዓለም አይሸሽግህም፡፡ ዓለም ሁሉ የጨለማ ( የዲያቢሎስ) ልጅ አሽቀንጥሮ ለሚበላውና ለሚቆረጥመው አውሬ (እሳተ ጎሞራ እንደሚተፋው ዓይነት የቀለጠ የእሳት ፈሳሽ) ውስጥ ትጥልሃለች፡፡ በቁምህ ገሃነምን ታየዋለህ፡፡ ክፉ ስራህ ያመጣው ፍርድ ነውና መቀበል ብቻ ነው፡፡

መ / ስለ ኢትዮጵያውያንና ስለ ባህረነጋሽ (ኤርትራ ) አሁኑ ገዥዎቻችን የተቀናጀ ኢትጵያውያንና ተዋህዶ እምነቷን ማጥፋት ተልእኮ

በኢትዮጵያ ሃገራችን ላይ የሚካሄደው፤ ሁሉን አቀፍ ሕዝብና ሃገራችንን የማጥፋት ስራ፤ እየተከናወነ ያለው በተቀናበረ፣ በግንባር ቀደም የኢትዮጵያና የባህረነጋሽ መሪዎች የሚመሩት የጥፋት ስራ ነው፡፡ ኢትዮጵያ ዛሬ ለደረሰችበት ድቀት ፣ ድህነት፣ የአገር መሸራረፍ ፣ የሕዝብ እልቂት፣ የተዋህዶ እምነቷን አንደ መቦርቦርና ጭርሱን ማጥፋት፤ ኢኮኖሚዋን በሙሉ ተቆጣጥሮ መዝረፍ፤ ሕዝቧን እርስ በእርስ በማፋጀት፣ ማንኛውም የታሪክ መሰረቷን ማጥፋት፤ ታሪኳን በማያውቁ መርገጥ፣ መግዛት፤ የብሄር ጥላቻን፣ ዘረኛነትን የታጠቁ፣ በኢትዮጵያ ታሪክ አንዳችም የሀገር መከላከል ውለታ የሌላቸው ህዳጣን ሰዎችን ጥላቻ መንፈስ አስታጥቆ፣ መርገጥ፣ መግዛት፣ የሃገሪቱን ቁልፍ፣ ኢኮኖሚ፣ የፖለቲካ፣ የእምነት፣ የማህበራዊ ሕይወት፣ማከናወኛ ስልጣኖችን በሙሉ፤ በነዚህ ሰዎች ማስያዝ፤ የታሪኩን፣ የእምነቱን ባለቤት በመላ ሕይወቱ ለይ በመዘመት የማፍረስ፣ የማሳደድ፣የመግደል፣ የማሰር፣ ያልተቋረጠ ጥፋት ማካሄድ፤እንደ ስራ በእቅድ ማካሄድ ዋና ስራቸው ነው፡፡ የባህረነጋሽ ሰዎች እንደ ቡድን ሳይሆን እንደ ሕዝብ ተዋቅረው ፤ በዚች ሃገር ላይ የልተቋረጠ ዘመቻ አካሂደዋል፡፡ እነዚህ ሰዎች ነጻ ነን ብለው፤ ከአገሪቱ 99 በመቶ ድምጽ ሰጥተው፤ የሄዱ ሲሆን፤ ይህ ድርጊታቸው ያልከበዳቸው እንደገና ለዲያብሎስ የተመቸ አካሄድ ይዘዋልና፤ የዚች ሃገር የጥፋቷ መሃንዲሶች ደግሞ እነዚህን ሰዎች በመሰረትነትና የኃይሉም የጸጥታውም የኢኮኖሚውም ተረካቢ አድርገው በኢትዮጵያ ሕዝብ ለይ ከጫኑአቸው 20 ዓመት አልፏቸዋል፡፡ በአሁኑ ሰአት በኢትዮጵያ ሕዝብ አናት ላይ ጠመንጃና ታንካቸውን መክተው ከላይ ሁሉንም የሃገሪቱን ሕይወት በማነቅ፤ በነዚሁ እንደ ሕዝብ በተደራጁ ኤርትራውያን እጅ ገብቶ፤ ኢትዮጵያም ሆነች ዓለም በታሪካቸው ያላዩት አመጽ፤ ዘረፋ፣ በመንግስትነት፣ በሕግ ሽፋን፣ በግብር፣ በልማት፣ ኢትዮጵያዊ ወገኔ ስጋው ተበልቶ አጥንቱ በመቅርጠም ላይ ይገኛል፡፡ የዚህ የጥፋት ቀዳሚ መሃንዲስ ጠቅላይ ሚንስትራችን ሲሆኑ ከመረጃ በስተጀርባ ደግሞ አመራሩንም ዘረፋውንም የሚመሩት የባህረነጋሹ ( ኤርትራ ) መሪና አገልጋዮቻቸው ናቸው፡፡

እኒህ ደፋሮችና ጨካኞች በዚህ በአንድ ተዋህዶ እምነቱ በጸና ህዝብ ላይ ዘምተው ለዲያብሎስ የየቀን ግዳይ የሚጥሉ ናቸው፡፡ ማናችንም እንደምናየው እንደምንሰማው፤ የሃገሪቱ ሃብት፤ ቅርስ፤ አለኝ የምትለው ሁሉ ተዘርፎ በውጭ ተከማችቷል፡፡ በየገዥው ቡድን አባላት የመሸሸጊያ ጎሬ በብዙ ስፍራ ተወትፎአል፡፡ ይህ የሃገር ጥፋቶች ከደቡብ፣ ከኦሮሚያ፣ ከምእራብም ከምስራቁም ተሰበሰቡ ስለኢትጵያ ታሪክ አንዳች የማያውቁ ሲጠየቁም ስለብሄራቸው መጨቆንና ነፃ መውጣት ገድል የሚነግሩን ምርኩዛቸው ሲሆኑ፤ ይህ ሽፋናቸው እንጂ እንዲያጠፉ አገሬ ኢትዮጵያ የሚለውን ሰው፤ በስራውም በንብረቱም ገብተው እንዲወስኑ አድርገዋል፡፡ የሁለቱ ሰዎቻችን ስትራተጂ ተግባሪዎችም ናቸው፡፡ ይህ ሁሉ ጥፋት በነባቢሎን የመናፍቁ ጌታ፣ በነተረት አምላኪዎች፤ ዲብሎስ ነፍሰ ገዳዮችን የአረብ አገራት፤ በድራጎንና ጣኦት አምላኪዎች ሁሉን አቀፍ ድጋፍ ሰጪነት የሚከናወን ነው፡፡

ለዚህ ሁሉ ታይቶም ተሰምቶም የማይታወቅ እንደ ሕዝብ ዘምቶ ዘርንና ምልክትን፣ አሻራንና ታሪክን፣ ኢኮኖሚንና ቀጣይ ዘርን የመግደል ስራ፤ በትእግስት ብዙ የእግዚአብሄር ሕዝቦች ወደፈጣሪያቸው በማመልከት በእንባቸውና በማያቋርጥ ጩኸታቸው ኃያሉን ጌታ ከመንበሩ በመቀስቀስ የልዑልን ውሳኔ አስገኝተዋል፡፡ ማንም አይታደገውም እንፈጨዋለን እንቆላዋለን ብላችሁ ጌታዋን ተማምና ሏቷን እውጭ እንዳሳደረቻው በግ ይህ ምስኪን ሕዝብ ላይ ተንሰራፍታችሁ ፤ ጥፍርና እግራችሁን ዘርግታችሁ፤ በማን አለብኝነት ተቀምጣችኋል፡፡ የእምነት ጀግኖች ተፈጥረዋል፡፡ዓለም ሰምታም የማታውቀውን እሳት ተጭኖ መጥቶላችኋል፡፡ የደማችሁለት ስልጣን፤ የሰበሰባችሁት ሃብት የደሃ ደምና አጥንት የተመካችሁበት ዘር አስተማርነው ከበረልን በአለም በትነን መሰረት አስይዘናል ፤ የምትሉት ዘራችሁ፤ ወገናችሁ፤ መሸሸጊያ ያላችሁት በሙሉ ፤ ለእሳት ተደብቆ፤ ከዚህ በታች ያለው የቅጣት ዝርዝር መግለጫ፤ በናንተና በሁለቱም ሃገር ገዥና አለቃ ምንዝሮቻችሁ እንደ ሕዝብ ተቧድኖ፤ የዘመተው፣ ዘራችሁና ተዳዳሪያችሁ ላይ፤ ተፈጻሚ ይሆን ዘንድ የልዑል ፈቃድና ትእዛዝ አርፎበታል፡፡ ተገጣሚም ይሆን ዘንድ የልዑል ትእዛዝና ፈቃድ በኔ በባሪው በኩል ከዚህ በታች ተዘርዝሮአል፡፡

የኢትዮጵያ ገዥዎችና የባህረነጋሽ ( ኤርትራ ) ገዥዎች ከነሱ ስር ሆነው የኢትዮጵን ህልውና ፣ ታሪክ የተዋህዶ እምነት፤ ኢኮኖሚ አጠቃላይ ሕይወቷንና ገጽታዋን በሙሉ ማጥፋት ከውጭ በዚሁ ዘርፍ ከተሰለፉ ጋር የመቀናጀት ስራ መስራትን እንደ እለት ከእለት ስራቸው የደረጉ ሁሉ ወንጀላቸው አንቀጽ ያልተበጀለት ፤ ሰውም በህሊናው ይፈጥረዋል ያልተባለ፤ የአለም ምርጠ የዘር፣ የሃገር፤ የተዋህዶ እምነት መግደል ስራ ሰለሰሩና እየሰሩም ስላሉ የመጀመሪያውንም ሆነ ሁለት ሶስት መልእክቶች ያቀፈውን ( ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን ) በሚል የተገለጸውን ፍርድና አፈጻጸም እያወቁ ከመጸጸት ይልቅ በጥፋታቸው እንደ ዓላማቸው ገፍተውበታል፡፡ የእግዚአብሄር የተመረጠን የክብር ሃገር ለማጥፋት እራሱን የምድርና የሰማዩን ባለቤት አጠፋለሁ ብሎ መዝመት እንደ ሆነ ማንም የሚረዳዉ ነው፡፡ ስለሆነም የእግዚአብሄር ቃል እንደሚነግረን (ከእግዚአብሄር ጋር የሚጣሉ ይደቅቃሉ) ይላል፡፡ እነዚህ ጉዶች ግን ከመጣላት በላይም፤ ዲያቢሎስ እንኳን መንበሩን ሊወርስ ነው የተመኘው እነዚህ ከመምህራቸው ከዲያቢሎስ በላይ ልዑልን ፈቃዱን ትእዛዙን ሁሉ እናጠፋለን ብለው የተነሱ ናቸው፡፡ ስለሆነም ለነዚህ ሞት ቶሎ አይሰጥም፡፡ ሞት እጅግ በጥቂቱ ለተሳተፉ የሚሰጥ ብቻ ነው፡፡ በጥፋቱ ጠልቀው ለገቡት ግን ሞት እንደሚመኙት አይቻልም በሕይወት ሆነው የሰበሰቡትን ይሆነኛል ያሉትን ሁለመናቸውን ያጡታል፡፡ ፍፁም እድል የማይሰጥ በርባሪ፣ ቆርጣሚ እሳት በባህሪያቸው ይሰለጥናል ምንም ማድረግ የማይችሉ ሽባዎች ይሆናሉ፡፡ በመላ አካላቸው ላይ ሁሉም በሽታዎች ይከድኑአቸዋል፡፡ እረፍትና እንቅልፍ ምድሪቱን እስከሚለቁ አያገኙአቸውም፡፡ ዓለምን በግርምት የሚያስደምም እሳት ቆርጥሞ ይጨርሳቸዋል፡፡ በዓለም ላይ በተለይ በነአሜሪካ፣ በነአውሮፓ፣ በነኤሽያ ላይ ተፈጻሚ ይሆኑ ዘንድ የታዘዙት ቅጣቶች በዚህ ርእስ ውስጥ ለተጠቀሰው ወንጀል ተጠያቂ በሆኑ ላይ ሁሉ ተፈጻሚ ይሆናሉ፡፡ የነሱ የጥፋት ተባባሪ የሆኑትም እንደ ተሳትፎአቸው የሚመጥነውን ቅጣት ይቀበላሉ፡፡ ኤርትራም ወደፊት የሚታወቅ ወይም የሚታወስ ምንም ቅሬት አይኖራትም፡፡ ሰው ያለ ማረጋገጫ በነበር ብቻ የሚያነሳት እንደ አፈ ታሪክ የሚያስቆጥር ወሬ ብቻ ሆና ትቀራለች፡፡

ዓለም በቅጣቱ ክብደት የሚደነግጥበት ይሆናል፡፡ የትኛውም የነሱ ዘር፤ በየትኛውም የዓለም ክፍል ይሽጉጡ እንደሰሩት ወንጀል ክብደት ቅጣቱ ተፈጻሚ ይሆናል፡፡ በተለይ ይህቺን የተመረጠች ሃገር ሳትበድላቸው በድለዋታልና፡፡ ሃገሪቱን ለባህረነጋሽ ሰዎች በዘመኑ ሁሉ በአናቷ ላይ አስቀምጣ ስቡን አብልታ ማርና ወተቱን አጠጥታ የቅምጥል ልጅ አድርጋ አኑራቸዋለች፡፡ ሌሎች የሃገሪቱ ዜጎች በልመና፣ በማጣት፣በእለት ተእለት ኑሮ ተቀይዶ ሲሰቃይ፣ እነዚህ ቅምጥሎች ግን በሁሉም የሃገሪቱ ሃብት ተጠቃሚ ሆነው ኖረዋል፡፤ እንዲህም ሆኖላቸው ነው ዛሬ ይህችን አገር በመዝረፍና በማፍረስ ላይ ያሉት፤ ስለዚህ በዚህ መልእክት ያልተካተተ፤ ለሰውም እንግዳ የሆነ፤ ዘግናኝ ብርቱ ቅጣት ነው እድላቸው፡፡ ሌላ እድል የላቸውም፡፡ በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል እነሆ ተገልጾአል፡፡ታዞላቸዋል፡፡ እስትንፋስ የሚገኘው ምንአልባትም ቢሆን እንደበላየሰብ ራስን በፈጣሪ እጅ በመተው ብቻ ሊሆን ይችላል፡፡ ምናልባት ከሚፈላው እሳት በልዑል ምህረት አግኝተው በመዳናቸው ለሰው ግርምት የሚያጭሩ በጣት የሚቆጠሩ ይታዩ ይሆናል፡፡

የመልእክቱ አስተዋይ አንባቢዎች፤ ከላይ ለተጠቀሰው ርእስ፤ መፅሃፈ አስቴርን በሙሉ እንድታነቡና እንድትረዱት እያሳሰብኩ፤ የዛሬ መርዶኪዮሶች፤ እንስት አንበሳ አስቴሮች አይዞአችሁ፡፡ ስለሃማና ጭፍሮቹ የግፍ ስራ ወሰን የለሽ በደል የሚመስሉአቸው እንዲያውም የሚበልጡአቸው የሃገራችን ገገሮችና እንደ ቡድንና እንደ ሕዝብ ተደራጅተው፣ የእግዚአብሄርን ህዝብ፣ በተዋህዶነት የጸናውን ወገን፣ ያጠፉ ዘንድ የዘመቱ የባህረ ነጋሽ ህዝቦች፣ የሃማና ወገኖች እጣ ፈንታ ተሰጥቶአቸዋል፡፡ የነሃማ እጣ ፈንታ የኢትዮጵያ ገገሮች ከነምንዝሮቻቸው፤ የባህረ ነጋሽ ህዝቦች በነገገሮቻቸው በብዙ እጥፍ ሆኖ የሚቀበሉት ነው፡፡

## 8/ሥ እውነተኞቹ ኢትዮጵያውያን የተዋህዶ ልጆችና መጪው እጣቸው፡፡

ቀንና ጊዜ ባለፈ ቁጥር ስጋ ለባሽ በመከራ ክብደት ይደክማል፡፡ ሃያል ጌታ ግን ለበረከቱ፣ ለምህረቱ ያተማቸውን ልጆቹን ያጸናል፡፡ የሰጠውን ( የገባውን) ቃል ኪዳን ያከብራል፡፡ ሰው በድካም ዝሎ የተገባለትን ተስፋ ሁሉ ይተዋል፡፡ በብርቱ ድካም ዝሎ ይወድቃል፡፡ ልዑል ግን ያኔ ድካሙን ሁሉ ከድኖ አድሶ በብርታት ሞልቶ በደስታ እንዲቦርቅ ያደርገዋል፡፡ የታመንበት የሰራዊት ጌታ ሁሌም እስከዘለአለሙ የታመነ ነው፡፡ የእግዚአብሄር ፍቅሩ፣ መታደጉ፣ በረከቱ ልቡን የሞላው ዳዊት እንዲሁ አለ፡፡

| | |
|---|---|
| አይኖቼን ወደ ተራራ አነሳሁ | እግዚአብሄርም በቀኝ እጅህ በኩል ይጋርድሃል |
| ረዳቴ ከወዴት ይምጣ | ፀሃይ በቀን አያቃጥልህም ጨረቃም በሌሊት |
| ረዳቴ ሰማይንና ምድርን ከሰራ | እግዚአብሄር ከክፉ ሁሉ ይጠብቅሃል |
| ከእግዚአብሄር ዘንድ ነው | ነፍስህንም ይጠብቃታል |
| እግርህን ለመናወጥ አይሰጠውም | ከዛሬ ጀምሮ እሰከ ዘለአለም |
| የሚጠበቅህ አይተኛም | እግዚአብሄር መውጣትህንና መግባትህን ይጠብቃል |

እነሆ እስራኤልን የሚጠብቅ አይተኛም አያንቀላፋምም

እግዚአብሄር ይጠብቅሃል

የዳዊት መዝሙር 120 / 121/

እግዚአብሄር ወገኖቹን እንደ አይን ብሌን ይጠብቃቸዋል፡፡ በማንኛውም የዲያበሎስ ዘዴ ይወድቁና ይጠፉ ዘንድ በፍፁም አይፈቅድም፡፡ ወገኔ የልዑል ልጅ፤ የቅዱሳን የከበሩት መላእክት ልጆች ብዙ ብተሰቃዩም ይድረሳችሁ የተገባችሁን ነጭ ልብስ ለበሳችሁ፡፡ አገራችን ኢትዮጵያ ልዑል ዙፋኑን የሚዘረጋባት፣ ልጆቹን እንቁዎቹን በዙፋኑ የሚያኖርባት፣ ድንግል ልጆችዋን በበረከቷ፣ በፍቅሯ የምታረሰርሳት፣ ኢትዮጵያ ቅዱሳን የከበሩት መላእክት ዙሪያዋን በእሳት አጥረው የሚጠብቁአት፣ የሚባርኳት ኢትዮጵያ፣ የፀናችው አንዲቷ የተዋህዶ እምነት እንደፀሃይ የምታበራባት ኢትዮጵያ ለልዑል የሰራዊት ጌታ ሌትም ቀንም ለክብሩ ለስሙ ምስጋና እንደጅረት የሚፈስባት ድንግልና ቅዱሳን የከበሩት መላእክት፣ ቅዱሳን ሰማእታት፣ ነቢያት፣ሐዋርያት፣ ስማቸው የሚከብርባት፣ የሚመሰገኑባት ኢትዮጵያ በክብሯ ጥግ ማንም የማይደርስባት የእግዚአብሄር የስስት ልጅ ናት፡፡

ከዚህ ድንቅ አገር የተፈጠራችሁ፣ ለአባታችሁ ለልዑል፣ ለእንቁዋ ለአገራችሁ ኢትዮጵያ ዋጋ ከፍላችሁ በጭንቅ እዚህ ለደረሳችሁ ወገኖቼ እንኳን ደስ ያላችሁ፡፡ በእምነት ድሉን ተቀዳጅታችኋልና!

የእሳቱ ብረቱ ግለት ተጭኖ ደረሶአልና በሁሉም ነገር ቁጥብ አስተዋይ ታጋሽ ሁኑ፡፡ ከአህዛብ ጋር፣ ከመናፍቃን ጋር፣ከካቶሊኮች ጋር፣ከተረት አምላኪዎች ጋር፣ ከአምልኮ ባእድ ተከታዮች ጋርና በግልፅ አይናችሁ በሚያየው ሰውን እየጎዱ ካሉ የስርአቱ አገልጋዮች ጋር በማይመች አካሄድ አትጠመዱ፡፡ ቅድመ ጥንቃቄ ይኑራችሁ አደጋው በአካባቢያችሁ ሲከሰት እናንተም በፈርኦንና በአገልጋዮቹ ላይ ሞት ሲወርድ ሙሴ በሩን ዘግቶ ሞትን ከወገኖቹ በምስጋና እንዳሳለፈ ሁሉ በራችሁን ዝጉ በበራችሁም ላይ የድንግልን ማህተም የቅዱሳን መላእክት ጥበቃና ፈጣሪያችሁን በማመስገን አሳልፉ፡፡ ሳታስቡት በውጪ የጥፋቱ ሃይል ሲመታና ሲጠርግ ስታዩ አትደንግጡ ምልክት አላችሁና እናንተን አይነካም፡፡ በጥቅሉ ዓለም በመልእክቶቹ እየተሰፈረች፣ እየተበጠረች እናም ወደማይቀረው አዘቅት እየወረደች ትገኛለች፡፡ ዛሬ እንደምናየው ዓለም በተለይም ባቢሎንና መሰሎችዋ ሃያላን የመጀመሪያው የእሳት ወንፊት ከመጀመሪያው መልእክት መውጣት ጀምሮ ስራውን እየሰራባቸው አናሳዎቹን አገሮችንም አብሮ እየፈጨ ይገኛል፡፡ ከእግር ጥፍር የተነሳው ውሃ ከፍታውን እየጨመረ ዛሬ እወገብ ላይ ደርሶአል፡፡ ዛሬ ደግሞ ይህ መልእክት መውጣት ጀምሮ ጉልበቱን ያልታየ ሃይልና ፍጥነቱም መቼም ያልተገመተ ሆኖ ይጨምራል፡፡ እስትንፋስን ለመዝጋት አፍንጫ ስርም ደርሶ ያጠናቅቃል፡፡ የግድ ካልተጠረገ የማይሰማው ይህ የዲያቢሎስ መንግሥትና ዓለም ተገድዶ የፊጢኝ ተወጥሮና አፍንጫው ተሰንጎ በኔ በምስኪኑ በባሪያው በኩል ልዑል የፈረደው ሙሉ ቃል በመልእክቶቹ እንደተገለጸው ሁሉም ተፈጻሚ ሁነው፤ በምድሪቱ በሙሉ አባታችን፣ አዳኛችን፣ ትምክህታችን፣ ሁለንተናችን የሆነው የልዑልና የሁሉ ፈጣሪ፤ አያል የሰራዊት ጌተ፤ ቅድስተ ቅዱሳን፤ ንጽህተ ንጹሃን እናታችን ድንግል፤ እጅግ የከበሩት አስራ ሁለቱም ሊቃነ መላእክት፤ በታላቅ ተጋድሎና ሰማእትነት ያለፉት ሰማእቱ ጊዮርጊስ፤ ሰማእቷ አርሴማ፤ እናም እጅግ የተከበሩት በሰማእትነትም በቅድስናም ያሉት ነቢያት፣ ሐዋርያት ሁሉም የተዋህዶ ጀግኖች የሚከብሩባት ዓለም ትጸናለች፡፡ እንደ ፀሃይም ታበራለች፡፡

## 9/ አውሮፓና በመልእክቶቹ አንጻር ያለፈችበት የመጀመሪያው እሳትና በሁለተኛው የእሳት ወንፊት የሚገጥማት እጣ

አውሮፓ፡- በመጀመሪያውም በሁለተኛውም በሶስተኛውም የአፈጻጸም መልእክቶች ሁሉ በሁሉም

አቅጣጫ የተመዘነችበትን፤ በውስጧም ያቀፈቻቸው አገሮች በሙሉ፤ እጣ ፈንታቸውን የተመዘኑበትንም ሁሉ እንዲያውቁት ተደርጓአል፡፡ ከዚህ ሁኔታ ጀምሮ እስከዚች ወቅት ድረስ በመጀመሪያው የእሳት ወንፊት እየተበጠሩ ይገኛሉ፡፡ አንዲት ተዋህዶን የማጥፋት ስራ የተጀመረና የተስፋፋባት፤ የጥፋት እምብርት አውሮፓ ናት፡፡ እንግሊዝ፣ ጣሊያን፣ ፈረንሳይ፣ ጀርመን፣ ፖርቱጋል፣ ስፔይን፣ ቤልጂየም፣ ደች/ሆላንድ/ በዋናነት ዲያቢሎስ ቀድሞ የነገሰባቸው በአውሮፓ ታላላቅ ተብለው የሚጠሩ ናቸው፡፡ አውሮፓ ዛሬ ወደ ራሺያ ጎራ ሄደው የነበሩትን ሰብስባ ከ28 በላይ አገሮችን የአውሮፓ ሕብረት በሚል ጥላ አሰባስባ የያዘች አህጉር ናት፡፡ ይህች ክፍለ አህጉር በሙሉ መልእክቶች ተመዝና ጥፋትና ፍርዷ ተገልጾላታል፡፡ ሙሉ መልእክቱ በእንግሊዝኛ ተዘጋጅቶ ባለው መንገድ ሁሉ መንግስታቶቹና፤ ሚዲያዎቹ፤ ዩኒቨርስቲዎቿ የጥፋቷ ቁንጮና የእምነቷ መሪ ካቶሊክ ከደረሳቸው ዋነኞቹ ናቸው፡፡ አልፎ አልፎ ግለሰቦችም ደርሷቸዋል፡፡ ለሕዝቡ እንዲገልጹ ቢነገራቸውም ማናቸውም ትንፍሽ አላሉም፡፡ ቢያንስ ጥፋቱ ከጀመረ በኋላ እንኳን ሕዝብ ከሚያምንበት መንገድ ላይ እንዳያርፍ እስከ አሁን አፍኖ ጥፋቱን እንዲጎነጭ እያደረጉት ይገኛሉ፡፡ አውሮፓ የመናፍቃን አገር እንደመሆንዋ በዲያቢሎስ አባቷ የተወደደች የምንዝርና፣ የክህደት፣ የፍልስፍና፣ የግብረሰዶም፣የጨካኞች፣ የዘረኞች፣ አገር ናት፡፡ በመሆኑም የተሰጣትን መልእክቶች የልዑል ፍርድን የያዙ መሆናቸውን እያወቀች ፍርዱን ወደ አፈጻጸም መሸጋገሩን ተረጋግጠ

ተነግሮአት በንቀትና በፌዝ አልፋዋለች፡፡ ባታምንበትና ዛሬም ባባትዋ በዲያቢሎስ ምክር ሳይንሳዊ መፍትሄ አገኝለታለሁ ብላ በመደናበር ላይ ትገኛለች፡፡ የመጀመሪያው የእሳት ወንፊት ምን እያከናወነ ይገኛል፡፡

-ኢኮኖሚዋ በታላቅ ቀውስ ተመቶባታል፤ የኢኮኖሚ እድገት መቀዝቀዝ፣ ግሽበት፣የበጀት ጉድለት፣ የገንዘብ ቀውስ፣ ስራ ፈትነት፣ የባንክና ኢንሹራንስ መውደቅ፣ መክሰርና ሌሎችም የኢኮኖሚ ህመሞች ወጥረው ይዘዋታል፡፡ የተፈጥሮ አደጋ፣ የሙቀት መጨመር፣ ጭጋግና በረዶ መከመር፣ አውሎ ነፋስ፣ ጎርፍና የመሬት ርደት መተዋታል፡፡ መሃበራዊ ቀውስ፣ ትራንስፓርት በአደጋ የተሞላ ሆኖአል፡፡ ብዙ የመደጋገፊያ ተቋማት ወድቀዋል፣ የሕዝብ አመጽ በብርቱ ተስፋፍቷል፣ አዳዲስ በሽታዎች ተከስተው ሕዝቡን አስጨንቀዋል፡፡ የሃይል አቅርቦት ፈተና ገጥሞታል፡፡ የእሳተ ጎሞራ ብናኝ በኢኮኖሚውም በአየር ትራንስፖርትም ቀውስ አስከትሏል፡፡ ሌሎችም ባይጎሉም ብዙ አደጋዎችና ጥፋቶች ተከስተዋል፡፡ ይህ ጅምር እርምጃ ወደሁለተኛው ምእራፍ ለመሸጋገር የዚህን አምስተኛ መልእክት እየተጠባበቀ ይገኛል፡፡ ከእግዚአብሄር ጋር የሚጣሉ ይደቃሉ፡፡ አውሮፓም ትእቢቷና የጥበብ ትምክህቷ ተሟጦ እስከሚረግፍ ድረስ ጠረጋው ይቀጥላል፡፡ የልዑልን ማንነት ፍርዱንና እኛም አገልጋይ ባሮች ምን እንደሆንን እየጠፋች የሺዎች ዘመናትን የጥበብና የቁሳቁስ አድጌአለሁ ክምርዋን ስታጣው ታውቀዋለች፡፡ ልዑል ማን እንደሁነ ያኔ ትረዳዋለች፡፡

-ሁለተኛው እሳት ወንፊት ከዚህ የሚከተለውን ያካተተና ሌሎችንም ጨምሮ ይመታል፡፡ ኢኮኖ ሚው አሁን ከሚተየው ቀውሱ በ7 ጊዜ 7 49 ጊዜ እጥፍ አድጎ ፍጹም ይደረማመሳል፡፡ መንግስታትም ባለ ሃብቱም ባጠቃላይ በሕዝብ አናት ላይ የተቀመጠ ሁሉ በእጁ የያዘውን ሁሉ ያጣል፡፡ ሕዝቡም ከጭንቁ የተነሳ አይኑ እያየው ቤቱን ንብረቱን ስለሚፈርስ፤ ሞትን አይፈራም፡፡ ስለሆነም በመንግስትም ሆነ በሚታመንበት ሃይል ላይ ዘምቶ መተላለቅ ይሰፍናል፡፡ ትራንስፓርት ይፈራርሳል፣ የጦር የጸጥታ የፖሊስ ሃይል የመሳሪያ ክምችትና ማምረቻው በተለያየ መንገድ ይወድማሉ፡፡ የፍትህ ስራ ይቆማል፡፡ ግሽበት፣ የበጀት ጉድለት፣ ማንም የማይፈታው ጥፋት ያስከትላል፡፡ ማንምም አይፈታውም፡፡ መሸቀጥ፣ መላክ፣ ማምጣት ፍጹም ይወድቃል ይቆማል፡፡ ማምረቻ ድርጅቶች ይከረቸማሉ፡፡ ማንም የማያንቀሳቅሳቸው ሆናሉ፡፡ እንደ ጃፓን አይነቱ የኒውክሌር ጥፋት በ49 እጥፍ ሆኖ በሚሊዮኖች ላይ ፍጹም ውድመትንና የሚሊዮኖችን ሞት ያስከትላል፡፡ ርእደ መሬት እስከአሁን ሆኖ በማይታወቅ ማግኒቲዩድ ተደጋግሞ ይከሰታል፡፡ የተከሰተበት ስፍራ ላይ ለምልክት የሚታይ አንዳችም የሰውም ሆነ የቁሳቁስ ወይም ፍርስራሽ ብናኝ አይገኝበትም፡፡ የተለያየ ስም የሰጣችኋቸው አውሎ ንፋሶች፣ ሱናሚ፣ ቶርኔዶዎች፣ ሃርኬኖች፣ ካትሪናውች ሌሎችም አሁን ከምናውቃቸው ጉልበታቸው በ49 እጥፍ ጉልበት አድገው ይመጣሉ፡፡ ጎርፎች ታይተው በማይታወቅ መጠን ይመጣሉ፡፡ ይጠርጋሉ፡፡ እሳቶች ከተነሱ የማይጠፉ፤ አውሎ ነፋስ አዘል ሆነው ብዙ ከተሞችን ያወድማሉ፡፡ መብረቆች በ49 እጥፍ ጉልበት ይመጣሉ፡፡ በተለይ ገገርዎችን፣ ባለ ሃብቶችን፣ የወታደር አለቆችን፣ የጸጥታ ኃላፊዎችን፣ የኒውክሊየር፣ የኬሚካል፣ የባኦሎጂካል ክምችቶችን፣ መፈብረኪያዎችን፣ የመረጃ መረቦችን፣ ሳተላይቶች / የተለያዩ የጥፋት ተልእኮ ያላቸውን/ ቋሚ ሳተላይቶችን ሁሉ ያወድማሉ፡፡ ግማሽ ሰው ግማሽ አውሬ ቅርጽ ያላቸው አውሬዎች ይፈሱባችኋል፡፡ ምንም ምሽግ አይከለክላቸውም፡፡ በምንም ዘዴ አይጠፉም፡፡ የካቶሊክ፣ የመናፍቅ፣ የተረት አምላኪዎች፣ ቀጥተኛ የዲያብሎስ አምላኪዎች በሙሉ በአውሬዎቹና በመባርቅት ትጠረጋላችሁ፡፡ ይህ ጥፋታችሁ እስትንፋስ እንኳን የማይሰጥ በመሆኑ የታዘዛችሁትን ለመፈጸም ስትወስኑ፤ ቀድማችሁ ለህዝባችሁ ከአንድ ጀምሮ እሰከ ሶስትና ይህንን አምስተኛውን መልእክት በሁሉም ቋንቋ በአለም አቀፍም በብሄራዊ የቴሌቭዥን፣ የሬዲዮ፣ የሳተላይት እንዲሁም በማናቸውም የመረጃ መረብ በጋዜጣ፣ በመጽሄት በየቀኑ ማስተላለፍ አለባቸው፡፡ ከዚህ በኋላ እጃችሁን በኢትዮጵያ ለሚጸናው የልዑል እግዚአብሄር መንግስት ዙፋን ላይ ለሚሆኑት ባሮቹ ስትሰጡ የታዘዛችሁትን ሁሉ ስትፈጽሙ ብቻ መፍትሄ የማግኛ መንገድ የከፈትላችኋል፡፡

ሁሉም መቅሰፍቶች በአውሮፓ ላይ ይፈሳሉ፣ በዮሐንስ ራዕይ 9 ፤ 1 – 11 እንዲሁም በዮሐንስ ራዕይ 9 ፤ 13 – 19 እኒህ በእናንተ ላይ ያርፋሉ፡፡

## 10/ ሰሜን አሜሪካ በመልእክቶቹ አንጻር በመጀመሪያው የእሳት ወንፊት ውስጥና በሁለተኛው የእሳት ወንፊት የሚገጥማት እጣ

ሰሜን አሜሪካ ሁላችንም እንደምናውቃት የዘመኑን የኃጢያት አዝመራ የምታመርትና እንደ እለት

ከእለት ምግብና ውኃ ለመላው ዓለም በግድም በውድም የምታከፋፍል የምታራግፍና በዲያቢሎስ ዋና አስፈጻሚነቷ የምትታወቅ አገር ናት፡፡ አሜሪካ / ባቢሎን / ይህንን ክፍለ አህጉር በዋናነት የያዘችው ሲሆን በስዋ ተዘዋዋሪ አገዛዝ ስር የሆኑ ካናዳና ሜክሲኮ በሰሜንና በደቡብ ዘብ የቆሙላት አገር ነች፡፡ አሜሪካ ሁሉንም የዓለም ሃገራት በቀጥታም ይሁን በተዘዋዋሪ በስሯ አድርጋለች ማለት ይቻላል፡፡ የአለም ሃያላን ከሚባሉት ውስጥ ራሽያ፣ ቻይና፣ እንግሊዝ፣ ፈረንሳይ በዋናነት አምስቱ ኃያላን ተብለው ይጠቀሳሉ፡፡ እነዚህ ኃያላን በራሳቸው በአሜሪካ የቀጥታም ይሁን የተዘዋዋሪ ተገዢ ናቸው፡፡ እንደ ምሳሌ ብናይ ራሽያ ትልቁ ገቢዋ የተፈጥሮ ጋዝ መሸጥ ነው፡፡ ሁሉም የሚረከቧት አውሮፓውያን ናቸው፡፡ የአውሮፓውያን ኢኮኖሚ ድግሞ በአሜሪካ ስር ነው፡፡በሙሉ መልእክት እደታዘዘው ቅጣቱ ሲሰነዘር የአለም ኢኮኖሚ፣ የባንክ፣ የሞርጌጅ ባንክ መውደቅ ሀ ብሎ የተነሳው ማፌና ማዩ የሚባል የአሜሪካን ሞርጌጅ ባንክ ሁለት ትሪሊዮን ከሰርኩ ብሎ ዘጋ፡፡ ባንኮቹም፣ ኢንሹራንሶቹም ሁሉም ከሰሩ፤ ወዲያው ተቀጣጥሎ አውሮፓ በክስረትና በቀውስ

ተጥለቀለቀ፡፡ ከዚህ ነጻ ያልነበረችው ራሽያ በመጀመሪያ 28 ቢሊዮን፣ ቀጥሎ መጠኑ ያልታወቀ የአሜሪካን ብር ድጎማ በማድረግ የደረሰባትን ቀውስ ለመቋቋም ታግላለች፡፡ ቻይና 500 ቢሊዮን በላይ የአሜሪካን ብር ክስረቷን ለማካካስ ኢኮኖሚዋን ደጉማለች፡፡ በአጠቃላይ ጌታቸው ባቢሎን ስትመታ የነሱም ጓዳ ዝብርቅርቁ ወጣ፡፡ አሜሪካ ከሞተች ሁሉም አብረው መሞታቸው ነው፡፡ ለቅሶአቸውም አብሮ ነው፡፡

የዮሐንስ ራዕይ ገጽ 18 በሙሉ አስተውለው ያንብቡ! የባቢሎን እጣ ፈንታ ይህ ነውና፡፡ ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን በሚለው የቀደሙት ሶስት መልእክቶች እንደተገለጸው ሁሉም የሰለጠንን፣ ያደግን፣ በማደግ ላይ ያለን ነን የሚሉ ሃገሮች በሙሉ፤ ግብይታቸው ሁሉ ከዚችው እንደ አምላካቸው ከሚያዩአት ባቢሎን /አሜሪካ/ ጋር ሲሆን እስዋ ከሌለች የሉም ማለት ይቻላል፡፡ የእኛው ሃገር ቡናዋን፣ ቆዳዋን፣ ሰሊጧን የሚገዛ የበለፀገ አገር ቢጠፋ የዛሬው እቅድ እድገት ተወነጨፍኩ ያዙኝ ልቀቁኝ ከወዴት ይመጣል፡፡ ስለዚሁም ነው ባቢሎን ያዘዘችው ዲሞክራሲ የሚሉት ከዲያቢሎስ ዋናው መስሪያ ቤት ወይም ዋናው ማዘዣ ጣቢያ የተዘጋጀ ኪኒን ሁሉም ሃገራት ለመውሰድ ግድ የሚሆንባቸው ፡፡ ከእሷ እጅ ቢሸሹ ከሌላኛው የእጅ አዙር እጇ መሸሽ አይቻልም ስለዚህም ነው በመጀመሪያ የእሳት ወንፊት ባቢሎን ስትመታ ሁሉም የአለም ሕዝብ መውሽልሸል የጀመረው፡፡ ዓለም በሙሉ ሊያውቅ የሚገባው ቢኖር አሁን ባለበት የጥፋት ጎዳና እንዲጓዝ ዘመናዊ መሣንዲስና አስተዳዳሪው የሆነችው፤ እንደ አምላኩም የሚያየት ባቢሎን ናት፡፡ የምንዝርናው፣ የግብረሶዶሙ፣ የነጣቂው፣ የዘራፊው፣ የመናፍቁ፣ የካቶሊኩ፣ የተረት አምላኪው፣ የጣኦት አምላኪው በአለም ሁሉ ያለ ገገር ሁሉ እንደ አምላኩና እንደ ቤተክርስቲያን የሚሳለማት ይህቺው ባቢሎን ናት፡፡

የመጀመሪያውን እሳት አይታዋለች ዛሬም በዛው ውስጥ እቋቋማለሁ ብላ እየዳከረች ነው፡፡ ረግረግ ውስጥ እንደጠለቀ ሰው፤ በዚህ ርእስ ስለሷ በመዘርዘር ጊዜ አናጠፋም የቀደሙት 3 መልእክቶች ፍርዷንም አፈጻጸሙን ስለነገሩን እነሱን ማስተያየት በቂ ነው፡፡ ይህ መልእክት ትኩረት የሚያደርገው ስለሁለተኛው የእሳት ወንፊት መመታቷን ለመግለጽ ነው፡፡ አሜሪካ /ባቢሎን/ መልእክቶች ሁሉ፤ ለመንግስቷ፣ ለሚዲያዎቿ ደርሷል፡፡ ስላልሰማች እንደፍርዱ የመጀመሪያውን የእሳት ወንፊት እየማሰነችበት ሲሆን ሁለተኛውን የእሳት ወንፊት እንድትቀበለው ከዚህ ቀጥሎ በተዘረዘረው መልኩ በልዑል ውሳኔ በኔ በባሪያው በኩል ታዟል፡፡

## ትዕዛዞች፤

በዚች ሃገርና፤ አብረዋት ባሉ ተዋሳኝ አገሮች ላይ፤ በሙሉ አሁን እየደረሰ ያለው የኢኮኖሚ ቀውስ ማለትም ግሽበት፣ ሪሴሽን፣ የበጀት ጉድለት፣ የእዳ ቀውስ፣ የባንክ የኢንሹራንስና የሞርጌጅ ባንክ ቀውስ፣ የመሸቃቀጫ ገበያ / ስቶክ ማርኬት/ ቀውስ፣ የምግብ እጦት፣ የስራ ማጣት፣ የጤና ችግር፣ የትራንስፖርት ቀውስ፣ የትምህርት ቀውስ ባጠቃላይ የኢኮኖሚው አካልና ህይወት በሙሉ፤ እሰከአሁን ከተመታው መጠንና ስፋት ጥልቀት በ49 እጥፍ ተባዝቶ እንዲመታና እንዲያፈራርስ በልዑል ተወስኖበታል፡፡

- የተፈጥሮ አደጋዎች፣ ርእደ መሬት፣ የዱር እሳት፣ ቶርኔዶ፣ ካተሪና፣ ሃሪከን፣በረዶ፣ ሙቀት፣ ሱናሚ፣ ከባድ ዝናብ፣ ሌሎችም የተፈጥሮ አደጋዎች በሙሉ፣ በተጣመረም በብዛትም ሆነውና ተቀናጅተው በ49 እጥፍ ጉልበት አድገው እንዲያወድሙ፡፡ ትራንስፖርት ንግድ የመሳሰለው በሙሉ እንዲወድቅ ታዟል፡፡ መባርቅት፣ ቀድመው ከሚታወቁበት ጉልበታቸው በላይ በ49 እጥፍ ጉልበት ማናቸውንም የኒውክሊየር፣ የባዮሎጂካል፣ የኬሚካል ክምችትና ማምረቻ ሁሉ ለሰው ጥፋት የተሰናዱ ማናቸውም የጦር ክምችቶች፤ ከነተገልጋዩ፤ የነዚህ አዛዥ ናዛዥ በሙሉ ገገርውና የገገርው እጅና እግሮች በሙሉ የትም ይደበቁ የትም ፈልገው እንዲያወድሙ ታዘዋል፡፡ በተለይ ባቢሎን እንደ ትልቅ ጉልበቷ የምትመካባቸው በአለም ያከማቸቻቸው በየበስ ያሉ የጥፋት መሳሪያዎች በሙሉ በነዚሁ መባርቅት ይወድማሉ፡፡ በውቅያኖስ ላይ የተሰማሩ የጦር የጥፋት መርከቦች በታላላቅ ማዕበልና መባርቅት እየተጠረጉ በውቅያኖስ ውስጥ ሰምጠው ይቀራሉ፡፡ አለምን እንዲሰልሉ በታጠቁት መሳሪያ ከህዋ ላይ ሆነው እንዲያጠቁ የተዘጋጁ ሳተላይቶቻችሁ ሁሉ እንዲወድሙ ታዟል፡፡ ባቢሎን እወቂ በእጇ አለኝ ይመክትልኛል፤ ይታደገኛል ያልሽው ማናቸውም መሳሪያም ይሁኑ ሌላ ካለበት እዚያው እንዲወድም ታዟል፡፡ የትእቢትሽ ምንጭና ምልክቶች ሁሉ እንደ ቋሚ ሳተላይት እስቴሽን አይነቱ እንዲወድም ታዞበታል፡፡

እጅግ አስፈሪ የሆኑ የተለያዩ ሁለት አይነት አካል የሚይዙ አውሬዎች ምልክት አልባ ይሆኑ ሰዎችን ይቆረጣጥማሉ፡፡ ይበላሉ፡፡ በተለይ በአገዛዛችሁ ዋልታና ማገር ሆነው አገዛዛችሁን ያቆሙና ባለሃብቶች ነን የሚሉ፤ መናፍቃኖቻችሁ፤ ሁሉም የዲያቢሎስ እምነቶቻችሁ ሁሉ ከላይ በተዘረዘሩት መቅሰፍቶች ይጠረጋሉ፡፡

ከላይ የታዘዙት መቅሰፍቶች በሙሉ ሰው እስከዛሬ ባላየው ባልሰማው ጉልበት ይመጣሉ፡፡ በዚህ ጠረጋ መሰረታችን፣ እድገታችን፣ ብልጽግናችን፣ ጥበባችን የሚታይባቸው ናቸው፡፡ የምትሏቸው ከተሞች ተጠርገው ይጠፋሉ፡፡ ለሌላው አገር ጦርነትን ትልካላችሁና ይኸው ጦርነት በገባችሁበት ስፍራ ሁሉ ለናንተው መውደሚያ ይሆናል፡፡ ለሌው ሃገርም ስለራሳችሁ ሁሉን አቀፍ ዲያቢሎሳዊ አመጻችሁን በስልጣናችሁ ተመክታችሁ፤ ለምታደረጁና ለምትደግፉ፤ በላያችሁ ላይ ሞትን የሚያስመኝ በርባሪ እሳት ታዞላችኋል፡፡

ማናቸውም የባቢሎንም ሆነ የካናዳ፣ የሜክሲኮ ሌሎችም ድንበረተኞች ዜጋም ይሁን የሌላ በተዋህዶ እምነት ውስጥ በመምሰልና በመለባበስ ካሉና ከልዑል የታዘዘው ምልክት ካልተደረገባቸውም በጭንቅና በውድመት ውስጥ ያመልጡ ዘንድ ልዑል ከወሰነላቸው በቀር፤ የተቀረው ከላይ የተዘረዘሩት ቅጣቶች ሰለባ ይሆናል፡፡ ይጠረጋል፡፡ ባቢሎንም ተረት ሆና ትቀራለች፡፡ እለዚህ ከላይ የተዘረዘሩት ሁሉ መልእክቱ ከወጣ ጊዜ ጀምሮ በማናቸውም ያልታሰበ ጊዜና ሁኔታ ጠረጋቸውን እንዲጀምሩ ታዘዋል፡፡ እስትንፋስ የሚገኘው፤ የታዘዛችሁትንና አድርጉ የተባላችሁትን ለመፈጸም እጃችሁን በኢትዮጵያ ለምትጸናው የልዑል መንግስትና ለተዋህዶ እምነት አምናችሁበት ስታስረክቡ ብቻ ነው፡፡ የሚወርድባችሁ መቅሰፍት የሚቆመው ከዚህ ከኢትየዮጵያ ከጸናው መንግስት ከልዑል ባሮች ታምኖበት ሲወሰን ብቻ ነው፡፡ ለመንበረከካችሁና ለመወሰናችሁ ቅድመ ምልክት ይሆን ዘንድ ቀድሞ የወጣውን ሙሉ መልእክትና ይህን አምስተኛውን መልእክት በሁሉም ሚዲያና ፕሬሶቻችሁ እንዲሁም በማናቸውም መረጃ መረቦቻችሁ በቀን ቢያንስ 2 ጊዜ ማግለጽ አለባችሁ፡፡ በመልእክቱ ላይ አንዳች መጨመር ወይም መቀነስ አይቻልም፡፡

## 11 / ኤሽያ በመልእክቶቹ አንጻር ያለፈችበት የመጀመሪያው የእሳት ወንወፊትና በአሁኑ የ2ኛው ዙር የእሳት ወንፊት የሚገጥማት እጣዋ

ኤሽያ አጅግ የከፋ አመጽ፣ ክህደት፣ ጣኦት ማምለክ፣ ምንዝርና፣ ግብረሰዶም፣ የተለያዩ የቀጥታ ጥንቆላዎች፣ መተብትቦች፣ የተንሰራፋባት አገር ነች፡፡ ጥቂት የተዋህዶ እምነት ተከታዮች በህንድ፣ በአርሜኒያ ከሚኖሩ በቀር፤ ሌላው ሁሉ በምንፍቅናና በካቶሊክ፣ በተረት/እስልምና/ እምነት የተተበተበ ነው፡፡ ሰፊውን የአለም ሕዝብ ቁጥር የያዘችው ይህች ኤሽያ ናት/ ወደ 3 ቢሊዮን የሚጠጋ ሕዝብ ይዛለች፡፡ ቻይና ወደ 1.3 ቢሊዮን፣ ሕንድ ወደ 1.1 ቢሊዮን ሕዝብ ሌሎች ሲደማመሩ ከ6መቶ ሚሊዮን በላይ ሕዝብ ሲሆኑ በድምሩ ከ 3 ቢሊዮን በለይ ሕዝብ አላት ፡፡

በኤሽያ ጎልተው የታዩት አገሮች እንደ ምሳሌ ወስደን ብናይ ቻይና ፡- የዚህ አህጉር ዋናው አካል ሆና እናገኛታለን፡፡ ቻይና 1.3 ቢሊዮን ሕዝብ ይዛ አንድም የተውህዶ እምነት ተከታይ የለባትም፡፡ የአለምን አንድ ስድስተኛ ሕዝብ የሸፈነች አገር ምንም የተዋህዶ እምነት ተከታይ የሌለባት ከሆነች ምንም ሰው አይድንም ማለት ይሆን ? አይደለም በተዋህዶ እምነት አምኖ ሆኖ መገኘት ከምንም በላይ ሲሆን፤ ሁለተኛው መስፈረያ ደግሞ የዋህ፣ ቅን፣ ትሁት በምንም መልኩ ይሁን ፈጣሪውን የሚፈራ የልዑልን ምርጫ ማንም አያውቀውምና ምልክት ያለው ሁሉ ይድናል፡፡ ነገር ግን ከዚች አገር ሰው ተረፈ ለማለት በፍጹም አይቻልም፡፡ ምክንያቱም የተለያዩ ጣኦታትንና ኮንፌሺየስና መሰሎቹ የፈጠሩት እንደ ታኦይዝም፣ ሺንንቶይዝም የመሳሰሉ እምነቶችን ሲያምኑ፣ድራጎንን ከምንም በላይ የሚያምኑበት ምልክታቸው ነው፡፡ ህንድ፤- ይህችም አገር በህዝብ ቁጥሯ 1..1 ቢሊየን የደረሰች ናት፡፡ በዚህ አገር አሉ ሳይሆን የሉም የሚያስብል ቁጥር ያላቸው ዘመናቸውን ሁሉ በታላቅ የዲያቢሎስ ውጊያ የከደኑ የተዋህዶ እምነት ተከታዮች ያሉባት ስትሆን የተቀረው በከብት፣ በእባብ፣ከሽክላ በተሰራ ጣኦት፣ በጥቅሉ ቡዲሂዝም፣ ሲኪዝም በመሳሰሉ የሚያምንና ሁለት ሶስተኛውን ህዝብ ይይዛል፡፡ ሌላው ደግሞ በተረት (እስልምና) የሚያምን ሲሆን ከዚህ የተረፈው በተለያዩ እምነቶች ውስጥ የወደቀ ነው፡፡

የማናቸውንም አገሮችና ክፍለ አህጉሮች እጣ ፈንታና ዝርዝር ሁኔታዎችን ለማወቅም ሆነ ፍርዳቸውን (ሽክማቸውን) ለማወቅ ሙሉውን መልእክት (ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን) የሚለውን ማንበብ መሰረቱን ለመረዳት ያስችላል፡፡

ሌሎች አገሮች እንደ ጃፓን፣ ራሺያ፣ ኢንዶኔዥያ፣ ባንግላዴሽ፣ ፓኪስታን፣ ታይላንድ፣ ካምቦዲያ፣ ቬይትናም፣ ኔፓል፣ በርማ፣ሲሪላንካ፣ፊሊፒንስ፣ ታጂክስታን፣ካዛኪስታን፣ዩዝቬክስታን፣ ቱርኪሚስታን፣ አርመንያን፣ ኮርያዎች፣ ሞንጎሊያና ሌሎችን ያቀፈችው ኢሺያ እጅግ ሰፊ አህጉር ናት፡፡

እነዚህና ሌሎችም አገሮች በተለያየ መንገድ መልእክቱ እንዲደርሳቸው ተደርጎአል፡፡ ነገር ግን ማናቸውም ቦታ አልሰጡትም፡፡ መንግስቶቻቸውም ሆነ ሚዲያዎቻቸው ከምእራባውያን የተገኙ አይደሉም፡፡ ምንም ለህዝቡ አላዳረሱም፡፡ ይህች አህጉር በመጀመሪያው የእሳት ወንፊት እየተበጠረች የምትገኝ ሲሆን ምንም አይነት የመጸጸታ ምልክት የማይታይባት ክ/አህጉር ነች፡፡ የመሬት ነውጥ፣ ሱናሚ፣ ረሃብ፣ የኒውክሌር ቀውስ፣ ከፍተኛ ጎርፍና የመሬት መንሸራተት፣ ስራ ማጣት በአጠቃላይ ብዙ አይነት ማህበራዊ፣ ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚያዊ ቀውሶች እያመሷት ቢገኙም ምንም አይነት ወደ ፈጣሪ የመመለስ ምልክት አላሳየችምና፤ ቀጣዩ የሁለተኛው የእሳት ወንፊት ይረከባት ዘንድ በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል ከዚህ በታች የሚዘረዘረው የእሳትም መጥረጊያ ታዟል፡፡

### ትእዛዞች፡-

- ርእደ መሬት፣ ሱናሚ፣ ቶርኔዶ፣ ከባድ ጎርፍ፣ ታይፉን፣ ካተሪና፣ ሃሪኬን የመሳሰሉት የተፈጥሮ አደጋዎች በ49 እጥፍ ጉልበት ሃይልና ፍጥነት ጨምረው ያልተዳረሰውን ክልል አዳርሰው ይጠርጉ ዘንድ ታዘዋል፡፡
- የኢኮኖሚ ቀውስ፣ የበጀት ጉድለት፣ ግሽበት፣ ሪሴሽን፣ የገንዘብ ቀውስ፣ የወጪና የገቢ ንግድ ቀውስ፣ የኢንዱስትሪ ቀውስ፣ የማህበራዊ ቀውስ፣ የፖለቲካ ቀውስ፣ ረሃብ፣ ስራ ማጣት፣ በሽታ በሙሉ በ49 እጥፍ ተባዝተው እንዲበታትነአችሁ ታዘዋል፡፡ ትራንስፖርት ባልታየ ሁኔታ የአደጋ ምንጭ ሆኖአል፡፡
- መባርቅት በ49 እጥፍ ጉልበት ሁሉንም ክፍለ አህጉራችሁን ሌሊትም ቀንም ይመታሉ፡፡ ተደብቆ ተሸሽጎ ማምለጥ በፍጹም አይቻልም፡፡ በተለይ በአገዛዙም፣ በእምነቱም፣ በጥበቡም፣ እንመራለን የሚሉት የመባርቅት ሰለባ ይሆናሉ በመባርቅቱም ይጠረጉ ዘንድም ታዞአል፡፡ አውሬዎች የሰውና የአውሬ ቅርጽ ያላቸው በእግዚአብሄር የተሰጠውን ምልክት በግንባራቸው የሌለውን ይበላሉ፡፡ ምንም አይነት መሳሪያ ወይም የሰው ዘዴ አያጠፈቸውም ከእርምጃቸውም አይገታቸውም፡፡ በክፍለ አህጉርዋ የተካተቱ አገሮች በሙሉ በቅጣቱ ይሸፈናሉ፡፡
- የሁሉንም የኤሽያ ሃገሮች ቀድሞ ከወጣው ሙሉ መልእክቶች/ ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን 1፤ 2፤ 3፤/ ዝርዝረ እጣ ፈንታቸው ማንኛውም መልእክቱ የደረሰው ፈልጎ ሊያነበው ይገባል፡፡ አሁን የሚመጣውን እሳት የትኛውም የሰው ጉልበት፣ ጥበብ ሊያቆመው አይችልም፡፡ የሚሞክሩ ካሉ ይዞ ከመጣው የ49 እጥፍ ጉልበት የኸውም 49 እጥፍ ጉልበት እንደገና በ7 ተባዝቶ 343 እጥፍ ይሆናል፡፡ የሚመጣውንም መገመት ያስቸግራል፡፡ እስትንፋስ ማግኘት የሚቻለው እንዴት ነው ለሚለው በመጀመሪያ ሙሉውን መልእክት፣ ይህንንም መልእክት 5 ጨምሮ በሁሉም ፕሬስና ሚዲያዎች፤ በመረጃ መረቦች ሁሉ በመግለጽ በቀን ሁለት ጊዜ በሬዲዮና በቴሌቪዥን እንዲለቀቅ ማድረግ፡፡ ከዚያ በኋላ እጅን ለመስጠት መዘጋጀትና የታዘዙትን ሁሉ ፈጽሞ እጅን መስጠት፡፡ እጅ የሚሰጠው፤ በኢትዮጵያ ለሚጸናው የሰራዊት ጌታ እግዚአብሄር መንግስት ሲሆን በዚያ በዙፋኑ ላይ ያሉት የልዑል ባሮች ትእዛዝ ሲተላለፍ፣ ሰላምም፣ እውነተኛይቱ የተዋህዶ እምነት፣ በረከቱም ከቁጣው እሳት ለተረፉት ይሰጣቸዋል፡፡ የተረፉት ህዝቦች ሁሉ ተጠርገው በሄዱት ወገኖቻቸው እድል ያዝናሉ፡፡ ከላይ የተዘረዘሩት ቅጣቶች ሌሎችንም ቅጣቶች አካቶ ሁለተኛው የእሳት ወንፊት እንዲጠርጋቸው በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል ታዟል፡፡
-

## 12/ አውስትራሊያ፡-

ይህች አህጉር የተለያዩ እንደ ሃገር የቆሙ ደሴቶችን የያዘች ሲሆን የመጀመሪው የእሳት ወንፊት በሚገባ እየመታት ይገኛል፡፡ የሶዶሞች፣ የነፍሰ ገዳዮች ቀዳሚ መስፈሪያም ነች፡፡ቀደምት ነዋሪዎችም እንደ አሜሪካ ጠርጋ ያጠፋችና ምድራቸውን ወርሳ ዛሬም እያጠፋቻቸው ያለች የእንግሊዝና የአይርሽ ዘሮች በሃይል የሰፈሩባት አህጉር ነች፡፡ ስለዚህ ይህች ክ/አህጉር በሙሉ መልእክት / ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን 1፤ 2፤ 3፤ / ማየት ይቻላል፡፡ ይህች አህጉር ሁሉም አመጾች የሚካሄዱባት ናት፡፡ ግብረሰዶም፣ አመንዝሪው፣ ነፍሰ ገዳዩ፣ ዘራፊው፣ ዘረኛው፣ የሞሉባት ሃገርም ነች፡፡ መናፍቃኑ፣ ካቶሊኩ፣ እስላሙ፣ በዋናነት ያሉባት ሲሆን ፖሊሲዋም፣ ኢኮኖሚዋም ከምእራቡ አለም ጋር አንድና ተመሳሳይ ነው፡፡ የመጀመሪያው እሳት ምን እንደ ሆነ በሚገባ አይታዋለች፡፡ ይህ በዚህ እንዳለ ሆኖ አልተጸጸደተችምና! ለሕዝብዋም የደረሳትን ሙሉ መልእክት በአግባቡ አላደረሰችምና፤ ፌዘኛና እንደወገኖቿ አውሮፓውያን አሜሪካውያን፣ ኤሽያውያን በትእቢት እንደ ተሞላች ስለሆነ፤ ከዚህ በታች የተዘረዘረው ሁለተኛው የእሳት ወንፊት በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል እንዲፈጸምባት የኸው ታዞአል፡፡

## ትእዛዞች፡-

ለሰሜን አሜሪካ፣ ለአውሮፓ፣ ለኤሽያ የታዘዙት ሁለተኛ ደረጃ የእሳት ወንፊቶች በሙሉ፣ አንዳችም ሳየቀሩ፣ ተፈጻሚ እንዲሆኑባት ስለተወሰነ፣ የነዚህን አህጉራት የቅጣት ትእዛዝ ሲመለከቱ ቅጣቶቹ በሙሉ በአውስትራሊያና በዙሪያዋ ባሉ ደሴቶች ላይ ተፈጻሚ እንዲሆን በልዑል ታዟል፡፡ በዚህ የሁለተኛው እሳት የምትበጠረው አውስትራሊያ እስትንፋስ ለማግኘት ከወሰነች እጇን በኢትዮጵያ በሚጸናው የሰራዊት ጌታ በሚነግስበት ዙፋኑ ላይ ለሚቀመጡት ባሮቹ እጇን መስጠት አለባት፡፡ ከዚህ ቀድማ ሙሉውን መልእክትና ይህንንም አምስተኛ መልእክት ባላት መገናኛ ብዙሃን ሁሉ፤ ለህዝቧም ሆነ ለመላው አለም ህዝብ መግለጽ አለባት፡፡

## 13/ ደቡብ አሜሪካንና የካሬቢያን ደሴቶች በመጀመሪያው የእሳት ወንፊትና እንዲሁም በቀጣዩ 2ኛ ደረጃ የእሳት ወንፊት የሚገጥማቸው እጣ

ደቡብ አሜሪካ ከማንም በላይ ግብረሰዶሙ ፤ግልጽና ምንም መሸፈኛ የሌለው ፣ ምንዝርና ፣ ከእጽ ጋር የተያያዘ ፍጅት የሞላባት፣ የወንጀለኞች፣ የነፍሰ ገዳዮች፣ የዘራፊዎች፣ ጉበኞች፣ የጨካኝ ገዢዎች፣ አገር ስትሆን፣ ምንፍቅና፣ በተለይ ካቶሊክና እስላሙም በስፋት የሞሉባት አገር ናት፡፡ ጥንቆላው፣ ትብታቡ ሁሉ በስፋት ተንሰራፍቶባታል፡፡ ይህች አህጉር በመጀመሪያው የእሳት

ወንፊት ተደጋጋሚ በትር ቢመታትም በተገለጸላት በተሰጣት መልእክት ያላመነችበትና በንቀትም የዘለለችው ሆናለች፡፡ በመጀመሪያው የእሳት ወንፊት ካየቻቸው እንደ ምሳሌ ብናነሳ ሃይቲ በርእደ መሬት ከግማሽ ሚሊዮን ሕዝብ በላይ አታለች ያኔ የፈረረሰ ኑሮና መኖሪያ ማንም ሊመልሰው አልቻለም፡፡ ቺሊ እንዲሁ በከባድ ርእደ መሬት ስትመታ ብራዚል የታላላቅ ጎርፍና የመሬት መደርመስ ተመታለች፡፡ ሌሎቹም የአህጉሪቱ አገሮች በብዙ መልኩ የተመቱ ሲሆን አለምን የመታው የኢኮኖሚ ቀውስም የህቺን አህጉር እየመታት ይገኛል፡፡ የህቺም አህጉር በውስጧ ያቀፈቻቸውን አገሮች በሙሉ በመጀመሪያው እሳት እንደዳረገች ሁሉ፤ የመጸጸት ምልክት ያልታየባት ሆናለችና፤ ሁለተኛው የእሳት ወንፊት ይጠርጋት ዘንድ በልዑል የተፈቀደና የታዘዘ ሲሆን ትእዛዙም በኔ በባሪያው በኩል ከዚህ በታች በሰፈረው መልኩ ታዟል፡፡

## ትእዛዞች፡-

ይህች ክ/አህጉር ያቀፈቻቸው አገሮች በሙሉ ከላይ ለሰሜን አሜሪካ፣ ለአውሮፓ፣ ለኤሽያ የታዘዙት ቅጣቶች በሙሉ በዚችው የደቡብ አሜሪካና ካሪቢያን አገሮች ላይ ተፈጻሚ እንዲሆን ታዟል፡፡

በመከራው ውስጥ እስትንፋስ የሚገኘው ለመላው ሕዝቦቿ ከዚህ በፊት የወጡትን ሙሉ መልእክቶች ማለትም / ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን 1፤ 2፤ 3፤/ የሚለውንና እንዲሁም ይህን ቁጥር አምስት መልእክት በሁሉም የመገናኛ ብዙሃንና በሁሉም ቋንቋ ለመላው ሃገሮች ስትገልጽና እጇንም በኢትዮጵያ ለሚጸናው የሰራዊት ጌታ መንግስትና በዙፋኑ ለሚሰየሙት ባሮቹ ስትሰጥ ብቻ ነው፡፡ የልዑል ባሮች የሰላም ትእዛዝ ሲያስተላልፉም ነው እጃቸውን ለሰጡ ሁሉ ሰላማዊ የሚመለሰው፡፡

## 14/ አፍሪካ፡-

አፍሪካ ይህች ክ/አህጉር በድህነቷ የምትታወቅና እጅግ ወደኋላ የቀረች ተብላ የተፈረጀችም፣ የሆነችም ክ/አህጉር ናት፡፡ይህች አህጉር በድህነትም፣ በረሃብም፣ በሁሉም ሰው አደኩበት በሚለው መንገድ ሁሉ ወደኋላ የቀረች በጌቶቿ አባባል ወደኋላ የቀረች፣ ያላደገች አህጉር ብለው ይጠርዋታል፡፡ የሰው እይታ፣ ሰው እንደ ሰው ሆኖ የመኖሩ መለኪያው እንደ ሰው እንዲሁም በአለም ውስጥ ሲኖር በአንድም በሌላም የሁከት፣ የጥበብ፣ ጎዳና፣ የሞያና የክህሎት ባለቤት እንዲሆን ይህ እውቀቱና ሞያው ለሰው የማያባራ የቁስና በዚች አለም ተመችቶት የመኖር መንገድ እንዲያገለግል ማድረግ ሲሆን፤ ከዚህም በተጨማሪ እንዳሻው ያለምንም ገደብ ስጋው ደስ ያለውን ሁሉ እንዲያደርግ የሚገፋ ነው፡፡ በዚህ ጉዞ ነጥቀው፣ ዘርፈው፣ ሆነ ገገር ሆነው በተለያዩ መንገድ በሕዝቡ አናት ላይ የመቀመጥ እድል ከገጠማቸው ደግሞ ይህንኑ የበላይነታቸውን እውን ለማድረግ የሚደክሙባት አለም ናት፡፡  አለም በዚህ ጉዞና የኑሮ መሰናዶዋ የስጋው ብርቱ ፣ የዲያቢሎስ ታዛዥ ብርቱ፣ ማናቸውንም አመጽና ግፍ የሚጠቀም የጭለማው ገገር ያኖረው ህግ ተጠቃሚ ዛሬም ትናንትም ለሺዎች አመታትም በእንዲህ መልክ ብዙዎች የኖሩባት አለም ውስጥ በዚህ ውጣ ውረድ እንዳያልቁ ላጨራረሱም ሳይቀናት የቀረች አፍሪካ ብቻ ናት፡፡ የመጀመሪያው የአለም ሩጫዋ አንደኛ ነበረች፤ በቅንነት ሩጨዋ ማለት ነው፡፡ ኋላ ግን ደግሞ ዲያቢሎስ በአለም ሲነግስበት ዛሬ ወደ ደረሰችበት ውድቀት ደረሰች፡፡ በዲያቢሎስ መለኪያ ታማኝ አገልጋዮችን ማግኘት ዋንኛ ስራው ነበር፡፡ ስለሆነም ለሱ ታምነው የተገኙት ዛሬ ገዢፈው የምናያቸው ሆነዋል፡፡ ለአፍሪካ ዋንኛው የመውደቅና የመድከም ምክንያት እውቀት ማጣት ወይም ለመስራት፣ ለመጠበብ አለመቻል አልነበረም፡፡   ነገር ግን በአፍሪካ ከመሰረቱ ምድርና ሰማይን በዘረጋው በፈጠረው ዛሬ ምድሪቱን በጥፋት ጎዳና እየነዳ ያለውን ዲያቢሎስንም የፈጠረው በትእቢቱ፣ በንግዱ፣ ከክብሩ ወደ ምድር ወድቆ ለሰውም ፈተና እንዲሆን ያደረገው አብ ወልድ መንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክን አምላኬ ብላ በትእዛዙ ተደስታ እንደ ሃገር የምትኖር ሃገረ እግዚአብሄር ለስሙ፣ ለክብሩ አስቀረ፤ ይህች አገር ደግሞ ያለችው በአፍሪካ ውስጥ ነው፡፡  የህች ሃገር ደግሞ እስከዛሬ የዲያቢሎስን የጨለማ ህግ የሚያፈርስ፤ የፈጠራትን አምላኳን ህግ የሚያጸና እምነት፣ የተዋህዶ እምነት አጽንታ በመያዟ በዋናነት እራሷ በቀጣይ እሷ ያለችበት አህጉር በሁሉም ነገር እንድትመታ ተደረገች፡፡

አለም ለረሃብ፣ ለችግር እንደ ምሳሌ እንዲቆጥራት የተደረገችም ናት፡ የአህጉሪቱ ሌሎች አገሮች ዘግይተው አሸከርነታቸውን ቢቀበሉም ለረጅም ጊዜ ሳትደፈር የቆየች አገር ኢትዮጵያ ብቻ ናት፡፡ ስለዚህ ዛሬ የምናየው የጥፋት ሁሉ ቀስት በዚችው ምስኪን አገራችን ላይ ሳያቋርጥ የሚዘንበው፡፡

ይህ ሁሉ ሆኖ አፍሪካም የዲየያቢሎስ የጨለማ ስራ ሰለባ ሆናለች፡፡  ምንዝርናው፣ ግብረሰዶሙ፣ ዘረፋው፣ ነፍስ ግድያው፣ ውሸቱ፣ ጨካኝ አረመኔ ገዥዎቹ የሰፈነባት ምድር ናት፡፡ የሁሉንም የዲያቢሎስ ስራዎች እንደ ትክክልና እንደ መሰልጠን በማየት አብዛኛው የአፍሪካ ሕዝብ በዚሁ የጥፋት ጎዳና እየጓዘ ይገኛል፡፡  ይህችውም አህጉር አገራችንን ጨምሮ አመጸኞች በልዑል ሕግ ላይ የመጹና የካዱ ሕዝቦች የሞሉባትና የሸፈኑአት ናት፡፡

ኢትዮጵያ ለምን ተወደደች የሚለው የብዙው የአለም ቅን ጥያቄ አቅራቢ መልስ የሚሻ ነው፡፡  ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን በሚለው መልእክቶች 1፤ 2፤ 3፤ በሚገባ ተብራርቶአልና፡፡  እንደ ተጨማሪ ዝርዝር ማገናዘቢያ ልታዩት ትችላላችሁ፡፡ ኢትዮጵያ የተወደደችው

ዛሬ ባለነው ወገኖች ስራ አይደለም ነገር ግን የቀደሙ አባቶቻችን በከፈሉት ዋጋ እንደ እግዚአብሄር ፈቃድና ትእዛዝ ተደስተውበት፣ አምነውበት፣ወድደውት ለልጅ ልጆቻቸውም እንደ ግል ሀብታቸው አውርሰውት ስለኖሩበት ነው፡፡ ዓለም ሲንቅ ፣ የልዑልን ህግና ፈቃድ ሲያነቋሽሽ አያቶቻችን ግን የኖሩበትን የሚከፈለውን ዋጋ ከፈሉበት፤ ተደሰቱበት፡፡ማንም ያላገኘውን ክብር አፈሱበት፡፡ ዛሬ ዓለም እንግዳ ቢሆንበት አይደንቅም ምክንያቱም አያቶቹ ቅድመ አያቶቹ የወረሱትን የዲያብሎስ መንገድ ወርሷልና፡፡ እግዚአብሄርንም ሊወቅስ አይቻለውም፤ ምርጫው ነውና፡፡ በየዘመኑ ሁሉ ከጨለማና ከብርሃን እንዲመርጥ እድል ተሰጥቶታል፡፡ ልዑል ዋጋ ከፍሎ ና ወደ እኔ ፍቅር ግባ ልጄም ሁን ያላየኸውን ፍጹም መለኪያ የሌለውን የዘላለም ሕይወትና ደስታዬን ውረስ ብሎ በፍቅሩ ጠራው፡ ለዚህ ኢትዮጵያ ቀድሞም በሕገ ልቡና ፣ በሕገ ኦሪት ፤ ከዚያም በወንጌል አምና ወደ ፍቅሩ ከፈለሰች ሺዎች ዘመናት ተቆጠሩ፡፤ ዓለም አፈዘ፣ ተሳለቀ፣ ከንቱ ዓለም ዲያብሎስ በሰጠው ቅራቅንቦ፤ በተኮለኮለው የሲሚንቶ ክምር፣ በወረቀት ብር ተደልሎ፣ የዘላለም ሕይወቱን ወርውሮ ጣለ፡፡ ይህ በሽታ ኢትጵያውያንንም ከተዋህዶ እምነት ውጭ ሆነው ወደ ዲያብሎስ እንዲፈልሱ አድርጎአቸዋል፡፡ ከተመረጡት በስተቀርና የአለም ቅራቅንቦ የዲያብሎስ ፈተናና መደለያ ያላሸነፋቸው ዛሬ ባለ ድል ሆነዋል፡፡ አንዱ መልእክትም ይኸው ዛሬ በዲያብሎስና እሱን በተከተሉ የአለም ሕዝብ ላይ የእግዚአብሄር ፍርድ እንዲፈጸም እያደረጉ ይገኛሉ፡፡ እነሱ ወደ ድል ! ዓለም ወደ ጥፋት የመተላለፍ ጉዞ ጀምረዋል፡፡ ይህ ጉዞ ከጀመረም ወደ ሰባት ዓመት እየተጠጋ ነው፡፡ ማን ባለድል እንደሚሆን በቅርብ የምናየው ይሆናል፡፡ አፍሪካ በሁለተኛው የእሳት ወንፊት ምን ይገጥማታል፡፡ ዓለም የሚገጠመው እጣ ፋንታ ሁሉ ምልክት አልባ የሆኑ የአፍሪካ ሕዝቦችም፤ተፈጻሚ ይሆን ዘንድ በልዑል ታዟል፡፡ አፍሪካም በመናፍቃን ፣ በተረት አምላኪዎች፣ በካቶሊኮች፣ በባእድ አምልኮ ተከታዮች፣ በጠንቋዮች፣ በተብታቢዎች፣የተተበተቡች ናት፡፡ መሪዎቹ እንዲሁ ከመምሩ ደቀ መዝሙሩ እንዲሉ በአለም ካሉ የከፋት ባለጸጎች በልጠው ስለተገኙ፤ ከላይ የተዘረዘሩት የቅጣት ትዛዞች በሙሉ ተፈጻሚ ይሆንባቸዋል፡፡ ለአውሮፓ፣ ለአሜሪካ፣ ለኤሽያ የታዘዙት የቅጣት ፍሰቶች በሙሉ እንዲፈጸሙባቸው በልዑል ፈቃድና ትዕዛዝ በኔ በባርያው በኩል ታዟል፡፡ ይህ የቅጣት ፍሰት ሁሉም የአፍሪካ ሃገሮች እጃቸውን በኢትጵያ ለሚጸናው የልዑል የጽድቅ መንግስት በዙፋኑም ለሚቀመጡት ባሮች ሲሰጡ ብቻ ይሆናል የሠላም አየር የሚያዩት፡፡

## 15 / መካከለኛው ምስራቅ፡-

ይህ ስፍራ በአህጉራት መሃከል ላይ የሚገኝ ሲሆን የአመጹም፣ የክህደቱም፣ የተረት እምነቱም ፣ የዲያብሎስ ጽ/ቤቱም በዚህ ስፍራ ይገኛል፡፡ይህ ስፍራ እነ ሶሪያን፣ኢራንን፣እነቱርክንን ፣ ዮርዳኖስን፣ እስራኤልን፣ የመንን ኢራቅን፣ሳውዲ አረቢያን፣ ባህሬንን፣ አማንን፣ኩዌትን፣ ዱባይን፣ ካታርን፣ ኤምሬትስ፣ ሊባኖስ ያቀፈ ነው፡፡ ይህ ስፍራ እስልምና ከሁሉም በላይ መሰረቱን የተከለበት ፍጹም የአመጽ ምድር ነው ማለት ይቻላል፡፡ የብዙ ክርስቲያን የልዑል ወገኖች ያለቁበት ቦታ ነው፡፡ ምንዝርና፣ ግብረሰዶም፣ ዘረፋ፣ ጨካኝ አገዛዝ፣ በሙሉ የሰፈነበት ሲሆን በአውሮፓና በአሜሪካ የምናየው አመጽ ሁሉ በዚህም ገዝፎ የሚታይ ነው፡፡ ይህም ስፍራ በሁለተኛው የእሳት ወንፊት እንዲመታና እንዲበተን በልዑል ታዝዞበታል፡፡ ምልክት ካለው በቀር የተቀረው በሙሉ ይጠረጋል፡፡ የአንደኛው የእሳት ወንፊት ምን እያደረጋቸው እንዳለ ሁላችንም የምንሰማው የምናየው ነው፡፡ ስለሆነም ይህ ቅጣት እንዲጸጸቱ ለማድረግ ቢሰነዘርም አፌዙበት እንጂ አልተመለሱም፡፡ እንደውም በአመጻቸው በርትተው ገፉበት፡፡ በእግዚአብሄር ፍርድም አላገጡበት፡፡ በመሆኑም ለአውሮፓ፣ ለአሜሪካ፣ ለኤሽያ የታዘዘው ሁለተኛው የእሳት ወንፊት ሙሉ በሙሉ ተግባራዊ ይሆን ዘንድ በልዑል ፈቃድና ትዕዛዝ ተወስኖ ፤ በኔ በባርያው በኩል እነሆ እንዲገለጽ ሆኗል፡፡ ከቅጣቱ የተሰጣችሁን መልእክቶችና ይህንንም አምስተኛ መልእክት፣ በመላው ሚዲያና ፕሬሶቻችሁ ፣ በሬዲና ቴሌቭዥን ፣ እንዲሁም በመላው መረብ ሁሉ በቀን ሁለት ጊዜ ማግለጥ ስትችሉ፡፡ ተጨማሪ ትዛዞችንም በአግባቡ ተግባራዊ ስታደርጉና ሙሉ በሙሉ እጃችሁን በኢትዮጵያ ለሚጸናው የልዑል መንግስትና በዙፋኑም ለሚጸኑት ባሮቹ እጃችሁን ስትሰጡ ብቻ ነው፡፡ የህን ስትፈጽሙ ብቻ ነው ከዚህ ከኢትዮጵያ የልዑል ዙፋን ከባሮቹ ትእዛዝ በምድራችሁ ሲደርስ ሰላማችሁ የሚረጋጋው ሕይወታችሁ የሚመለሰው ከዚህ ውቺ የሚመጣ መፍትሄ የለም፡፡ ስለመካከለኛውም ምስራቅ አገሮች /ኢትዮጵያ የኣለሙ ብርሃን መልእክቶች 1፤ 2፤ 3፤/ በዝርዝር ስለተገለጸ ያንን ያገናዝቡ፡፡

## 16/ የእስካንዲኔቪያን ሃገሮች፡-

እነዚህ ሃገሮች የሚያቅፉት እነስዊድንን፤ ኖርዌይን፣ ፊንላንድን፣ አየርላንድ፣ ስኮትላንድ፣ ግሪንላንድ የመሳሰሉትን ሲሆን እነዚህ ሃገሮች በሁሉም ድርጊታቸው ከአውሮፓውያን ምንም የሚለዩ አይደሉም፡፡ ግብረሶዶሙ፣ ምንዝርናው፣ ዝርፊያው፣ ንጥቂያው፣ ዘረኝነቱ የሞላባቸው ናቸው፡፡ የመናፍቃን ከባቢሎን ቀጥሎ ትልቁ ምሽግ ናቸው በነዚህም ዘንድ ሃገሮቹን ሸፍኖ የሚሰራ ተግባር ነው፡፡ እነዚህም የዲያቢሎስ ምሽጎች ከዚህ የሚከተለው ቅጣት በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል እንደሚከተለው ታዟል፡፡

## ትእዛዞች፡-

በእነዚህ የእስካንዲኔቪያን ሃገሮች በሙሉ፤ በአውሮፓ፣ በአሜሪካ፣ በኤሽያ ይፈጸሙ ዘንድ የታዘዙት ሁለተኛ ደረጃ የእሳት ወንፊት ይጠርጋቸውና ያጸዳ ዘንድ ታዟል፡፡ እስትምፋስ የሚገኘው ለሌሎች እንደታዘዘው እኒህም ሃገሮች አለምንም ቅድመ ሁኔታ ሙሉውን መልእክት /ኢትዮጵያ የአለሙ ብርሃን መላእክቶች 1፤ 2፤ 3፤/ባላቸው ሚዲያና ፕሬሶች፣ የመረጃ መረቦች፣በሬዲዮና በቴሌቪዥኖች በየቀኑ ሁለት ጊዜ ማስተላለፍ ከመልእክቱም አንዳች እንዳይጎድል እንዳይቀነስ መሆንም አለበት፡፡ ይህን ፈጽመው እጃቸውን በኢትዮጵያ ለሚጸናው የልዑል የከበረ መንግስት በዙፋኑም ለሚሰየሙት ልጆቹ መስጠት ግድ ይሆናል፡፡ በአገሮቻቸው ሰላሙ የሚመለሰው ከዚህ ከኢትዮጵያ ከፀናው የልዑል መንግስት ትእዛዝ ተሰጥቶ በየአገሮቻቸው ሲደርስ ብቻ ነው፡፡

## 17/ በተለይ ዓለምን ለመቆጣጠር በታለመ ንዩክለር፣ ኬሚካል፣ ባዮሎጂካል፣ አልፎም በህዋ ላይ የተጠመዱ የጨረርንም፣ የኒዩክለርንም መሳሪያ የታጠቁ አገሮች እጣ ፈንታ

ዓለም የዛሬው ገፅታዋ ከበፊቱ የተለየ ነው፡፡ የኒዩክለር መሳሪያ እና ሌሎችም የጥፋት መሳሪያዎች ከመፈጠራቸው በፊት ለብዙ ሰዎች መጥፋት ለሃገር ጥፋት የሚሆን መሳሪያ ስላልነበር ዓለም ስጋት አልነበረባትም የጥፋት መሳሪያዎች ከተሰሩ በኋላ ግን ዓለም የስጋት የጭንቀት ዓለም ሆነች፡፡ ዲያቢሎስ የመጨረሻው ጥፋቱ ዓለምንና የሰውን ዘር በሃጢያቱ እንደተጨማለቀ ማውደም ነበር፡፡ ይህ ጥረቱ ተሳክቶለት ዛሬ ዓለምን ለስጋት ያበቁ ኒዩክለር የታጠቁ ሃገሮች / በመሳሪያነት/ ወደ 10 ደርሰዋል፡፡ እነዚህ ሃገሮች እነማናቸው፡- አሜሪካ፣ እንድሊዝ፣ ራሽያ፣ ቻይና፣ ፈረንሳይ፣ ሕንድ፣ ፓኪስታን፣ ሰሜን ኮሪያ፣ እስራኤል እናም ኢራን በመንገድ ላይ ናቸው፡፡ ለኤሌክትሪክ ማመንጫነት ተብሎ በአውሮፓ ከመቶ በላይ በኤሺያም እንዲሁ በብዛት በአፍሪካ እነደቡብ አፍሪካ፣ እነግብፅ ይህንኑ መሳሪያ በሰላማዊ አገልግሎት ስም ለመጨበጥ እየታገሉ ይገኛሉ፡፡

አሜሪካ ከ8000 በላይ የኒዩክለር አረር የያዘች ሲሆን ከሷ በመቀጠል ራሺያ ወደ 8000 የተጠጋ የኒዩክለር አረሮች ይዛለች፡፡ ሌሎች በሺ የተቆጠሩ አንዳንዶችም በመቶ የተቆጠሩ ሌሎችም በ10 የተቆጠሩ የኒዩክለር አረሮች ይዘዋል፡፡ ዓለምን አንዴ ሳይሆን 10 ጊዜ መላልሰው ሊያጠፏት የሚችሉ ናቸው፡፡ ልዑል ባይገታቸው ለሃገር፤ ለሰውም ዘር ባለቤቱ ጥበቃውን ባያደርግ ዛሬ በዓለማችን ምንም የሰው ዘር አይኖርም ነበር፡፡ ዲያቢሎስ ምኞቱ ተሳክቶ ነበር፡፡

አሜሪካም፣ ራሺያም፣ እንግሊዝም፣ ፈረንሳይም፣ ቻይናም እኒህ ሁሉ በምድር ከተከሉት የኒዩክለር ታጣቂ ሚሳዬል በተጨማሪ ከባህር ወደምድር፣ ከባህር ወደባህር፣ ከባህርም ከምድርም ወደ ሕዋ የሚወነጨፉ ኒዩክለር ታጣቂ ሚሳየሎች ከአንዱ ዓለም ጫፍ ወደአንዱ ይህንኑ ኒዪክለርና ባዮሎጂካል፣ ኬሚካል መሳሪያ ተጭነው የሚበሩ ኒዩክለር ቦንብ ጣይ አውሮፕላኖች አሰናድተው፤ ምድሩንም ባህሩንም በመርከብና በጀቶቻቸው ከድነውታል፡፡ ዓለምን ቤተ ሙከራም አድርገዋታል የጃፓንን የ300ሺ ሕዝብ እልቂት ማስታወስ በቂ ነው፡፡ ያዘጋጇት የፍጅት መሳሪያ አይነቱ ተቆጠሮ የሚያልቅ አይደለም፡፡ ኒዩትሮኑ፣ ኒዩክለሩ፣ ባዮሎጂካል፣ ኬሚካል መሳሪያው ሁሉም የሰውን ዘር ለማጥፋት የተሰናዱ ናቸው፡፡ በዚህም የሚጠቀሙት ደግሞ የዲያቢሎስ ሎሌዎች የሆኑት ሞኖፖሊስቶቹና ገዢዎቹ ናቸው፡፡ ስለሆነም ለሰላምም ይበሉት ለጦር ኒዩክለር የፈበረኩ አገሮች አይነታቸው የበዙትን የፍጅት መሳሪያዎች የሚፈበርኩ፣ የሚያከማቹ ሁሉ፡- ከላይ በዝርዝር የተገለጠው ቅጣት እንዳለ ሆኖ ከላይ ለተዘረዘሩት 10 ሃገራት በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባርያው በኩል እነሆ ይህ ተጨማሪ ትእዛዝ ወጪ ሆኖአል፡፡

## ትእዛዞች፡-

ኒዩክለር፣ ባዮሎጂካል፣ ኬሚካል፣ ኒዩትሮንና ሌሎችም የተለያዩ ህዝብ ጨራሽ መሳሪያ የታጠቃችሁ ኒዩክለርን ለሰላምም በሉት ለጥፋት የያዛችሁ የትም አኑሩት የትም፣ ከአገራችሁ ውጪም ብትደብቁት ምላጩአን አንዱ የዚሁ መሳሪያዎች ባለቤት የሆነ ከሳበ ሁሉም መሳሪያዎች ይህንኑ መሳሪያዎች በጨበጣችሁት ላይ ብቻ በናንተው ሕዝብ ላይ ያርፋል፡፡ በላዩ ላይ የጠመዳችሁት ማናቸውም መሪ ኮምፒተሮች የናንተን የታቀደ ፕሮግራም አይከተሉምና፡፡ ኮምፒተሮቻችሁ በሙሉ የተሳከሩና በተለይም አድገናል በማደግም ላይ ነን የምትሉና የናንተንም ይህንኑ የኮምፑዩተር ስርዓት የሚጠቀሙ ሁሉ በሚሳከረው ኮምፒዩተር ሰበብ ኢኮኖሚያችሁ፣ ባነኮቻችሁ፣ ኢንሹራንሶቻችሁ፣ ገበያዎቻችሁ፣ የመንግስትና የሞኖፖሊስት ተቋሞቻችሁ፣ ባቡሮቻችሁ፣ አውሮፕላኖቻችሁ፣ ፋብሪካዎች የጦር ድርጅቶቻችሁ፣ ማንቸውም ከኮምፒዩተር ጋርና በሱ... ያያዙ ሁሉ፣ በዚሁ የኮምፒዩተር መሳከርና ውድቀት፣ ከላይ የተጠቀሱት ንብረቶቻቸው ሁሉ ይወድማሉ፣ ወይም ላንድኛውን ላይከፈቱ ይከረቸማሉ፡፡ ይህም ይፈጸም ዘንድ በልዑል ታዞባችኋል፡፡

ማንኛውም ኒዩክለር፣ ባዮሎጂካል፣ ኬሚካል፣ኒዩትሮን መሳሪያ የታጠቀ አገር ሁሉ እነዚህን የፍጅት መሳሪያዎች በማንኛውም አገር ላይ ለመጠቀም ማሰቡ አይቀርምና፡፡ ይህንን የሚያስብ ሃገር ከተከሰተ መሳሪያው በገዛ ሕዝቡ ላይ ይፈነዳል እንጂ ከአገሩ ወጥቶ በሌላ አገር ላይ አይውልም፡፡ ስለሆነም ከላይ የተዘረዘሩት የጥፋት መሳሪያዎች በሙሉ እገለገልበታለሁ ብሎ የያዘውን ሃገር እራሱን ያጠፉት ዘንድ ታዘዋል፡፡ ጃፓን ለኤሌክትሪክ የገነባችው ሲፈነዳ ለራስዋ ጥፋት ዋለ፡፡ ልክ እንዲሁ ማንኛውም የኒዩክለር ፣ የኒዩትሮን፣ ባዮሎጂካል፣ ኬሚካል መሳሪያ ሁሉ የዚሁ መገልገያ የሆኑ መሳሪያዎች ሁሉ በጨበጡአቸው አገሮች ውስጥ እየፈነዱና ከቁጥጥር ውጪ እየወጡ ሕዝባቸውን ይጠርጋሉ፡፡ በነዚህ መሳሪያዎች ዙሪያ የተሰበሰቡ ገዢዎችም፤ የፀጥታ አባላት፣ ሁሉም ዓይነት ወታደሮች በሙሉ

የጥቃቱ ሰለባ ይሆናሉ፡፡ ከላይ ሞት የተነፈጋቸው ደግሞ በአደጋው ተመትተው በቁማቸው የሰሩትን መሳሪያ ማሰቃያነት እንደላቦራቶሪ እንሰሳ እየተሰቃዩበት ይቆያሊ፡፡ በልዑል ለተመረጠችው፤ ዙፋኑም የልዑል ለሆነችው መንግስትና ተዋህዶ እምነት ከላይ እንደታዘዘው ሊንበረከኩና እጃቸውን ሊሰጡ፤ ጉዳያቸው እዚህ ኢትዮጵያ በልዑል የፍርድ አደባባይ በባሮቹ ፊት ለሚሰየመው ፍትህ ይቀርባሉ፡፡ የልዑልን ቅን ፍርድም ይቀበላሉ፡፡

ትንቢተ ኢሳኢያስ ም፤ 5፤ 11 – 30 ያንብቡ

## 18/ ስለአባቶች እናቶች ስለወንድሞች፣ እህቶች፣ የተመረጡ የልዑል ባሪያዎች /አገልጋዮች/ ላይ የተፈጸመ ጥቃትና ከልዑል የተሰጠ የቅጣት ውሳኔ

እኔም ሆንኩ ወንድሞቼና እህቶቼ፣ አባቶቼ እናቶቼ የልዑልና፣ የድንግል ልጆች እንዲሁም

የከበሩት ቅዱሳን መላእክት ወዳጆች እስከዛሬ በሁለመናችን ላይ ጥቃት ሲሰነዘር ኖሮአል፡፡ ከዚህ መልእክት መውጣት ጀምሮ እስከዛሬ በኛ ላይ ሁለገብ ጥቃትና ስለላ ስታደርጉ የቆያችሁ በየትኛውም መስመር፤ ከማናቸውም ስፍራ ተሰማርታችሁ፣ ከውጪም ይሁን ከአገር ውስጥ ተሰማሩ ለሰራችሁት ስራ ዋጋ መከፈል ስላለባችሁ ከዚህ የሚከተለው ቅጣት በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል ተዟል፡፡

ማንኛውም ግለሰብ ቡድን ባለው የጥፋት መንግስት ተመክቶ ላደረሰብን /ላደረሰችብን/ ሁለገብ ጥቃት በዚህ በተሳተፉ፣ እየተሳተፉ ባሉ ላይ በመላ አካላቸው ላይ አይተውትም ሰምተውትም የማያውቁት አካላቸውን ሽባ የሚያደርግ እሳት፣ በከፍተኛ ስቃይ አቻኩሎ ወደሞት የሚወስድ እቶን በራሳቸው ላይ፣ በመሰረቱት ትዳር፣ ባደራጁት ቤት ንብረት ላይ የውድመት አደጋ፣ የአይን መታወር፣ የአንደበት መዘጋት በመላ ሕይወታቸውና ቤተሰባቸው ላይ የማይጠገን የማይመልሱት አደጋና መጠረግ ይገጥማቸው ዘንድ በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔም በባሪያው በኩል ታዟል፡፡ ይህ ትእዛዝ ከላይ ከታዘዙት ትእዛዞች ጋራ ለሚመለከታቸው እንደ ተጨማሪ እጣት የሚመጣ ነው፡፡ ስለዚህ የእግዚአብሄር ምርጦችና እንቁዎችን መድፈር ምን ያህል እግዚአብሄርን እንደሚያስቆጣና እርምጃ እንደሚወስድ ከዚህ በታች ባለው የእግዚአብሄር ቃል ልታውቁ ትችላላችሁ፡፡

እነሆ እግዚአብሄር ፍጹም ሰው አይጥለውም

የሃጢያተኞችም ድንኳን አይገኝም

የሃጢያተኞችንም እጅ አያበረታም፣ አፍህን እንደገና ሳቅ ይሞላል

ከንፈሮችህንም እልልታ ይሞላል፤ የሚጠሉህ እፍረት ይለብሳሉ   ኢዮብ ምዕራፍ 8፤ 20 – 22

የቀባኋቸውን አትዳስሱ፤ በነቢያቴም ክፉ አታድርጉ ብሎ፤ ሰው ግፍ ያደርግባቸው ዘንድ አልፈቀደም ስለእነርሱም ነገስታትን ገሰጸ፤ በምድር ላይ ራብን ጠራ፤ የእህልን ሃይል ሁሉ ሰበረ፤ በፊታቸው ሰው ላከ፡፡ መዝሙረ - ዳዊት 104፤ 14 – 16

## 19/ የእምነት መርከባችን /የኖህ መርከብ/

የሰራዊት ጌታ ወገኖች፣ የድንግል ልጆች፣ የከበሩት ቅዱሳን መላእክት ወዳጆች፣ የሰማእታት፣ የጻድቃን ወዳጆች እዚህ ሰዓት ላደረሰን አምላካችን ምስጋና ይፍሰስለት፡፡ ባሳለፍነው መከራ፣ ውጣ ውረድ፣ እንግልት ያልተለዩን ልዑል፣ ድንግልና፣ ቅዱሳን መላእክት ከልብ እናመሰግናለን፡፡

በእግዚአብሄር ተሰፋ ፀንታችሁ የጠላትን ማናቸውንም ጥቃት በእግዚአብሄር ፀጋና ቸርነት በተስፋው ታምናችሁ ለተቀበላችሁ፤ የእግዚአብሄር ልጆች፤ እነሆ በትእግስት እፍጻሜው ደርሳችኋል፡፡ የተገባችሁ ስለሆነ ነጩን ልብስ ለብሳችኋል፡፡ ጉዞዋን በጀመረችው የእምነት፣ የጽድቅ መርከብ ተሳፍራችኋል፡፡ አንዳንዶች ውስጧ ገብተው ተደላድለው ስፍራቸውን ይዘዋል፡፡ አንዳንዶች በሁለመናዋ ላይ ተንጠላጥለዋል /ዘግይተው ንስሃ የገቡት/ የሆነ ሆኖ እግዚአብሄርን መጠጊያቸው፣ ምሽጋቸው ያደረጉ ሁሉ፤ ዓለም ከገጠማት የእሳት ወንፊትና መጠረግ አምልጠዋል፡፡ እግዚአብሄር የገባላቸውን የተስፋ ቃል ታምነውበታልና ድሉን ሊጨብጡ በመገስገስ ላይ ናቸው / በመረከባቸው ተሳፍረው/፡፡ ይህ የሁለተኛው የእሳት ወንፊት ዛሬ በአንደኛው የእሳት ወንፊት ውስጥ የምትበጠረውን ዓለም ወደከፈው የእሳት ወፍጮ የሚያሸጋግር ነው፡፡ ጉልበቱም፤ ዛሬ የምናየውንም ሆነ እስከዛሬ ያላየነውን የጥፋትና የጠረጋ ማእበል፤ በ49 እጥፍ አሳድጎ ዓለም በውኑአም በህልሙአም ያላየችውን ጥፋት ይዞ መጥቶአል፡፡ ወገኔ የእግዚአብሄር ሕዝብ

እንደ ሎጥ ሚስት ወደ ኋላ አትይ በእምነት ወደ ተሰጠችህ የልዑልና የድንግል መንግስትና ሃገር ብቻ ተመልከት፡፡ ካጠገብህ ብዙዎች ሊሄዱ ይችላሉ፤ ዘመድ፣ ጓደኛም ሊጓዙ ይችላሉ በነሱ የእሳት መበላት ደንግጠህ ወደኋላ ልብህን አትመልስ ወደጉዳት ትገባልህና፤ አንተ ስትራብ፣ ስትገፋ፣ ስትታሰር፣ ስትንከራተት፣ ቤተሰብህም ሆነ እራስህ ስትናቁ በትእቢት ተሞልተው በዲያቢሎስ ተመክተው ሲያላግጡብህ የነበሩ ሁሉ ቀኑ ጨለመባቸው፡ የማያልፍ መሰላቸው ዓለም ዘወትር እንደደነሱባት የሚኖሩባት ዓለም ምንዝርናው፣ ግብረሶዶሙ፣ውሸቱ፣ ግድያው፣ዘረፋው ሁሉም እንዲሁ ሆኖ የሚቀጥል የመሰላቸው ዝንጉዎች በእሳት ይጠረጉ ዘንድ ሰዓቱ ሞላ፡ በተስፋ መቁረጥ በእምነትህ ጥርጥርን እስከማስገባት የደረስክ ወገኔ አይዞህ ወደመርከብህ ገብተሃል፡፡ መርከቧ ውስጥ ሆነህ ውጪ ያለውን ጩኸት የስቃይ ድምጽ ትሰማ ዘንድ ግድ ነው፡፡ አትረበሽ፣ ዓለም የዘራችውን ስለሆነ የምታጭደው በእግዚአብሄር የፍርድ ሂደት ውስጥ አታጉረምርም! አመስግን እንጂ! እስከዛሬ ደከመህለት፣ መከረኸው፣ ገስጸኸው፣ ንቆህ ትቶህ ሲሳለቅብህ የነበረን በፍርድ ሲያዝ! አንተ ደግሞ ልዑልን ባለቅን ፍርዱ ማመስገን እንጂ ቅር ልትሰኝ አይገባህም፡፡ እኔም አንተም ከምንወዳቸው በላይ ፍፁም በሚልቅ ልዑል ፍጡሮቹን ይወዳል፡፡ ትእግስቱ ሺዎች ዘመናትን ከድኖ መምጣቱን አትርሳ!

አሁን ለፍርዱ እሳት የተጣዱ ሰዎች ይህ መልእክት በመውጣቱ እንኳን በፍጹም የመጸጸት ምልክት አይታይባቸውም፡፡ በምን ህሊናቸው በለመዱት የዲያቢሎሳዊ ህይወት የተቃኘ ነውና፤ የተሸከሙት ዲያቢሎስ ደግሞ ሳይፈጽማቸው አይለቃቸውም፡፡ ስለዚህ መርከብህ ማለት የተዋህዶ እምነትህ ናት፡፡ ቤትህና ቤተሰብህ በዚችው እንቁ እምነትህ በእሳት ስለታጠረች፤ በእምነትህ ፀንተህ ቁም፡፡ የቁጣው እሳት እስከሚያልፍ በቤትህ ተወሰን፡፡ ለተገባቸው ነጩን ለለበሱት በተዋህዶ እምነታቸው ለፀኑት ምልክቱንም ለጨበጡት ባሉበት ስፍራ በመረከቢቱ ተሳፍረዋል፡፡ አንዳችም ይነካቸው ዘንድ ፍፁም አይቻልም፡፡

ትንቢተ ኢሳኢያስ ም ፤ 26 ፤ 20 – 21 ያንብቡ!

20/ ትንሽ ምክር ለልዑል ባሮች፡- መጪው አደጋ ብርቱና ሰው በታሪኩም ሰምቶትም አይቶትም የማያውቅ ስለሆነ፤ የእግዚአብሔር ህዝብ የተዋህዶ ልጆች፤ ቅን፣ የዋህ፣ ትሁት፣ ንፁህ ልብ ላላችሁ ወገኖቼ ማንኛውንም ያስፈልጋል ብሎ ህሊናችሁ ያመነበትን ጥንቃቄ ሁሉ አድረጉ፡፡ ይህ መልእክት እንዲደርሰው ያገኝ ዘንድ ይገባዋል ብላችሁ ላመናችሁበትና ህሊናችሁ ለተቀበለው ሰው ብቻ ስጡ፡፡ ለፍርድ የተጠበቀው ሁሉ ቢያገኘውም ሆነ ባያገኘውም ምንም አይጠቅመውም የመጸፀቻውም የንስሃ መግቢያውም ጊዜ በሹፈት፣ በትእቢት ጨርሷልና! ከእንደነዚህ አይነት ሰዎች በማይመች አካሄድ እንዳትጠመዱ፤ ተጠንቀቁ ! ለሱ መጣው እሳት በማይሆን ተዛምዶ የተጣመሩትን ለብርቱ ፈተና ይዳርጋቸዋልና! እሳት ላይ የተጣለን ስጋ በእጃችሁ ልታወጡት ብትሞክሩ እጃችሁን እንደሚያቃጥላችሁ ሁሉ፤ ወዳጄ፣ ወንድሜ፣ እህቴ ፣ እናቴ፣ አባቴ፣ አክስቴ፣ አጎቴ ሁሉም ስራቸው የተከተላቸው ናቸውና! በእርዳ ተረዳዳ ካለም ባገኘሽው ብልጠትና ዘዴ ልትታደጋቸው አይቻልምና ይህን ምክር ሳትንቅ ተግባራዊ አድርግ፡፡

በእግዚአብሔር ቤት በአገልግሎቱ ላይ የተሰማራችሁ፤ ከአለም ጉድፍ እራሳችሁን የጠበቃችሁ፣ በልዑልና በድንግል እንዲሁም በቅዱሳን መላእክት የተመረጣችሁ ሁሉ፤ አደጋው ቢያስደነግጥም፤ በቤቱ አንድም ሰው ቢገኝ አገልግሎቱን እንዳታቋርጡ አሳስባችኋለሁ፡፡ በስጋው አለም በመንግስትም ስራ ላይ የተሰማራችሁ የተዋህዶ ልጆች እሳቱ ቢፈላም፤ ቢጠርግም ቦታችሁን አገልግሎታችሁን በቅንነት ስሩ እንጂ ሰው ሁሉ ከአጠገባችሁ ቢጠረግ አለቃችሁ ህሊናችሁና የፈጠራችሁ አምላክ ነውና ! ከፊቱ በበለጠ ሁሉንም ሸክም እንደራሳችሁ እንድምነታችሁ ግዴታ ቆጥራችሁ ስሩ፡፡ በአንድ ቦታ፣ በቤተክርስቲያን ፣ በገዳም ወይም መስሪያ ቤት አንድ ወይም ምንም ላይገኝ ይችላልና ! ለምትቀሩት ወሰን የሌለው ሸክም ቢሆንም ግድ ነውና ! አቅማችሁ እስከሚችል መሸከም ይኖርባችኋል፡፡ የልዑል ባሮች በአምላካችሁ፣ በእናታችውና በእናታችሁ፣ እየተመሩ ሁሉንም እስከሚያስተካክሉ ድረስ ! ሸክሙ ሁሉ የልዑል ልጆች ሁሉ ይሆናል፡፡ ከቁጣው እሳት፤ ከመጠረግ ብዙን የሚድኑት ህፃናት ስለሆኑ በምድሪቱ ሁሉ ከእሳቱና ከማዕበሉ የተረፋችሁ ማንኛውምው የእከሌ ነው የእከሌ ነው ሳይል፤ እውነታዎች እስከሚስተካኩ ድረስ መንከባከብ ይገባቸዋል፡፡ ይህ ከልዑል የተሰጠ ገዴታና ትዕዛዝ ነው፡፡ የልዑል ባሮች ስፍራቸውን ሲይዙ ታስረከባላችሁ፡፡

21/ በመልእክቶቹ ስርጭት ላይ ስለሚሰሩ ጥፋቶች መልእክቶቹ እንዳይሰራጩ ለማድረግ መልእክቱ በዝግጅት ላይ ሙሆኑን ዲያቢሎስ እንደነገራችሁ እናውቃለን፡፡ ለዚህም ብላችሁ መልእክቱ በሄደበት አካባቢ የመልእክቱ ፈላጊ በመምሰል፣ ለመልቀም ወይም ያሰራጩታል ያላችሁትን ሰው በሌላ ጥፋት ስም በመወንጀል ለሌላ ሰው እንደይዳረስ ለመከላከል ሌሎችም ዘዴዎች እንደምትቀይሱ እናውቃለን፡፡ ለእሳቱም ቀርባችሁ የመጣው እሳት የማትሸከሙት ሆኖ እያለ ሌላም ጨምርልን የምትሉ ትመስላላችሁ፡፡ ስለሆነም በዚህ ሙከራ ላይ ለምትሰማሩ ሁሉ አዛዡም ታዛዡም አንዳች እንቅፋት ለመፍጠር ብትሞክሩ እንደሞከራችሁት ሁሉ ገና በጅምራችሁ ይህ ቅጣት ይይዛችሁ ዘንድ በልዑል ፈቃድና ትእዛዝ በኔ በባሪያው በኩል ታዘባችኋል፡፡

**ትእዛዝ-**

1/ በየትኛውም አለም ለሚበተነው የቀደሙት የአሁንን መልእክቶች ስርጭት ለማደናቀፍ የሚጥሩ ግለሰብም ይሁን ቡድን መንግስት በጥቅሉ፣ ግለሰብና ቡድኖች በየራሳቸው ላይ የሚፀና በፍፁም የማያራምድ፤ በሰው ሁሉ የተጠላን ነገር በአደባባይ

የሚያስደርግ፤ በጭንቀት በህመሙ ብዛት፤እንደ አውሬ ሆኖ የሚያስጮህን ጥሎም ለረጅም ጊዜ የሚያንፈራፍር፣ አይንንም ህሊናንም የሚያሳውር ነገር ግን የማይ... ጨካኝ መናፍስት የተቀላቀሉበት በርባሪ እሳት ታዘባችኋል፡፡ ይህ ቅጣት በሌሎች ጥፋቶች ላይ ያልተገኙት እንደተጨማሪ ይታከልባቸዋል እንጂ፡፡ ይህ ቅጣት ሌላውን አያስቀርላችሁም፡፡ በተለይ ይህ ማን እንደሆነ እስከአሁን የሰራውን ወደር የለሽ ጥፋቱን ስለምናውቅ በትእቢት ተሞልቶ አሁንም በድፍረት ትንሽም እስትንፋስ ጥፋትን ብቻ የሚያልም ቀጥተኛ ዲያቢሎሳዊ መንግስት ነው፡፡ የሆነ ሆኖ እንደገና ከዚህ መልእክት መውጣት በኋላ መደምደሚያቸውን ስለምናውቅ አያሰገርመንም፡፡ ባለቀው ስራቸው ውስጥ እኛን፣ የልዑል ባሮች እናወካን፣ እናስጨንቃለን፣ ኢኮኖሚያቸውን እንመታለን፣ በሚሉ ላይ ዲያቢሎስ የሰጠቸውን የቤት ስራ ሲሰሩ ቀንም ማታም እናያቸዋለን፡፡ በትንንሽ ጎጆአችን ዙሪያ በምንገባበት በምንውልበት ስፍራ ሁሉ መጠኑን ለመግለጽ የሚታክት የእግረኛ ሰላይ በመቶዎች የሚቆጠሩ በእለት ታርጋ የሚሰማሩ መኪኖች፤ በውስጣቸው የተለያየ መከለያና ምልከታን የማሳቻ ዘዴን የሚጠቀሙ ሰዎች አሰማርተው ሰልለን ዋልን ብለው ይደክማሉ፡፡ የሆነ ሆኖ እነሱም ሲደክሙ እዛው እየተደነቅን እንደሲኒማ ተግባራቸውን ሁሉ ስናይ እንውላለን፡፡ የሆነ ሆኖ ያለዋጋ የሚታለፍ ማናቸውም ስራ በልዑል ፊት የለምና ስራቸው የወለደላቸውን እነሆ በዚህ መልእክት አፍሰውታል፡፡ አይዞህ ባያቸው የዲያብሎስ መንግስትም በዚህ መልእክት ትረፋቸውን ዝቀውታል፡፡

በስራቸው በነውራቸው ለሆኑ የዘመናችን ጉዶች በትንሽ የእሳት ወንፊት ሲበጠሩ ዘራፍ እንቋቋመዋለን ብለው በትእቢት ቆመዋል፡፡ ለዚሁ ትእቢታቸው በ49 እጥፍ ተባዝቶና ያልታሰበና ያልታየ እሳት የተጫነው ሁለተኛው የእሳት ወንፊት ታዘላቸው ደርሷል፡፡ ከዚህ መልእክት መውጣት ጀምሮ ...ይ የውላል፡፡ መልእክቱ ለጥቂቱም ደረሰው ለብዙው ሥራው ስርጭቱን አይጠብቅም፤ የሚፈለገው የመልእክቱ አድራሽ የልዑል ባሪያ እጅ መውጣት ብቻ ነው፡፡ መልእክቱ ባሻው ይሄዳል፡፡ ቅጣቱም ..ሰለው አቅጣጫ ይሰማራል፡፡ በቃ !

አላደመጥክም አልተመለስክም፡፡ ጧትም ማታም ሌትም ቀንም ያለማቋረጥ ዲያብሎስ የሚሸከተውን ፕሮፖጋንዳ ሬዲዮ፣ ቴሌቪዥን፣ ጋዜጣ፣ መጽሔት ይህን አለ ያን አለ እያልክ፤ በእህል መሙላት የሚገባህን ሆድህን በወሬ ብዛት ትሞላለህ፡፡ እውነትን የሚያወራ አንዳች መንግስት በመላው ዓለም በሌለበት ተስፋን ከዲብሎሶች መንግስት ስትጠብቅ እድሜህን ጨርሰሃል፡፡ የዛሬ መንግስታት የኛን መንግስት ጨምሮ ሁሉም የዲያብሎስ ደላሎች ናቸው ብንል የሚቀል ምሳሌ ነው፡፡ ደላላ አንድን ነገር ለመሸጥ ውሸትን እንደ ስልትና ትክክለኛ መንገድ ይጠቀምበታል፡፡ ይህንንም ውሸቱን የሚሸፍንበትና የሚናገረው እውነት እንደሆነ እንዲታመንለት ውድ ልብሶችን፣ መኪናዎችን፣ የንግግር ብሂሎችን ይጠቀማል፡፡ ለዚህ የድለላ ስራ ጉዳቱ ያሳመናቸው ሰዎች ፤ እንዲህ ብለው ገጠሙለት / የደላላ ሃብቱ ልብሱና ውሸቱ / ፡፡ ዛሬም የኛን መንግስት .... ሉትን ሁሉ ብታዩአቸው ከዘረፉት ሕዝብ ከሰበሰቡት ገንዘብ ጥሩ ልብስ ይለብሳሉ፣ ጥሩ መኪና የተ... ይዘው ገደብ የሌለውን ውሸት ይደረድራሉ፡፡ ለዚህ ደግሞ ጥሩ ምሳሌዎች ገዥዎቻችን ናቸው፡፡ በቴሌቪዥን መስኮት ብቅ ብለው ሁሉን እንደሚፈጽሙ፣ ሁሉን አዋቂ እንደሆኑ፣ ከነሱ የሚሰወር መላ እንደ ሌለ ሲናገሩ እንደ ፈጣሪ ቆጥሮ የሚያያቸው የሚሰማቸው ቁጥሩ ብዙ ነው፡፡

ይሁ ሁሉ የእግዚአብሔርን ስራ ማደናቀፍ ያለ ዋጋ ክፍያ ይታለፋል ማለት ስህተት ነው፡፡ የእግዚአብሔር ስራ ማንም በስጋ ጥበብና ጉልበት ሊያደናቅፈው የሚቻል አይደለም፡፡ ሲሞከርም ቅጣቱ ይሰነዘራል፡፡

# ሺ ዘመን/ ምን ይላል፤ ምንስ ያስረዳናል !

# ሺው ዘመን በእግዚአብሄር ቃል እንዲህ ይላል፡፡

የጥልቁን መክፈቻና ታላቁን ሰንሰለት በእጁ የያዘ መልአክ ከሰማይ ሲወርድ አየሁ፡፤ የቀደመውንም እባብ ዘንዶውን እርሱም ዲያብሎስና ሰይጣን የተባለውን ያዘው፤ ሺ ዓመትም አሰረው፡፡ ወደ ጥልቁም ጣለው አህዛብንም ወደፊት እንዳያስት ፤ ሺ ዓመት እስኪፈጸም ድረስ በእርሱ ለይ ዘግቶ ማህተም አደረገበት፤ ከዚያም በኋላ ለጥቂት ጊዜ ይፈታ ዘንድ ይገባዋል፡፡

ከዚህም በኋላ ዙፋኖች ተዘርግተው የሰው ልጅ በላያቸው ተቀምጦ አየሁ፡፡ ስለ ኢየሱስና ስለ እግዚአብሔር ቃል ስለ ሞቱ ሰዎች ቅን ፍርድን ፈረደለቸው፡፡ ለአውሬውና ለምስሉ የልሰገዱትን ምልክቱንም በግንባራቸው በእጃቸውም ላይ ያልተቀበሉትን አየሁ ፤ ከክርስቶስም ጋር ሺ ዓመት ኖሩና ነገሱ፡፡ የቀሩቱ ሙታን ግን ይህ ሺ ዓመት እስኪፈጸም ድረስ አልኖሩም፡፡ ይህ የፊተኛው ትንሳኤ ነው፡፡ በፊተኛው ትንሳኤ እድል ያለው ብፁእና ቅዱስ ነው፡፡ ሁለተኛው ሞት በነሱ ለይ ስልጣን የለውም፡፡ ዳሩ ግን የእግዚአብሔርና የክርስቶስ ካህናት ይሆናሉ፡፡ ከእርሱም ጋር ይህን ሺ አመት ይነግሳሉ፡፡ ሺሁም ዓመት ሲፈጸም ሰይጣን ከእስራቱ ይፈታል፡፡ ባራቱም በምድር ማእዘን ያሉትን አህዛብ ጎግንና ማጎግን እንዲያስታቸው ለሰልፍም እንዲያስከትታቸው ይወጣል፡፡ ቁጥራቸው እንደ ባህር አሸዋ የሚያህል ነው፡፡ ወደ ምድረም ስፋት ወጡ የእቅዱሳንንም ሰፈርና የተወደደችውንም ከተማ ከበቡ እሳትም ከሰማይ ከእግዚአብሔር

ወርዳ በላቻቸው፡፡ ያሳታቸውም ዲያብሎስ ፤ አውሬውና ሃሰተኛው ነቢይ፤ ወደ አሉበት ወደ እሳቱና ወደ ዲኑ ባህር ተጣለ፡፡ ለዘለአለም እስከ ዘለአለም ቀንና ሌሊት ይሰቃያሉ፡፡

ታላቅና ነጭ ዙፋን በእርሱም ላይ የተቀመጠውን አየሁ፤ ምድርና ሰማይ ከፊቱ ሸሹ፡፡ ስፍራም አልተገኘላቸውም፡፡ ሙታንንም ታናናሾችንና ታላላቆችን በዙፋኑ ፊት ቆመው አየሁ፡፡ መጽሐፍት ተከፈቱ ሌላም መጽሐፍም ተከፈተ እርሱም የህይወት መጽሐፍ ነው፡፡ ሙታንም በመጽሐፍት ተጽፎ እንደነበረ እንደስራቸው ተከፈሉ፡፡ ባህርም በሱ ውስጥ ያሉትን ሙታን ሰጠ፤ ሞትና ሲኦልም በእሳት ባህር ውስጥ ተጣሉ፡፤ ይህም የእሳት ባህር ሁለተኛው ሞት ነው፡፡ በሕይወት መጽሐፍ ተጽፎ ያልተገኘው ማንናውም በእሳት ባህር ውስጥ ተጣለ፡፡

የዮሐንስ ራእይ ፤ ምዕራፍ 20 በሙሉ

ከላይ ያለውን የልዑል ቃል በሚገባ ለሚስተውለውና በእውነተኛይቱ የተዋህዶ እምነት ውስጥ ያለ ሰው መንፈሱም የልዑል ነውና ጠንቅቆ ይረዳወል ብለን እንምናለን፡፡ ብዙ የዘመኑ ፈላስፎችና እምነት ለበስ ካባ ያጠለቁ ቃሉን ፍጹም በተዛባ ሁኔታ በመተርጎም « በምድረ ላይ ክርስቶስ አይነግስም፤ ቃሉ የሚለው የው የመጨረሻ ዓለም ስትሰበሰብ ልዑል በሚሰጠው ፍርድ የዘላለም ሕይወት ወይም የዘላለም ሞት ይሆናል፤ ሁለት ትንሳኤ የለም ፤ ያው አንዱን ትንሳኤ መጀመሪያ ስናምን ስንጠመቅ የመጀመሪየው ትንሰኤ፤ ከሞት በኋላ ሲፈረድ ሁለተኛው ትንሳኤ ማለት ነው፤ የሚል ቃልን በራሳቸው ምሁርነት ዲያብሎሳዊ መነጽር በመመራት ከለይ ለነጽፅር ቃል በቃል ያስቀመጥኩትን የልዑልን ቃል አንድ ትንሳኤ እንጂ ሌላ የለም የሚል ድምዳሜ ይሰጣሉ፡፡ ዓላማው ዛሬ በመጨረሻው ሰአት እውነቱ መገለጫው ላይ በመድረሳችን ይህንን የተዛባ ትንታኔ የሚሰጡን መናፍቃንና፣ ካቶሊካውያን ፣ ምሁር ተብየዎች ናቸው፡፡ በቅርቡ አንዳንድ ጸሐፍት ነን ፤ የተዋህዶ እምነት ተከታይ ነን የሚሉ፤ በማህበረ ቅዱሳን ውስጥ ያሉ፤ ይህንኑ ጽሁፎቻቸውን ማህበሩ ባዘጋጀው ተዘዋዋሪ መሸጫ ላይ ሲሸጡ በማስረጃነት ይዤዋለሁ፡፡ የፍጻሜውም ዘመን የሚል ርእስ የያዘ ነው፡፡ ፈልጋችሁ ማየት ትችላላችሁ፡፡ ጽሁፎቻቸው የሺውን ዘመን ትንሳኤ የሚቀበሉትንና እንደ ልዑል ቃል የተረዱትን የሳይንስ ስያሜ ይሰጡአቸዋል፡፡ በዚህ ዘመን ሳይንሳዌ ትንታኔ በእምነት ላይ አክሎ መጻፍ የዚህ ዘመን የዲያብሎስ ከእውነት ማስወጫ ዘዴ ነው፡፡ ልብ በሉ ዲያብሎስ ወደ ጥልቁ ወርዶ ሲጠፈር ሰዓቱ ሞላ፤ እንዴት ብሎ ነው ለሺዘመን ልታሰር ነው ብሎ የሚነግረን፡፡ ሙለውን መልእክቶች ጠንቅቃችሁ ስታነቡ፤ መልክቶቹ የያዙት እውነት ዛሬ ሊፈጸም ስለቀረበው የልዑል መንግስት ዘመን ነው አስረግጠው የሚነግሩን፡፡ እንደ ቀደሙት እንደ መልክቶቹ ከለይ በንጽፅር የቀረበው ቃሉም የሚያረጋግጥልን ይህንኑ ነው፡፡ ሰማይና ምድር ይሸከሙት ዘንድ ያልቻሉት ኃያል ጌታ እንዴት በምድር ላይ ዙፋን ይዘረጋል ! አብረውትስ የሚነግሱት ልጆቹ እንዴት አብረውት ይነግሳሉ ! የሚለው ጥያቄ ለብዙዎች ግር ሊል ይችላል፡፡ ልዑል ከነ ክብሩ ትሸከም ዘነድ ምድር አትችልም፡፡ ሰማይ ዙፋኔ ምድርም የእግሬ መረገጫ ናት፤ ምን አይነት ቤት ለኔ ትሰራለህ ብሎ ጌታ ለዳዊት ቤትህን እሰራለሁ ጥያቄ መልሱን በጥያቄ ፤ የመለሰበትን ስናስብ፤ ለልዑል ዝፋንም ለእረሱ ማረፊያ ቤት ማዘጋጀት አይቻልም፡፡ ቃሉ የሚለው በፊተኛው ምሳሌ እድል ያለው በፁእና ቅዱስ ነው፤ ሁለተኛው ሞት በሱ ስልጣን የለውም ፤ ነገር ግን የእግዚአብሔርና የክርስቶስ ካህናት ይሆናሉ፡፡ ከእርሱም ጋር ይህን ሺ ዓመት ይነግሳሉ» ይላል፡፡ ከላይ ያለው ሙሉው ቃል የወሰድኩት ቃል፤ ካህናቱ እድለኞቹ ! የተመረጡት፣ የተወደዱት፣ በእግዚአብሔር መንግስት ዐይን የሚታዩት እንቁዎቹ የሚላቸው፤ በምድሪቱ ላይ እግዚአብሔር አብን፣ እግዚአብሔር ወልድን፣ እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስን ይለብሱታል፡፡ በአንደበታቸው ይፈርዳል፤ በ ቁጣቸው ይገስጻል፣ በፍረዳቸው እንደፍርዳቸው ቃሉን ያጸናል፡፡

የወደዱትን ይወዳል፣ የጠሉትን ይጠላል፡፡ ቃሉን ትዛዙን ይፈጽሙ ዘንድ በራሱ በከበረው መንፈስ ቅዱስ የተሞሉ ናቸውና የራሱን ፈቃድ ብቻ የፈጽማሉ ፡፡ በዚህ ሁኔታ ሺው ዘመን እስኪፈጸም ድረስ በዙፋኑ ላይ ከኒሁ የታመኑት ልጆቹ ይነግሳል፡፡ ስለዚህም በምድሪቱ ላይ ልዑል በወደዳቸው ባከበራቸው ልጆቹ ክብር መንፈሱን አዋህዶ ይነግሳል፡፡ ለዚህ ሰዓት የሚበቁት / ኢትዮጵያ የአለም ብርሃን መልእክቶች 1 ፤ 2 ፤ 3 ፤ / እንዳረጋገጡልን እጅግ ጥቂቶች ናቸው፡፡ ዓለም 7ቢሊዮን ህዝብ ተሸክማለች፡፡ ነገር ግን 99 በመቶው የዲያብሎስ ተስፈኛና ተጠዋሪ ነው፡፡ ስለዚህ ስንት ሰው ለዚህ ይበቃል፡፡ መልሱ አጭር ነው፤ እጅግ ጥቂት ሰው ያደለው / በኔ ግምት እንደ ጌታ ቁጥሩን ባላውቅም በጥቂት ሚሊዮኖች የሚቆጠር ሕዝብ ከተረፈ ድል እንጂ ጉዳት ነው አልልም፡፡ በጌታ ግን ሊያንስም ሊጨምርም ይችላልና ! የሚጸናው የአባቴ ፈቃድና ውሳኔ ብቻ ነው፡፡ / ስለዚህ በየዋህነት ስለ ሺ ው ዘመን የተዛባ ጽሁፍ የምትጽፉ ፤ የምታመጡት ጉዳት ባይኖርም ለራሳችሁ ከጥፋታችሁ ተመለሱ፡፡ ለጥፋቱ በዲያብሎስ ታዛችሁ ፣ ተመክራችሁ በምሁርነት ካባ ተጀቡናችሁ ለጥፋት ለምትዳክሩ የፖለቲካና የሆዳችሁ ፍርፋሪ የተሸነፋችሁ ደካሞች፤ በዚህ መልእክት ፍርዳችሁ ስለወጣ ፤ ለማታዩት ትንሳኤ ብትጽፉ፣ ባትጽፉ የምታመጡት እንደሌለ ላረጋግጥላችሁ እወዳለሁ፡፡ መልእክቱ ውስጥ ይህን ያህል ስፍራ የተሰጠው፤ ስለ ተጠራጊዎቹ ሳይሆን የልዑልን ፣ የድንግልን፣ የቅዱሳን መላእክት ወዳጆችን፣ ለመጀመሪያዪቱ ትንሳኤ የታደሉትን ከናንተ ዲያብሎሳዊ አረም ለማፅዳት ታስቦ ብቻ ነው፡፡

ቃሉን ማሳከር የሚያነበውንም ሰው ማሳሳት ፤ ለመረዳት የሚቸግረውን ሰውም ኢላማ አድርጎ የጥፋት መስረት ታላቅ ወንጀል ነው፡፡ ሺው ዓመት እስከሚፈጸም ድረስ በእርሱ ላይ ዘግቶ ማህተም አደረገበት፤ ከዚያም በኋላ ለጠቂት ዘመን ይፈታ ዘንድ ይገባዋል፡፡ ዲብሎስ ለዘላለም እስከ ዘለአለም ተጠናቆ ወደ ገሃነመ እሳት ከመውረዱ በፊት ከፊታችን ያለውን ሺውን ዘመን በከባድ

ሰንሰለት ታስሮ ያሳልፋል፡፡ እሱ አብሮ ብፁእና ቅዱስ የተባሉት የእግዚአብሄር ሕዝቦች ይነግሳሉ፡፡ ከለይ ያለው ቃል እንደሚነግረን ይህ ...ቸው ትንሳኤ ለነዚህ ለታደሉት ብቻ የተሰጠ ነው፡፡ ስለ ኢየሱስና ስለ እግዚአብሔር ቃል ስለሞቱ ሰዎች ነፍስ ቅን ፍርድ ፈረደላቸው፡ ዛሬ ያለን ሰዎች ስለነዚህ ቅዱሳን ሰማእታት ብዙም አንረዳም በቃሉ ...ያት በገዥዎች እንደ ካቶሊክ በመሰሉ ድርጅቶች እና በሌሎች እንደ ከብት ታርደዋል፣ ተጠብሰዋል፣ ተላጭተዋል፣ ለአውሬ እንደ መጫወቻ ተጥለዋል፡፡ ዛሬ ሁለቱም ገዳዩም ለእውነት፤ የተሰዋውም በመቃብር ውስጥ ሲሆኑ፤ ቅዱሳን በገነት፤ ነፍሰ ገዳዮቹ በሲኦል ፍርዳቸውን ይጠባበቃሉ፡፡ ዋናውና ሁሉም ምድር ወይም ተጠቅልለው የመደምደሚየው ፍርድ ከመሰጠቱ በፊት፤ ለነዚህ ሰማእታት ደም ፍርዱ ይሰጣል፡፡ የወንጀለኞቹ፣ የነፍሰገዳዮቹ ልጆችና ድርጅት ዛሬም ዓለምን እየነዱ እየፈጩ ለመሆናቸው፤ አንተም እኔም እነሆ ምስክር ነን፡፡ ይህ ሁሉ ፍርድና አፈጻፀም የመጣው የአያት ቅድመ አያቶቻቸውን ዛሬም እየፈጸሙ ያለውን ወንጀላቸውን በቅን ፍርድ ለመክደን፤ ከ6 ዓመት በፊት ጀምሮ የሚፈስልህን ቅን የልዑልን ፍርድ እሰከ ዛሬ በወጡት መልከቶች ስትሰማ ቆይተሃል፡፡ ፍርድ ተሰጥቶአል በተግባርም ሙሉ በሙሉ ይፈጸማል፡፡ የሰማእታቱ ጀግኖች ደም ብድራቱም ይከፈላል፡፡ የነሱ ፍሬ የደማቸው ዋጋ የሆኑት ልጆቻቸው የ..ት የተሰውለት ተዋህዶ እምነታቸው ባለድል ትሆናለች፡፡ ለአውሬውና ለምስሉ ያልሰገዱለትን ምልክቱንም በግንባራቸውና በእጃቸው ላይ ያልተቀበሉትን አየሁ፡፡ ከክርስቶስም ጋር ሺ ዓመት ኖሩና ነገሱ፡፡ የተቀሩቱ ሙታን ግን ይህ ሺ ዓመት እስኪፈጸም ድረስ በሕይወት አልኖሩም፡፡ ይህ የፊተኛው ትንሳኤ ነው፡፡

ሰመእቱ ጊዮርጊስ ፣ እነ ሰማእቷ አርሴማ ፣ ስፍር ቁጥር የሌላቸው ሰመእታት ሁሉ፤ በገነት ሆነው በአጸደ ነፍስ የልዑልን ፍርድ ሰምተዋል፡፡ ረክተውም አፈጻፀሙን እየተመለከቱ ይገኛሉ፡፡ ዛሬ የአውሬውን ምልክት በግንባራቸው በእጃቸውም ያላደረጉ ተለይተው የልዑልና የድንግል ማህተም ተደርጎባቸዋል፡፡ እጅግ በቁጥራቸው ትንሽ ናቸው፡፡ የነፍሰ ገዳዮቹ የአውሬው ልጆች ግን ከ6ቢሊዮን በለይ ቁጥር ይዘው ምድርን ሸፍነው የመጨረሻፍረዳቸውን በዚህ መልእክትና በቀደሙት መልእክቶች ሰምተዋል፤ እየሰሙም ነው፡፡ ባይሰሙም አይጨንቀንም አይገደንም ነገ ለማይኖሩት ! ስራቸው ላጠፉቸው ! የልዑል ቅን ፍርድ ለያዛቸው ለምን ይገደናል ! ሲሄዱም ወደ ሲኦል፤ ዓለም ከሺው ዘመን በኋላ ስትፈጸም ደግሞ ወደ ገሃነማቸው ይገባሉ፡፡ የልዑል ልጆች ደግሞ የዛሬዎቹ ከጀግኖች አባቶቻቸው የወረሱትን የተዋህዶ እምነታቸውን ጨብጠው በአባቶቻቸው በእናቶቻቸው ሰመእትነት በለ እድል ሁንው ዛሬ ተመርጠው ለሺው ዘመን ሊነግሱባት ተዘጋጅተዋል፡፡ የዮሐንስ ራእይ 20 ያስጨበጠን ታላቅ ሚስጥር ይኸው ከለይ ያየኸው ነው፡፡ ከዚህ ወጪ የሚጻፈው ሁሉ በይሆናልና በራስ ሃሳብ፤ የልዑልን ቃል እንደ ፈቀዱ በመተረጎም የሚከናወን በመሆኑ ሃሰተኛ ነው፡፡

# 5 / ማጠቃለያ

ለዚህ ሰአትና ጊዜ እንደቃሉ እንደገባልን ተስፋ፤ በእምነት እንደጠበቅነው ያደርግ ዘንድ፤ ፍርዱንም ..ሃይ ያወጣ ዘንድ፤ ለዑል የሺ ዘመን ትእግስቱን ጨረሰ፡፡ ከኅዳር 7 ቀን 1998 ዓ.ም ጀምሮ ፍጹም ፍርዱን ታውቅ ዘንድ በኔ ባንድ ውዳቂ የተናቀ ባሪየው በኩል ተናገረ፡ እንዲሁም ደግሞ ለፍርዱም ቅሬታም ለንስሃም ሁሉም የአዳም ዘር ይተጋበት ዘንድ ሁለት ዓመት ተኩል፤ በትእግስት ጠብቆ ፣ ቅር ላለውም ፣ ለተደሰተበትም ፣ በግንቦት 27/9/2000 ዓ.ም የመጀመሪያውን ውሳኔ ያጸና ፍርዱ በኔው ውዳቂ ባርያው በኩል ገለጸ፡፡ ከዚህ በኋላ ውሳኔው ወደ ተግባር መሸጋገሩን የሚያረጋግጥ የፍርድ አፈጻፀም ውሳኔ በመጋቢት 19 ቀን 2001 ዓ.ም አሁንም በናቃችሁት፤ በኔ ባንድ ውዳቂ ባሪየው በኩል እንዲገለጥ ሆነ፡፡ ይህ ሁሉ የሰውን ልጅ አላስደነገጠውም፤ በቁጥር እጅግ ጥቂት ከሆኑ በስተቀር፡፡ እንኳን ..ትበት እና ንስሃ ሊገባበት ፤ በመልእክቶቹ ማፌዝን ጨምሮ እንደ እብድ ቃል በመቁጠር ዋጋ ሳይሰጥ ቀረ፡፡ ዓለም ! ምን ይደረግ ! በምንስ ቢነግሩህ ይገባህ ይሆን? ተደከመ፣ ተቆየ አልሆነም፡፡ የመጀመሪያ የእሳት ወንፊት ቢያንስ ከእንቅልፍ ያነቀል፤ ሰው እንዴት እንደጌኛይቱ በዲያብሎስ፣ ጆሮውን ፊቱን ተሸብቦ ሲነዳ አይነቃም፡፡ ለኔ በግሌ ዘመኔን ሁሉ ሲገርመኝ የሚኖር ነው፡፡ የእግዚአብሔርም የትእግስቱ ብዛት እንዲሁ ሲያሰደምመኝ ይኖራል፡፡ ያም ሆነ ይህ እፍጻሜው ደርሰናል፡፡ አሁን ተመለስ አትመለስ ብሎ የሚያነጋግረን ነገር የለም፡፡ አይኖርምም፡፡ የዚህ መልእክት መውጣት ዋናው ጉዳይ የቅጣቱን ጅማሮ ያበሰረውን አሁንም በድርጊቱ ላይ ያለውን የመጀመሪያውን የእሳት ወንፊት የአዳም ዘር ሊደነግጥበትሲገባ፤ የለም በሳይንሳዊ ዘዴዎቼ /ዲያብሎስ ባስታጠቀኝ/ ብልሃትና እውቀቴ በሳይንሱም ባፈራኋቸው ቁሶቼ የመጣውን ሁሉ እመክታለሁ ፤ እየመከትኩም ነው፤ በሚል ፕሮፖጋንዳ ራሱንም መላውን ዓለምም እያደናገረ በመሆኑ ድራማዎቹና ተውኔቶቹ ሁሉ፤ እውነት መስለው ብዙውን ሰው፤ በተለይም የእግዚአብሔርን ሕዝቦች መንፈስ በማበሳጨቱና በማቁሰሉ፤ በትእቢቱም በጥፋቱም አንዳችም ወደ ሁዋላ ማለት ስላላሳየ ይህ ሁለተኛ የእሳት ወንፊት ከልዑል ታዞ ወጣ፡፡ ትእቢታችሁ የልዑልን ፍጹም ቁጣ ቀሰቅሶ ከመንበሩ በቁጣ እንዲነሳ አደረገ፡፡ ከአሁን በኋላ ይህንን ሁለተኛውን የእሳት ወንፊት የሚቋቋም አይደለም፡፡ ገና ከጅምሩ ሁሉም የሰው ዘር ፤ መቆሚያና መደበቂያ አጥቶ በጭንቀትና በምጥ በሞት ጥላ ውስጥ የሚወድቅበት ነው፡፡ እንኳን በሙሉ ኃይል መጥቶ ይቅርና ! እንግዲህ ይህ መልእክት ደርሷችሁ የምታነቡ የእግዚአብሔር ወገኖች እንዲሁም ጠላቶች ለሰው አድርሱት ይስማው ይወቀው እናንተም አገልግሎት ነውና ተባረኩበት፡፡ በልዑል ተስፋ ለጸናችሁ በጊዜያዊ ችግር ራሳችሁን አታውኩ፡፡ ስለ ብዙ አታስቡ ፤ ስለ እለቱ ብቻ ይበቃል፡፡ ምን ያደርግላችኋል፡፡ የሚሸኙት እኮ ብዙ ናቸው፡፡ ሁሉንም ትተውት ነው የሚሄዱት፡፡ ተለምናችሁ ነው የምትሹትን ሁሉ የምትወስዱት፡፡ በመልካም ሰዓት ሰው እንቁ ነው፡፡ የተወደደም ነው፡፡ እንኳን ሊቸገር ሊሰጠው የሚቀበለው ያጣል፡፡ ሁሉ ስላለው ማንም ለምንም እንደዛሬው ስለችግር በማውራትና በመጨነቅ አያሳልፍም፡፡ ዛሬም የምታዩዋቸው ተጠራጊዎች ገንብተዋል ኮልኩለዋል  በሃብት በብልጽግና ማማ ላይ

ናቸው፡፡ በናንተም እየተሳለቁ ! እንደፈረአን ሰራዊት ደግሞ አታዩአቸውም፡፡ ታሪካቸው ይከደናል፡፡ ዓለምን ቀይደው የያዙት የተባበሩት መንግስታት ፣ የአውሮፓ ህብረት፣ የአፍሪካ ህብረት፣ የአረብ ሊግ፣ የደቡብ አሜሪካ ህብረት የኔቶ ጦር ቃል ኪዳን ድርጅት፣ የጂ ስምንት ሀገሮች፣ የጂ 20 ሃገሮች፣ ሌሎችም አለም አቀፍ ድርጅቶች የሚባሉ ሁሉ ዲያብሎስ ደራጃቸው መጠቀሚያዎቹ ስለሆኑ ወደ ትቢያነት ይጣላሉ፡፡ የጨነቃቸው ስለሆኑ፤ በውጪ በአገር ውስጥ በተለያየ ጎሬ የዘረፉትን የከማቹትን ለመሸሽግ በየአለማቱ ሲንቆራጠጡ ታያላችሁ፡፡ የትም አያደርሱትም፤ ምድርን የሚወርሱ የእግዚአብሔር ሰዎች ናቸውና ! በባንክ ቢያኖሩትም ባያኖሩትም ባንኩም ኢንሹራንሱም  ሞርጌጅ ባንኩም ፤ ሌላውም መደበቂያ ሁሉ ይዞ ይወድማል፡፡ እቤታችሁም አታኑሩት ቤቱም እናንተም ጠፊ ናችሁ፡፡ ለልጆቼ አትሉት የእነሱም እጣ እንደናንተው ነው፡፡ ከተመረጡት ምንም ከማያውቁት ሕፃናት በስተቀር፤ ስለዚህ ፍርድህን መጠበቅ ብቻ ነው፡፡

ለማነፃፀር በአቡነ ተክለሃየማኖት ጊዜና ከዚያ በፊት የታተመና የተፃፈውን ግዕዙንም ሆነ አማርኛውን መጽሐፍ ቅዱስ / ሰማኒያ አሃዱ/ ብቻ ተጠቀሙ፡፡

አስጀምሮ ላስጨረሰኝ ፤ ፈቃዱንና ተእዛዙን ለሰው ዘር እገልጥ ዘንድ ከትቢያ አንስቶ ወድዶ ለላከኝ ለእግዚአብሄር አብ ፤ ለእግዚአብሄር ወልድ ፤ ለእግዚአብሄር መንፈስ ቅዱስ ፤ አሃዱ አምላክ ፤ በሃጢያት ባደፈው አንደበቴ ምስጋናዬን አፈስስለታለሁ ! ለእናቴ ለእናታችን ለእመብርሃን ፤ ለንጽህተ ንጹሐን ፤ ለቅድስተ ቅዱሳን ለድንግል ወላዲተ አምላክን አመሰግናታለሁ ፤ በሁሉም በእናትነት እቅፏ ይዛኛለችና ፤ እጅግ ለከበሩት ለቅዱሳን ሊቀ መላእክቶች / ለሚካኤል፣ ለገብርኤል ፣ ለሩፋኤል፣ ለፋኑኤል፣ ለራጉኤል፤ ለሳቁኤል፤ ለአፍንንኤል፣ ለሰዳካኤል፣ ለሰላትያል፣ ለሱርያል፣ ለራሙኤል / የኔ ብየ የምላቸው ወዳጆቼ ሁሉ አመሰግናቸዋለሁ፡፡

ለታመኑለት እኔም ለታመንኩለት ጌታ ለቅን ፈራጁ አምላካችን ምስጋና ለስሙ ሁሌም ከፍ ከፍ ለሚለው ክብርና ስሙ ምስጋና ከዘለዓለም እስከዘለዓለሙ ይፍሰስለት !!! አሜን !

ሃሌ ሉያ ! እግዚአብሄርን ከሰማያት አመስግኑት ፤ በአርያም አመስግኑት ፤ መላእክቱ ሁሉ አመስግኑት ፤ ሰራዊቱ ሁሉ አመስግኑት ፤ ፀሃይና ጨረቃ አመስግኑት ፤ ከዋክብትና ብርሃን ሁሉ አመስግኑት ፤ ሰማየ ሰማያት አመስግኑት!!

፤ መዝሙረ ዳዊት ፤ 148 ፤ 1 – 4

አንተ አምላኬ ነህና ፈቃድህን ለማድረግ አስተምረኝ ፤ ቅዱስ መንፈስህም በጽድቅ ምድር ይምራኝ ፤

መዝሙረ - ዳዊት ፤ 142 ፤ 10

አምላኬ ንጉሴ ሆይ ከፍ ከፍ አደርግሃለሁ ፤ ስምህንም ለዘለዓለም ዓለምም እባርካለሁ ፤ በየቀኑ ሁሉ  እባርክሃለሁ ፤ ስምህንም ለዘለዓለም ዓለምም አመሰግናለሁ!!! መዝሙረ ዳዊት ፤ 144 ፤ 1 – 2

## ጥብቅ ማሳሰቢያ፡-

- ይህ መልእክት የደረሳችሁ ሁሉ በማስተዋል አንብቡት ፤ ደጋግማችሁ ተረዱት፤ ቃሎቹንም ከሰማንያ አሃዱ መጽሐፍ ቅዱስ በመመልከት ለመረዳት ሞክሩ፤ በፍጹም ለክርክር አትታደሙ!! ያ ዘመን አልፎአል፡፡
- በብልጠት የማያልፉት፤ በማናቸውም ዘዴ የማይመክቱት፤ እጅግ ብርቱ ጥፋትና ጠረጋ ስለመጣ የለም ገና ነው፤ ቆይ እደርሳለሁ በሚል የተዘናጋ አካሄድ አትራመድ፤ ህሊናህ ባመነበት ሁሉ ተሰናዳ!!
- ጾምና ጸሎት ገንዘቦችህ ይሁኑ፤ ከዘሙኑ ገገሮች የጥፋት ጉባኤና ምክር ራስህን ፍጹም አርቅ፤ በተለይ ሰባራ ምክንያት / ስራ ነው ትዳር ነው እያልክ / በማያድንህ ምርኩዝ አትደገፍ!! ከተቸዎች፤ ከአላጋጮች፤ እናም ከዲያቢሎስ ሰራተኞች ተጠበቅ!! ከእሳት እራቶች ጋር ምን እጣስ አለህ! ምንስ ያገናኝህና!!

በስተመጨረሻም ሁሉንም በትእግስት ተሸክመህ እንደመጣህ ዛሬም ከንዋኔውን በትእግስት ተከታተል፤ በሺዎች መላእክት የምትጠበቅ የልዑል ልጁ ነህና! ራስህን አሕዛብ በሚለኩበት የስጋ መስፈሪያ / ገንዘብ፣ ሃብት፣ ስልጣን፣ ቤት፣ እውቀት፣ጥበብ / አትለካ፤ እነርሱ ሃብታቸው ከዚህ ዓለም የገበዩት እውቀት፤ የዘረፉት ሃብት፣ ምንዝርናው ውሸቱ ነውና አትምሰላቸው፡፡ ይህ መልእክት በውስጡ ገብተህ እንደተመለከትከው በልዑል የተፈቀዱና የታዘዙ ቅጣቶች ለግዳጅ አፈጻጸም ስለሚወጡ፤ ህሊናህን አረጋግተህ በትእግስት ጠብቅ የደነገጡትን በማበረታታት፤ ያዘኑትን በማጽናናት የእረኝነት ስራህን ተወጣ፡፡ ለዚህ ሰዓት ያደረሰህን ቅን ፈራጅ አምላክ አመስግን!! በጠላቶች የፕሮፓጋንዳ ማእበል ልብህ አይወሰድ! ውሸትና ምላስ ከዲያቢሎስ የተሰጣቸው ትልቁ መሳሪያቸው ነውና የእግዚአብሄር ሰው ግን በነገር ሁሉ ራሱን የገዛና ቁጥብ በመሆኑ በስሜት አትወሰድ!  ይህ አምስተኛው መልእክት የያዘው ብርቱ ትእዛዝን ነውና አፈጻጸሙ ከጀመረ የሚገኝ የእስትንፋስ ጊዜም የለምና! መልእክቱ እንደደረሰህ ልዑል እንዳሳሰበህ ራስህን አሰናዳ!!

ተፈጸመ

ከልዑል ባሪያና አገልጋይ የድንግል ልጅና አገልጋይ

የቅዱሳን የከበሩት መላእክት ወዳጅና ታማኝ

ቀን ---21 / 1 / 2004-------------

ፊርማ-------------------------------

በመስከረም 21 ቀን 2004 ዓመተ ምህረት ተዘገጅቶ ለአዳም ዘር ሁሉ ቀረበ!!

ቀን 19/4/2007 ዓ.ም

በመላው ዓለም ለምትገኙ የአዳም ዘር በሙሉ!!

ይህ መልእክት ስለ ሰባተኛው መልእክት ለመግለፅና ለማወጅ የመጣ አዋጅ ነጋሪ ስድስተኛው መልእክት ተብሎ የሚጠቀስ ነው !!

አዋጅ! አዋጅ! አዋጅ!

ስማ! ልብ ብለህ አድምጥ! ላልሰማም አሰማ!

የአዋጅ ነጋሪ ቃል ! —— የእግዚአብሔርን መንገድ በምድረ በዳ ጥረጉ ለአምላካችንም ጎዳና በበረሃ አስተካክሉ ፡ ሸለቆው ሁሉ ከፍ ይላል ተራራውና ኮረብታውም ሁሉ ዝቅ ይላል ጠማማውም ይቃናል፤ ስርጓጉጡም ሜዳ ይሆናል፤ የእግዚአብሔርም ክብር ይገለጣል ሥጋ ለባሽም ሁሉ በአንድነት ያየዋል የእግዚአብሔር አፍ ይህን ተናግሮአልና!!

ትንቢተ ኢሳኢያስ ምእራፍ 40፤ 3 – 8

ከላይ በርእሱ እንደተመለከትከውና ቀጥሎም በእግዚአብሔር ቃል እንደተረጋገጠልህ ዛሬ ከሰባት ዓመት ቆይታና ትእግሥት በኋላ ልኡል በሙላት መጣ !!!

ለሰባት ዓመት የተደረገው ቆይታ እኛ መልእክት አድራሾች እንደ እናንተ ፋክራ ስለጠፋን አይደለም:: የልኡል ጥበቃ ወዴት ሄዶ ? ትእግሥትና እድል መስጠት የእግዚአብሔር እጅ ሥራውን ተወ ማለት አይደለም ፤ እንዲህ ሆኖም አያውቅም :: ሃያሉ ጌታ አይደከም አይታክት ሁሌም ፈቃዱን ለመፈፀም ሁለመናው ሥራ ላይ ነው:: በቁጥር የማይደረስባቸው ሃይላት ቅዱሳን መላእክትም ያለምንም ዝንጋታ ሁሌም በሥራ ላይ ናቸው:: እኛም ባሮቹ ሥጋ ለባሽ ነንና በሰው ያለ ድካም እኛንም ቢይዘንም የቆምነው በልኡል ፀጋ ነውና ! ብንደክም ብንዝል ብናንቀላፋ ያኔ እንዳውም ብርቱ እንሆናለን ምክንያቱም በእኛ ድካም የልኡል ሃይልና ክብር ይገለፃልና!

የዛሬው አዋጅ ነጋሪና ዋናው አዋጅ ሊመክርህ ወይም ዛሬም ፍርድን ሊያሰማህ ወይም ደግሞ ማስጠንቀቂያ ሊሰጥህ የመጣ እንዳይመስልህ ይህ ሁሉ ሆኖ አልፎአል፤ የሰማም ሰማ የናቀም ናቀ የተፈረደበትም ፍርዱን ተሸከመ :: ለበጎው ቀን የታተመበትም ማረጋገጫውን በእጁ ከጨበጠ ሰነበተ::

በብዙ ምሳሌ በብዙ የእግዚአብሔር ባሮች ያልተደከመ ያልተፈነቀለ መንገድ የለም እንተን ለማዳን! አልሆነም እንጂ ይሁንና እጅግ ጥቂቶች አምልጠዋል :: እጅግ የሚበዛው ቀልጦአል :: ምን ይደረግ ሁሉም ነገር ማብቂያ አለው :: አበቃ!! አሁን የምትሰማው ስለመጠረግህ አይደለም ያ ተረጋግጦ ሰዐትና ደቂቃዎች እየተቆጠሩ ነው :: በማናቸውም ሰዓት ልኡል ባወቃት ጊዜ ተፈፃሚ ይሆናል::

ስለአዋጁ ከዚህ በሚከተለው መልኩ ቀርቦልሃል::

ስለምን የመጣ አዋጅ ነው? ማነው አዋጁን ያወጣው? የሚል ጥያቄ እንደሚነሣ ግልፅ ነው::

አዋጁ ለአንተ ሰማይንና ምድርን ከዘረጋ የሠራዊት ሁሉ ጌታ እግዚአብሔር ዘንድ የመጣ ነው:: ሁሉን ቻይ ከሆነው እግዚአብሔር አብ፤እግዚአብሔር ወልድ ፤ እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ ዘንድ በአ በአንድ እጅግ ታናሽና በደለኛ በሚሆን ባሪያው በኩል ዛሬ ለአንተ የሰው ዘር /መልካሙ ሰው/ ትሰማው ዘንድ ታውጆአል !!!

አዋጅ የሚወጣው ለውቀሳና ለምክር ወይም ተው ተመለስ ለማለት አይደለም ፤ አዋጅ ከአንድ የማስተዳደር የመ ምራት ወይም የመግዛት ሥልጣን ካለው አካል የሚወጣ የሚገዛውንና የሚያስተዳድረውን ሕዝብ እንዲገዛበት እንዲ መራበት የሚወጣ ፤ ይገዙለት ዘንድ ግድ የሆነ ሕግ ደንብና ሥርዓት ነው ። ዛሬ በዓለማችን ሕገ - መንግሥት ተብ ሎ እንደሚጠራው ማለት ነው ። የዛሬው አዋጅ አንግዳ የሚሆንብህ ሁሉን ከፈጠረ ሃያሉ ጌታ ዘንድ መውጣቱ ነው። አንተ የለመድከው ሰዎች ጠመንጃና ታንክን ይዘው ጦር አደራጅተው ሕግ ዘርግተው ገዢህ ነን ብለው በግድህ እንድትገዛላቸው አድርገው ስለሚነዱህ ነው።

የዛሬው አዋጅ ከየት እንደመጣ ካወቅህ ፤ ዓላማው ደግሞ ምን እንደሆን ከዚህ እንደሚከተለው ልትረዳው ትችላለህ ።

የአዋጁ ዓላማ ፤ — አዋጁ ለአንተ ለሰው ልጅ ከልኡል ዘንድ የተላከ ሲሆን ወደ ትንሳኤው ዘመን መሸጋገርህን ላወቅኸው በተጨማሪም ወደሽግግሩ ዘመን ለምትደርሰውም ሁሉ ትተዳደርበት ዘንድ የሚገባ የዓለምን ሁሉ ገጽታ የሚሸፍን የሽግግር ጊዜ ሕግጋተ - ሥላሴና በዘመነ ትንሳኤው ነግሶና ከብሮ ዓለምን ሁሉ የሚያስስተዳድረውን የሚገዛውን ቋሚው ሕግጋተ - ሥላሴ መታወጁን እንድትሰማ ለማድረግ ታስቦ ነው ።

አዋጁ አስራ ሁለት ርእሶችን የያዘ ሲሆን በ100 ገጽ የተሸፈነ ነው ። ርእሶቹም

- መግቢያ
- ከፉ ሰው
- መልካሙ ሰው
- ዕውቀትና ጥበብ ፤ እምነትና ማስተዋል
- ቀደምት ስለተገለጹት አምስት ተከታታይ መልእክቶች
- ወደ ትንሳኤው ተሻጋሪው ሰው
- ሥላሴን እኛ ስንረዳ
- ቅድስተ ቅዱሳን እናታችን ድንግል ማርያምን ስንገልፃት
- ስለተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ወቅታዊ ሁኔታ
- የሽግግሩ ጊዜ ሕግጋተ - ሥላሴና አፈፃፀሙ
- የትንሳኤው ዘመን የዓለም ገዢ ሕግጋተ - ሥላሴ
- ማጠቃለያ

ከላይ የዘረዘርናቸው ርእሶች ሁሉ በአዋጁ ውስጥ ተዳሰዋል። የሽግግሩ ጊዜ ሕግጋተ - ሥላሴ በውስጡ 5 ምእራፎችን 5 አንቀፆችን 19 ንኡስ አንቀፆችን የያዘ ነው ። አንረዳ! በዚህ የሽግግር ጊዜ አዋጅ፤ ሁሉም ሃገሮች ሁሉ ያልፉበት ዘንድ የግድ ነው ። ቅድሚያ ነፃ የምትወጣው ኢትዮጵያ ስትሆን ፤ የሽግግሩም ጊዜ ሕግጋት በኢትዮጵያ ላይ ሥራውን በመጀመር በአዋጁ ውስጥ የተጠቀሱትን ሕጎች በሙሉ ተግባራዊ ያደርጋል ። በፊቱ መሰናከልና ማደናቀፊያን አደራጅተው ለመቋቋም እንወጣለን ለሚሉት ሁሉ ከልኡል ዘንድ ታዘው ሕጉን ለማፅናት እርምጃቸዎችን የሚወስዱ ቅዱሳን መላእከትና የልኡል ባሮች እንደ አልታሰበ ታይቶም ተሰምቶም የማይታወቅ የእሳት ትንታግ ሆነው ይነሳሉ ። እምነታችንና ልኡልን የናቁ ፤ በዘመኑ ደርጅተውና በትእቢታቸው ፀንተው በሰበሰቡት የዘመነ ወታደራዊ ጡንቻቸው ታምነው ፍፁም የዲያብሎስን ሕግ አፅንተው ልኡልን ሲዋጉና ዛሬም የጨለማ ሕጋቸውን ሲያፀኑ ለቆሙ ሃይሎች ሁሉ ከምድሪቱ ፍጹም መጠረጋቸው የግድና አይቀሬ ነው። አዋጁም በፊቱ ያለውን ሰውኛ ጉልበቶችና ጥበቦች ሁሉ አከስሞ የልኡልን ትእዛዝና አዋጅ በምድሪቱ ተፈፃሚ እንዲሆን ማድረግ አለበት ይደረጋልም ። ይህም መወሰኑን አዋጁ ያረጋግጥልሃል።

ዓብዩ ሕግጋተ - ሥላሴ በዋናነት ተፈፃሚ ይሆን ዘንድ በልኡል የፀና ሕገ - እግዚአብሔር ነው ። በሕጉ ውስጥ የተዘረዘሩ 8 ምእራፎች 50 አንቀጾች 83 ንዑስ አንቀፆች የያዘ ነው። ሕግጋተ - ሥላሴ ፀንቶ የሚቆመው በፊቱ ለዘመናቶች የተተከሉትን የዲያብሎስ የጥፋት ተከሎችን በአድማኒያም ያረጁትን በጥፋት ሥራቸው የገረጀፉትን ሁሉ ከምድሪቱ ጠርጎ ካሰወገደ በኋላ ነው ። የቀደመው እባብና ከፉ ሥራው ፍፁም ምድሪቱን የሸፈነ ስለሆነና ምንም እሱ ያልዳሰሰው ሥፍራ ስለሌለ በጠረጋውና በማፅዳቱ ተግባር የማይዳሰስ ሥፍራ የለም። ዲያብሎስ ባቆመው ሥራና

መሠረቱ ላይ የእግዚአብሔር ቤት አይታነፅም ። በመሆኑም አዋጁ የመጣው ከፊቱ ያለውን የጥፋት ዓለም የሚያፀዱ መጥረጊያዎቹን በማስቀደም ነው ።

የሽግግር ጊዜ ያስፈለገው ለምንድንነው የሚል ጥያቄ ማስከተሉ አይቀርም ። ይህ አግባብ ያለው ጥያቄ ነው ። ዓለማችን በጥፋት ሃይሎችና ሰራዊቶች መሪነትና የተቀናጀ የጥፋት ሥራ ሲከናወንባትና ስታስተናግድ ኖራለች ። በዚህ ሂደት ደግሞ ያልተተከለ የጥፋት ተክል የለም ። የወሰደውም ጊዜ በሺዎች የተቆጠሩ ዓመታትን እንደሆነ ማንም አስተዋይ ሰው ይረዳዋል ተብሎ ይታመናል። በመሆኑም የጥፋትን ሥራ ለመንቀልና ለማፅዳት ጊዜ አስፈላጊ ነው።

መንቀል፣ መጥረግ፣ ማፅዳት ብቻ ሳይሆን በምትኩ መልካሙን ማብቀል፣ መትከል፣ መኮትኮት የሚካሄድበት ወቅት በመሆኑ ይህ ሥራ በሚፈጀው ጊዜ የሚከናወነው በሽግግር ህጉ በተቀመጠው መሰረት ይሆናል። ይህ ከተከናወነ በኋላ ዋናው የሚጠበቀው የትንሳኤው ዘመን እንደንጋት ጮራ ልእል በወደዳቸው በመረጣቸው ባፀደቃቸውና በባረካቸው ባሮቹ ታጅቦና ደምቆ ወደ ዘመኑ መግቢያ ንጋት ይዘልቃል ። ከሽግግሩ ሂደት ወደ ትንሳኤው ንጋት በመዝለቅ ውስጥ ታላላቅ የልኡል እርምጃዎች ይወሰዳሉ ።

በዋናው ሰነድ / በሰባተኛው የአዋጁ ሰነድ/ የተዘረዘሩት ርእሶች ለባሙብቶቹ ለልኡል ምርጦችና የተወደዱ ባሮቹን ያንፁ ዘንድ ፤ በሚገባ ከልኡል ቃል ጋር ተፕዝበውና ተደጋግፈው የቀረቡ ሲሆን ፤ ማናቸውም የትንሳኤው ዘመን ሙሽራዎች ሁሉ እራሳቸውን በመፈተሽ ሳያስተውሉትም ሆነ እስተውለውት ነገር ግን በማቅለል የተመለከቱትን በላያቸው ላይ ያሉና የበቀሉ ጉድፎችና እሾሆችን ነቅሰው በንስሃ ራሳቸውን የሚያፀዱበትን መንገድ ያመላከታቸዋል ተብሎ በማሰብ የተዘጋጀ ነው። ከአዋጁም ቀድመው በሰነዱ ውስጥ እንዲቀርቡ የተደረጉት በዚህ ራስን ለበጎው ቀን የማዘጋጀት ሥራን ሁሉም የልኡል ብሩካን እንዲፈጽሙት ለማድረግ ነው።

ይህን አዋጅ ነጋሪ ሰድስተኛው መልእክት ሁሉም ሰው ቢያገኘውም ምንም አይደለም ። የቀደሙት እምስት መልእክቶች ማንንም ሰው ሳይለዩ ለሁሉም ይደርሱ ዘንድ የተፈቀዱና እንዲያውም ዛሬ በዓለማችን ነግሰው ያሉ ገርዎች ሚዲያዎች ፕሬሶች በአብዛኛው አግኝተዋቸዋል። ቢያገኙአቸውም ማንም ዋጋ ሰጥቶ ለሕዝብ አልገለፀም ። ይህ ደግሞ የሚያሳየው የማናቸውም የሰው እንቅስቃሴ ፍፁም በዲያብሎስ ቁጥጥር ሥር ያለ በመሆኑ ማንም ስለመልእከቶቹ የተነፈሰ ሚዲያም ፕሬስም መንግሥትም እንዲሁም ድርጅትም የለም ። በዝምታ እንዲያልቁ ዲያብሎስ በመላው ዓለም ሕዝብ ላይ ከፈረደባቸው ቆይቶአል ። የቀደሙት መልእከቶች በተከታታይ ለእምስት ጊዜ ሲወጡ ፤ ለመላው ዓለም ሕዝብ የልኡልን ፍርድን ምክርን ማስጠንቀቂያን መጪውንም ያለውንም አደጋ በሙሉ በማንሳት ሁሉም ሰው እንዲሰማው የተደከመበት ነው ። በዚህ እጅግ ጥቂቶች ብቻ ተጠቅመውበታል ተብሎ ይታመናል። በንቀታቸው የፅኑት ደግሞ ለዛሬው የመጨረሻ የማይሻር ፍፁም የመጠረጊያ ሰዓት ላይ ደርሰዋል።

እንደቀድሞው ዛሬ ስማኝ ብሎ የሚለምንህ ወይም የሚጠይቅህ መልእክት አይደለም ይልቅስ ሰማህም እልሰማህም ያ ተመዝኖ ታውቆ ተለይቶ ማንነትህ ሰፍሮ በልኡል ሃይላት የመለያ ምልክት ተደርጓል ። በመልካሙ ሰው ፤ ለበጎው የትንሳኤው ዘመን ይደርስ ዘንድ በተመረጠው ሰው ግምባር ላይ ምልክት ተደርጎአል። ምልክቱን ያላገኙት በሙሉ ለታላቁ የቁጣ እሳት ቀርተው ተጠብቀዋል ።የልኡል ቃልም እንዲህ ያረጋግጥልሃል ። ተፈፃሚነቱም በማያወላዳ ሁኔታ የተረጋገጠ ነውና እንዲህ ያውጅልሃል!

እርሱም — እያንዳንዳቸው የሚያጠፉ መሣሪያን በእጃቸው ይዘው ከተማይቱን የሚቀስፉ ይቅረቡ ብሎ በታላቅ ድምፅ በጆሮዬ ጮኸ! እነሆም እያንዳንዳቸው አጥፊውን መሣሪያ በእጃቸው ይዘው ስድስት ሰዎች ወደ ሰሜን ከሚመለከተው ከላይኛው በር መንገድ መጡ በመካከላቸውም የበፍታ ልብስ የለበሰ የፀሐፊም ቀለም ቀንድ በወገቡ የያዘ አንድ ሰው ነበረ ። እነርሱም ገብተው በናሱ መሰዊያ አጠገብ ቆሙ ።

የእስራኤልም አምላክ ክብር በበላዩ ከነበረበት ኪሩብ ተነስቶ ወደ ቤቱ መድረክ ሄዶ ነበር በፍታም የለበሰውን የፀሐፊውንም ቀለም ቀንድ በወገቡ የያዘውን ሰው ጠራ ። እግዚአብሔርም — በከተማይቱ በኢየሩሳሌም መካከል እለፍ በመካከልዋም ስለተሰራው እርኩሰት ሁሉ በሚያለቅሱና በሚተክዙ ሰዎች ግንባር ላይ ምልክት ፃፍ አለው። እኔም እየሰማሁ ለሌሎቹ — እርሱን ተከትላችሁ በከተማይቱ መካከል እለፉ ግደሉም አይናችሁ አይራራ አትዘኑም ሽማግሌውንና ጎበዙን ቆንጆይቱንም ሕፃናቶችንና ሴቶችን ፈጽማችሁ ግደሉ ነገር ግን ምልክቱ ወደ አለበት ሰው ሁሉ አትቅረቡ በመቅደሴም ጀምሩ አላቸው። በቤቱም እንግር ባሉ ሽማግሌዎች ጀመሩ ። እርሱም ቤቱን እርከሱ በተገደሉትም ሰዎች አደባባዮችን ሙሉ ውጡ አላቸው ። እነርሱም ወጥተው በከተማይቱ ገደሉ ። ሲገድሉም እኔ ብቻዬን ቀርቼ ሳለሁ በግምባሬ ተደፍቼ — ጌታ እግዚአብሔር ሆይ ወዮ ! መዓትህን በኢየሩሳሌም ላይ ሲታፈስስ የእስራኤልን ቅሬታ ሁሉ ታጠፋለህን ብዬ ጮኽሁ ።

እርሱም — የእስራኤልና የይሁዳ ቤት ሃጢያት እጅግ በዝቶአል ፤ ምድሪቱም ደም ከተማይቱም አመፅን ተሞልታለች ፤ እነርሱም እግዚአብሔር ምድሪቱን ትቶአታል ፤ እግዚአብሔርም አያይም ብለዋል። እኔም ደግሞ በአይኔ አልራራም ፤ አላዝንምም መንገዳቸውንም

ባሪቾቸው ላይ አመልሳለሁ አለኝ ። እነሆም በፍታ የለበሰው የቀለም ቀንድም በወገቡ የያዘው ሰው — ያዘዝኸኝን አድርጌአለሁ ብሎ ቢቃሉ መለሰ ። ትንቢተ ሕዝቅኤል ምእራፍ ዘጠኝ በሙሉ

አመፃንና ግፍን በማድረግ ምድሪቱን ያከረፉ የሀገራችንም ሆነ የመላው ዓለም ሕዝብ ዛሬ በመጨረሻው ልትደመደሙ ሆነ ። ምልክት ማግኘት የቻሉ ጎበዞች በእንባና በለቅሶ ዘሩ ዛሬ በደስታ ያጭዳሉ ። ቅን የልኡል ፍርድ ምንግዜም አይዛነፍም ። ዳኝነቱም ፍፁም ነው ። ማንም በመሸምገል ወይም ሕፃን በመሆን ከፍርድ ማምለጥ አይቻልም ከቤቱም እንደሚጀምር በቃሉ አረጋግጦአል።

ዛሬ አዋጁን እንድትሰማ ሆኖአል ። አንድን ነገር በስአላዊ መግለጫ ብታየው በአካሉና በሕይወት እስትንፋሱ ስለማታየው አድለ ቢሱ ነህ ። ምክንያቱ ደግሞ ግልፅ ነው። አንተና መሰሎችህ በጥፋት መጥረጊያው ስለምትሸኙ ለማትኖርበት ዓለምና ሐግታ - ሥላሴ/ ስነዱን/ ማግኘትህ ምን ይጠቅምሃል ። ምንም አይጠቅምህም ። ለማየትም ሊኖርህም የሚያበቃ ቅድስና የለኸም ስለዚህ መታወጁን ሰምተህ ለቢጤህም አሰምተህ ፍፃሜህን መጠበቅ ነው። የዘራኸውን ነውና የምታጭደው እኛም በምርጫህ ባገኘኸው ኪሳራህ እያዘንን ከዛሬ ጀምሮ እኛም ተሰናብተንሃል ።ልኡል ተሸከመህ እስከዚህም ዘመን ታገሰህ መከረህ ገሥፀህ ቀጣህ ናቅኸው ካድከው እቃለልከው የሰጠህን ዘመን ሰበሰጠ አመፅና ጥፋት አዋልከው በእርግጥ ናቅኸው ስለዚህ ዘመንህን ሁሉ የተከተለህ ፍርድ ዛሬ ሊጨርስና መዝገብህን ሊዘጋ ከፊትህ ተሰደረ ፤ የማይመለሰውን ቅጣትህን ስላየነው ነው የተሰናበትንህ !!!

አዋጁ ከመቼ ጀምሮ ይፀናል ።

አዋጁ ለአንተ ትሰማው ዘንድ ግድ ስለሆነ ፤ የተወሰነ ጊዜ ለስርጭቱ ለመስጠት ተብሎ ከዚህ የአዋጁ ነጋሪ መልእክት ከወጣ ጀምሮ ከሁለት ወር ያላነሰ ጊዜ የተሰጠህ ሲሆን ፤ መፅናት የሚጀምረው የያዝነው ዓመት ዓብይ ፆም አልቆ የትንሳኤን ፍቼ እንደዋልክ ከሚያዚያ ሰባት ቀን ሁለት ሺ ሰባት ዓመተ ምሕረት ጀምሮ የፀና ይሆናል ። ከዚህ እለት በኋላ ከማናቸውም ጊዜና ሰአት ጀምሮ በአገራችን በኢትዮጵያ ውስጥ ያለውንም ሆነ በመላው ዓለምም የሰፈነውን የጨለማው ዓለምና ዝግንትሉን መጥረግና ማፅዳት ይጀምራል።

የዓለም የጥፋት ተከሎች የሊባኖስ ዛፎች አድገው ያረጁባት የገረጀፉባት መሆኗን ሁሉም ተዋናዩ የሰው ልጅ ሁሉ ያውቀዋል ። ድንጋጤህ ብርቱና አማትቋቋመውም ሊሆን ይችላል ። ዓይንህ እያየ ጆሮህም እየሰማ ፤ ትላንት የምታውቃቸው ምኞትህ ተሳከቶልህ ሄደህ የኖርከባቸው የጎበኘኻቸው የተማርከባቸው አገሮች ከተሞች በእርግጥ ነበሩ ወይ ተፈጥረውስ ነበር ወይ እስከምትል ድረስ አሻራና ምልክት ሳይተውላቸው በታላቅ ቁጣ ይጠረጋሉ ። ዛሬ ከዚህ አዋጅ መውጣት በሁዋላ ምንም ዓይነት የቅጣት ደረጃና ገደብ የለም ። ሁሉም ቅጣቶች ማናቸውንም የዲያብሎስ ሥራና ምልክቶች ፍፁም ለመጥረግና ለማስወገድ በመላው ዓለም ያለምንም እውከታ ይዘምታሉ ። ምልክት አልባ የአዳም ዘር በሙሉ በጠረጋው አብሮ ይጠረጋል በእሳቱም ይበላል ።

ታላላቅ የሚባሉ አገሮች በሰው ደምና አጥንት የከበሩ በዲያብሎስ የተወደሱና የተሸለሙ ዛሬም ሊድሃ አገሮች እንደአምላክ ያህል የሆኑ ፤ እንደምሳሌም ብናነሳ እነባቢሎን/አሜሪካ/ ፤ እነእንግሊዝ ፤ እነቻይና፤ እነራሺያ፤ እነፈረንሳይ፤ እነጀርመን ፤ እነጃፓን ፤ እነስፔን እነፖርቱጋል እነህንድ እነስካንዲኔቪያ ሃገሮች ፤ እነካናዳ ፤ እነብራዚል ፤ እነአውስትራሊያ ፤ እነኢራን ፤ እነሳኡዲ አረቢያ እነግብፅ ፤ እነደቡብ አፍሪካ ፤ እነእስራኤል ፤ እነቱርክ ፤ እነእስትሪያ ፤ እናም ሌሎችም የነዚህኑ ፈለግና መንገድ የተከተሉና በነሱም የሚታመኑ ሁሉ አብረው ይጠረጋሉ ። አንዳንዶችም እንደአገር ነበሩ ወይ የሚል ጥያቄ እስከሚያሰነሱ ድረስ ምልክትና አሻራ ሳይተውላቸው ከምድረ ገፅ ፍፁም ይጠፋሉ።

በተለይ ለዲያብሎስ ዋናው ተጠሪና ፈፃሚ ሆነው በግንባር ቀደምትነት ዲያብሎስ በኢትዮጵያ ላይ ያዘመታቸው አገሮች እንግሊዝን አሜሪካንን ቻይናን ሕንድን ጀርመንን የመሳሰሉ አገሮች ፍጹም ኢትዮጵያን በማጥፋት ሥራ ላይ የተሰማሩ ናቸው ። በመላው ኢትዮጵያ የተቀናጀ ዘመቻን ከሚያከናውኑ እምነቶች ባብዛኛው ዓለም አቀፋዊ ጉልበት ካላቸው እነካቶሊክ ፤ እነፕሮቴስታንት/መናፍቃን/ እነ ዓለም አቀፍ እስልምና እና ሌሎችም ባላቸው አቅምና ጉልበት ሁሉ በመዝመት ቤተ ክርስቲያናችን የኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያንን በመውረር ፍፁም ሽባና የማትላወስ አደርገዋታል ። አሁን እምነቱ ያለው በሕዝበ ክርስቲያኑ /ምእመኑ / ልብ ውስጥ በመሆኑ ሊያጠፏት አልተቻላቸውም። ይህ ደግሞ የእግዚአብሔር ድንቅ ሥራ ነው ። አገሊጋዩ በቁሙ ሞቶ በቁጥር ቢያንሱም ውስን ምእመናንና በየበረሃው የወደቁ አባቶች ፍፁም ፀንተው የቆሙ በመሆናቸው ለዲያብሎስ የጉሮሮ አጥንት ሆኖቢታል።

የቀደሙት መልእክቶች እንደነገሩህ ዛሬ መደምደሚያህ ሰዓት ላይ ደርሰሃል። የልኡል ውሳኔ እስካሁን ምድርን ያላነደደው ብትመለስ ብትፀፀት ተብሎ ቢሆንም አንተ ግን የበለጠ የሃጢያትና የጥፋት ማምረቻ የጨለማ ሥራን

•ማዘመኛ ዕንዲሁም የእግዚአብሔርን ቅን ሕዝቦች ፍፁም ማጥፊያ አደረግኸው ። በሰጠህ ጊዜ እግዚአብሔር እንዲፀፀት ሆኖአል።

ለዚህም ነው ዛሬ ለዓለም ሁሉ ጣእት የሆኑ የልኡልን ክብርና መመለክ ለራሳቸው ያደረጉ ሁሉ ምን ትልቅ ቢሆኑ ከምድረ - ገፅ እንዲጠፉ የታዘዘው ።

በመላው ዓለም ታላላቅ መንግሥታት የተባሉ ነገር ግን ፍፁም የዲያብሎስ አገዛዝና መጽሐፈ - ጽልመትን ያነገሱና በሱም እየተመሩ ያሉ የሚያመልኩትም ምን ምክንያት ሊሰጡ ይቻላቸዋል ? ምለው ተገዝተው ለዲያብሎስና ለፈቃዱ ተገዝተው ሊኖሩ ወስነው ረጅም እድሜን አስቆጥረዋል። ልኡልን ያስቀኑትም ዘንድ ለልጅ ልጆቻቸው ከህደትን ዲያብሎስን እንደትክክል እምነት ሲያወራርሱ ኖረዋል። በሱም በመፅናት በማናቸውም የዓለም ገፅታና ፊት ሕጉን አፍርሰው ስርአቱንና ፈቃዱን አቃለውና ንቀው በምትኩ የዲያብሎስን ድርሰት አፅንተዋል።

ደፋሮቹና በንቀትና በትእቢት የተሞሉት በአገኙትና በጨበጡት ዲያብሎሳዊ እውቀት ፍፁም ታምነው የጥፋት አዝመራን ሲያዘምሩ ይውላሉ ያድራሉ ። ልኡል በፀባኦት በመንበሩ ሆኖ ይስቅባቸዋል። ቀናቸው ማለቅና መቆረጡን ስለሚያውቀው ። ዛሬ ታላላቅ ተራሮች ናቸው ፤ ነገ ግን አቧራና ብናኝ ትቢያ ናቸው ። ከምድር ትቢያ የተፈጠረ በከበ

ረው መንፈስ ላይ ሲታበይ ፤ እንዳልነበረም አድርጎ ፍፁም ሲከድ ከዚህ በላይ ምን ዓይነት ወንጀል ሊወዳደረው ይችላል ? ልኡል ቅን ፈራጅ ! እውነተኛ ዳኛ ነው ። በፍርዱ ሕፀፅ የለም ኖሮም አያውቅም ። ልኡል ባህሪው ፍፁም እውነት ብቻ ነው ። ሁሉ በራሱ የተፈጠረ ስለክብሩም ይሆን ዘንድ የሚኖር ነው ።

ማናቸውም ፍጥረቶች በልኡል ትእዛዝና ፈቃዱ ላይ አንድም ጊዜ ወጥተው ከመንገዱም ስተው አያውቁም ። ሁሉም በተሰጣቸው ስርአትና ህግ የሚጓዙ ናቸው። ሰው ግን ፍፁም ሕግና ትእዛዙን በመናቅና በማፍረስ ተዋዳዳሪ አልተገኘለትም። እንዲያም ሆኖ ችሩ አምላክ ትእግሥትን ምን ያህል ገንዘቡ እንደሆነ ዛሬ እኛ ባሮቹ እየመሰከርን ነው ። እራሱም ፍቅር መሆኑን ለሰው ልጅ በመታገሥ ብቻ ሳይሆን እስከሞት በመውደድና ፍቅሩንም እስከ መቃብር በመውረድ አሳይቶናል። ታዲያ ይህን ያወቁ ልጆቹ በአመፀኞች ሲፈጩ ሲቆሉ ልኡልን ስለትእግስቱ ቢደንቃቸውም በዛው ልክ ደግሞ ዳኝነቱን ፍትህን እንዲሁም ንፁህ ደማቸውን በቅን ፍርዱ እንዲያካትት ዘወትር በእንባና በጩኸት ከመጠየቅ በርከው አያውቁም።

የትንሳኤው ዘመንም የቅን ፍርዱና የፍፁም ዳኝነቱ ውጤት ነው ። ለዚህ መድረስ የተገባቸው ባሮቹ ደግሞ ቀድሞም በሱ ዘንድ የታሰቡ ናቸው። ስለሆነም ዛሬ ባሮቹን ሊክስ ሊባርክ ፤ ወንጀለኞችንና በደለኞችን ወደ ሲኦል ሊልክ ዛሬ በሙላት መጣ! መድሃኒዓለም አባታችን እናቱንና እናታችንን ቅድስተ ቅዱሳን ድንግልን አስከትሎ በቅዱሳን ሊቃነ መላእክት ታጅቦ ፍርድን እንደ ፀሐይ ሊያወጣ እነሆ ደረሰ!

እኔም አንድ ምናምንቴ ባሪያው ዛሬ የሰማኸውን አዋጅና አዋጅ ነጋሪውን መልእክት እንዲሁም ለዘጠኝ ዓመታት ስትሰማና ሲታደምጥ የቆየኸውን 5 መልእክቶች ሁሉ ላንተ ለሰው ዘር አስተላልፍና እነግር ዘንድ የተሰጠኝን ትእዘዝ በአቅሜ ልክ ልኡል እንደሰጠኝ ጉልበት መጠን ላደርስልህ ጥሬአለሁ ለእንደኔ አይነቱ ደካማና ታናሽ ባሪያው ይህንን የከበደ ሃላፊነቱን ቢጭንብኝም በራሱ አከናውኖታል ብዬ አምናለሁ ። ስሙ የተመሰገነ ይሁን ።

እንግዲህ ከአዋጁ መውጣት በኋላ መጪው ጊዜ እጅግ አስጨናቂ እንደሚሆን ይታመናል። በልኡል ታምናችሁና ተወዳችሁ በእንባችሁ ዘርታችሁ በደስታ ልታጭዱ የተገባችሁ ስለሆነ ከታመናችሁለት አምላክ የተሰጠ እድል ስለሆነ በውጣ ውረዱ የሚያስጨንቃችሁ ነገር የለም። ምልክት እልባ የሆኑት ደግሞ በደስታ ዘርተዋል ፍሬውንም በልተው በአመፅ ትርፋቸው ተደስተው ኑረዋል ዛሬ ደግሞ በዚህ የልኡል ቅን ፍርድ ሊካተቱ ግድ ስለሆነ በእንባ ጥርስ በማፋጨት በሽሽት በመፍረስ በመሞት በመጠረግ በእሳት በተለያዩ መቅሰፍቶች ሊከደኑ ግድ ስለሆነ ትርፋቸውን ማፈስ ይገባቸዋል።

አዋጁ እራሱን ለማፅናት ብዙ እርምጃዎችን ስለሚወስድ በፊቱ እሳትን የለበሱ የእሳት ትንታግና ማእበል የሆኑ እንዳች ሃይል የማይቋቋማቸው ቅዱሳን መላእከትና ፤ ቀሳፊ መላእክት እንዲሁም ከልኡል ሃይልን የተላበሱ ምርጥ እቃዎቹ በተጣመር ለእርምጃው ይዘልቃሉ ።

አዋጁ ከኢትዮጵያ መነሻውን አድርጎ በሽግግሩ ሂደት ውስጥ የሚነቀለውን የሚጠረገውን የሚፈርሰውን ሁሉ ከነዝግንትሉ በማስወገድ በአኳያውም የሚተከለውን በመትከል የሚስተካከለውን በማስተካከል ብርሃናዊውን ዓለም በማዋለድ የሽግግር ጊዜ ሕግጋትን በመጠቀምና በማፅናት በኢትዮጵያ ብርሃናዊውን አገዛዝና የልኡል ሥርዐት በፀና መሰረት ላይ መትከል አለበት። በሂደት በአዋጁ እንደተመለከተው ለዋናው ሕግጋተ - ሥላሴ ጥርጊያውን በመፈፀምና

ብማስተከከል ቀናውንና የትንሳኤውን ዘመን ማልዶ መውጣትን በማስረገጥ አስረከቦ የሽግግሩ ጊዜ ሕግጋት ሥራቸውን ይጨርሳሉ :: ይህ ሂደት በሌሎችም የአለም ገፅታዎች እንደልኡል ፈቃድና ትእዛዝ ተፈፃሚ ይሆናሉ::

የኢትዮጵያ ሃገራችን ወቅታዊ ሁኔታ !

ዛሬ ሀገራችን ኢትዮጵያ በብርቱ ፈተና ውስጥ እንዳለች ሁሉም ስለሚያውቀው እንግዳ የሆኑትን ሁኔታዎች እንመለከታለን :: ዓለም የሚደመምበት ፍፁም የአውሬን ባህርይ የተላበሰ ገዢ ኢትዮጵያን ቀይዶ ይዞአታል:: የሰው ሕይወት ፍፁም ዋጋ አጥቶአል :: ሰው ይኖር ዘንድ የሚያስፈልጉት መሰረታዊ ፍላጎቶቹ ፤ እንደ መጠለያ ፤ እንደ ምግብ/ ሥራ/ ፤ ልብስ እነዚህ አንድ ሰው ይኖር ዘንድ የሚያስፈልጉት መሰረታዊ ፍላጎቶቹና በአለው መንግሥት ይሟሉለት ዘንድ የሚገባ ግዴታዎች ናቸው:: ይህንን ያልተወጣ መንግሥት በምንም መስፈርት መንግሥት ነው ለማለት አይቻልም ::

በዚህ መነሻነት ኢትዮጵያ ውስጥ ያለው ሁኔታ ፍፁም የተቃረነ ነው :: በመላው አገሪቱ ያለው ሕዝብ በጣት ከተቆጠሩ የአንድ መንደር ልጆች በስተቀር በረሃብ ፤ በሥራ ማጣት ፤ በበሽታ ፤ በስደት ፤ በመኖሪያ እጦት ፤ በዘር ልዩነትና ግጭት ታይቶም ተሰምቶም በማይታወቅ የኑሮ ውድነት ፤ በተለይ የተዋህዶ እምነት በመከተላቸው በአማራ ዘርነታቸው ተለይተው መንግሥት በሚያቀናብረው ጥቃት የተሙት የሞቱ የተጠረጉ ቤታቸው ንብረታቸው የፈረሰባቸው የተወረሰባቸው ፤ በልማት ስም ከዋናው ከተማም ሆነ ከገጠሩም ቤታቸው ንብረታቸው መሬታቸው የተነጠቁ የተባረሩ ቤታቸው ይቁጠራቸውና በፍርደ ገምድል ፍርድ በየወሕኒ ቤቱ የተጣሉ እነዚህ ሁሉ በኢትዮጵያ የነገሱ ስር የሰደዱ ችግሮች ናቸው::

ያለው መንግስት እንደመንግሥት የማያስብ ፤ ስለዜጎች ምንም የማይገደው በአንድ መንደር ስሜት አእምሮው የተሸፈነ በመሆኑ ከእነዚህ ምንም የሚገኝ ትርፍ እንደሌለ ሁሉም የተረዳው ይመስለኛል:: በሁሉም የሕይወት ገፅታ የኢትዮጵያ ሕዝብም ሆነ የመላው ዓለም ሕብረተሰብ ቢታላቅ ቀውስ ውስጥ መውደቁን ሁሉም ያወቀው እውነት ሆኖአል :: መፍቻ የጠፋለት የምናየውና እያለፍን ያለንበት መከራ ብርቱ እሳት ሆኖ እየበላ ነው :: በኑሮ ውድነት እሳት ፤ በበሽታ እሳት በሰላም ማጣት እሳት በመኖሪያ ማጣት እሳት በስደት እሳት ሌሎችም እሳቶች ቁጥራቸው የበዛ ሰውን እንደእሻሮ እየቆሉት ነው::

ይህ ሁሉ የሆነው የቀደሙት መልእክቶች እንደነገሩህ ደረጃ በደረጃ የቅጣት ማእበሉና እሳቱ እየጨመረ ይሄዳል እንጂ አይቀንስም :: ይህ እንደማይሆን ደግሞ ሁሉም መልእክቶች አረጋግጠውልሃል :: ከደረጃ አንድ ተነስቶ በሰባት እጥፍ እየተባዛ እሳቱ ይጨምራል እንጂ የዛሬ ገዢዎች /በመላው ዓለም ያሉ ሁሉ/ እንደሚሉት ባለን እውቀት ጉልበት ገንዘብ ሃብትና ዘዴዎች ሁሉ ተጠቅመን እንቋቋማዋለን በማለት ፤ ዓለምን ከድኖ በያዘው ሚዲያና ፕሬሳቸው እንዲሁም ፕሮፓጋንዳቸው ሲለፍፉ ይውላሉ ያድራሉ :: ዛሬ ማንም የማይክደው እውነት አለ :: በመላው ዓለም ያለው ሕብረተሰብ የቁርስና የምሳው ያህል ወሬንም ከገዢዎቹ እንዲፈስለት የሚወድና የለመደም ነው::

የልኡል ቅጣት ለምን በረታ የሚል ጥያቄ መነሳቱ አይቀርም :: ለዚህ ከሚጠቀሱ ምክንያቶች ጥቂቱን ብናነሳ : —

በመጀመሪያ የሚወርደው እሳት የልኡልን ልጆች /ወርቅ/ በእሳት በተደጋጋሚ እንደሚቀቀልና እንደሚጠበስ እነሱንም በእሳቱ ውስጥ ዕየነጠሩ እንዲወጡ ለማድረግ ታስቦ ዕየተፈፀመ ያለ ነው:: ብርቱና የማይበገሩ እንዲሆኑ ለማድረግ ስለሚያስፈልግ! ለመጪው የትንሳኤው ዘመን የበረቱና በተዋህዶ እምነታቸው የፀኑ ሃላፊነትን በቅንነትና በታማኝነት ሊወጡ የሚችሉ አገልጋዮችን ለማነፅም ነው:: የልኡል ዩኒቨርሲቲና ትምህርት አሰጣጡ የሚከናወነው እንደሥጋው ዓለም በአንድ ቤት ውስጥ በወንበር ላይ ተቀምጦ ከፊትም አንድ መምህር ተሰድሮ በሚሰጠው አንድና ሁለት ሲደመር ሲቀነስ በሚል አይደለም:: የእግዚአብሔር ትምህርት ቤት ከጥቃቅኗ የእለት ከእለት የኑሮ ውጣ ውረዳችን ጀምሮ እስከ ትልቁ ፈታኝ የሕይወት መቸገር መራብ መጠማት መሳደድ መታሰር መፈተን የሚጨምር ነው:: ዩኒቨርሲቲው እንዲህ ነው :: በዚህ እሳት እየለበለበና ዕየጠበሰ ወርቁን የተዋህዶ አርበኛ ያወጣል :: የብቃት ማረጋገጫው የሚሠጠው ምድርና ሰማይን ከዘረጋው የሰራዊት ጌታ እጅ ሲሆን የፍቅር ማረጋገጫዋን የምትሰጠው ደግሞ ድንግል ናት አቅራቢዎቹ ደግሞ ሊቃነ መላእከቱ እነሚካኤል እነገብርኤል ናቸው::

የዚች ዓለም የትምህርት ቅኝት ለሥጋው ለሥጋው የሚል ነው:: የእግዚአብሔር ትምህርት ቤት ግን መንፈሳዊነት ይቅደም ሥጋ ለመንፈስ ይገዛ የሚል ነው::

ሁለተኛውና የማያቋርጠው እሳት ደግሞ፤እምቢ ብለው በእሳቱ እየተለበለቡ መፍቻ ዘዴ ሲያጡ በግድ ተሰንገው የጠፉበትን መንገድ ተረድተው ወደ እውነተኛይቱ እምነታቸው እንዲመለሱ የሚያደርግ ነው::

፣ በሦስተኛው ምክንያት እሳቱ የሚለበልባቸው ደግሞ እነዚህ የማይመለሱ ሁሌም ከዲያብሎስ መዝገብ /መፅሐፈ-ጽልመት/ መፍትሄ የሚሹ በመሆናቸው ፤ እየሞቱም ከከደናቸው የጨለማ መንገዳቸው ስለማይመለሱ በዚያው ያከትማሉ፡፡

ቤተ ክርስቲያን ፤ የተዋህዶ ቤታችን ፍፁም በዲያብሎስ ተወራለች፡፡ በውስጧም ለዲያብሎስ አገልጋይ የሆኑ ወርሰዋታል፡፡ ሁሉም አንዱ ቅባት ሌላው ፀጋ አንዱ ደግሞ ተሃድሶ ፤ እንዲሁም መናፍቅ ፤ ካቶሊክ በሚል ዶግማ ወጥረው ይዘዋታል፡፡ ሁሉም መለያቸው ደግሞ አንድ ለአምስት በሚል የዲያብሎስ አገልጋይ መንግሥት ባዘጋጀው መረብ የተተበተቡ መሆናቸው ነው ፡፡ የመንግሥት ተብዬው አባል ያልሆነ የለም ቢባል ይቀላል፡፡ መጪው ጠረጋ የሚከብደው ሂያጁ ስለሚበዛ ነው፡፡ ተራራው እጅግ ጥቂት ነው የሚባለውም ያለምክንያት አይደለም፡፡

ዛሬ በቤተ ክርስቲያን የሚሳተፉ ሊያውቁት የሚገባው ቢኖር ቅዳሴው ማሕሌቱ ኪዳኑ ሁሉ ከቤተ ክርስቲያኑ ጣሪያ እንደማያልፍ ነው፡፡ ሊያውቁት ይገባልና እንዲያስተውሉ ይመከራሉ ፡፡ ምክንያቱ ሺ ጊዜ ተነግሯል፡፡ አልሰማ ላለ ሲያይና ሲሰማ ቅበረው እንደሚባለው ተረት ይሆንባቸዋል ፡፡ በቤተ እምነታችን ውስጥ የተሰገሰጉት የዲያብሎስ ተጠዋሪዎች ጌታን ሰቅለው ቁስሉን የሚወጉ ናቸው፡፡ ጨለማ ከብርሃን ጋር ምን ሕብረት አለው ዛሬ መስዋእታቸውን ከዲያብሎስ አገልጋዮች ጋር ቀላቅለው መስዋእት አቀረብን እስቀደስን የሚሉ ሁሉ ጌታን ከአመፀኞች ጋር ሰቅለው ቁስሉን የሚወጉ እንደሆኑ ይወቁ ! በግላቸው እንደኤሊያስ መስዋእታቸውን ማቅረብ ይችላሉ፡፡ ለዲያብሎስ እጅ ከሰጡ ጋር ከሱም ፍርፋሪ ከሚለቅሙ ጋር የፖለቲካው ታማኝ ከሆኑ ዲያቆናትና ቀሳውስት ጋር አብሮ የሚደረግ ፀሎት ማረፊያው ከዲያብሎስ እጅ ነው፡፡ ስለዚህ ቤተ ክርስቲያን ስትሄዱ በግል የግል ፀሎታችሁን አድርሱ አሊያም ሰላም ለኪ እምዬ ቤተ ክርስቲያን እምሳለ እየናሳሌም ብላችሁ ተሳልማችሁ ተሰማሩ! በቂ ነው፡፡ አንድ ምሳሌ እንውሰድ

የብርሃን ሠራዊት የሆኑ ለውጊያ የተዘጋጁ በስተቀኝ ግንባር ሲሰለፉ በስተግራ ግንባር ደግሞ የጨለማ ሰራዊቶች ተሰልፈዋል፡፡ በሁለቱ መሃል የተተወ የፈሪ ምድር የሚሉት ሥፍራ አለ ፤ በሁለቱ ሀይላት አንፃር ድጋፍ የሚሰጡ ወይም የሚተባበሩ ስፍራቸውን ከየሚደግፉት ሰራዊት ጎን ቆመው ውጤቱን ይጠባበቃሉ ፡፡ አንድ እንግዳ ነገር በፈሪው ምድር ላይ ይታያል ፡፡ ውስን ቁጥር ያላቸው ሰዎች በዚያ በተተወ ምድር ላይ ወደ ሥራቸው ይሄዳሉ ውለውም በዚያው ይመለሳሉ፡፡ በማናቸውም ሰአት ውጊያ በሚነሳበት የውጊያ ወረዳ ላይ የሰላም ቀጠና ሳይሆን በነዚህ ሰዎች ግን ምንም የማይከሰትበት ምድር ነው ብለው ያምናሉ፡፡ ውጊያው ሲነሳ ግን ከማንም በላይ አደጋው ውስጥ የሚወድቁ እነዚህ የዋሃን አለአስተዋዮች ናቸው፡፡ ዛሬ በቤተ ክርስቲያን ለቅዳሴውም ለኪዳኑም ማልደው የሚገኙ ሰዎች በቅንነት የሚያደርጉት ቢሆንም ከዚህ አዋጅ መውጣት በኋላ ከሥፍራው ራሳቸውን ቢያርቁና የግል ፀሎታቸውን በቤታቸው ቢያደረጉ መልካም እንደሆነ ይመከራሉ ፡፡

የእግዚአብሔር እርምጃ የሚጀምረው ከቤቱ መሆኑን ሁሉም ሊያስተውለው ይገባል፡፡ በተለየ ሴቶች እናቶች ቤተ ክርስቲያን የሚሄዱት የእልልታ ጥማታቸውን ለማርካት ይመስላል ፡፡ የዲያብሎስ ጭፍሮች ገንዘብ ሲሰበስቡ እከሌ በዚህ ምክንያት ይህን ያህል ብር ሰጠ እልል በሉ! እልል ! ቤተ ክርስቲያንን አፍርሰን ልንሰራ ነው እልል! ወዘተ የእልልታ ሰራዊት እስነዋሪ ትውልድ የጠፋ ሰው ልንል እንችላለን ፡፡

ታላላቅ ገዳማትን አፍርሰው አባቶችን ደብድበው አስደብድበው ገለው አሳስረው እንደዋልድባ የመሳሰሉትን ገዳማት አፍርሰው ዛሬ ደግሞ እልል በሉ ሲሏችሁ እልል እምትሉ ቤተ ክርስቲያንን አስፈርሰው የተጉ አባቶችን ደብድበውና ገለው አስረው የመጨረሻ የተዋህዶ አባቶች መካተቻና ወደ ፈጣሪ መሰብሰቢያ የሆኑትን ገዳማት ፍፁም አፍርሰው እነዚህ በነገሱበት ቤተ እምነት አብረው እንቀድሳለን እናስቀድሳለን የሚሉ ስለእውነተኛይቱ ተዋህዶ የሞቱትን የተጋዙትን የታሰሩትን ንቆ ለከሃዲው እምነት እልባው የአምልኮ ባእድ እምላኪው ከቆሙ የቡኤል ዘቡኤል የዘመኑ ካህናት ጋር መሰለፍና አብሮ መስዋእት ማቅረብ ለማን ክብር ነው? ለዲያብሎስ ብቻ ነው፡፡ በቤተ ክርስቲያን የሰለላ መዋቅር ዘርግቼ በሚገባ እየተቆጣጠርሁ ነው የሚለው ስሙን እንኳን ማንሳት የሚቀፍ ዲያብሎሳዊው መንግሥት ለዚህ ካደሩለት ሰራዊቶቹ ጋር መሰለፍ ማለት ምን ማለት ነው? በቃ! ከሥፈራው እንዳትገኙ አስጠነቅቅሃለሁ ፡፡

የዚህ ጉደኛ የኢትዮጵያ መንግሥት ተብዬ አባል የሆናችሁ ከማናቸውም ጥቅማችሁ ወይም ጭፍን ስሜት ተነስታችሁ የምትደግፉት በዘረኝነት የተተበተባችሁ በተለያየ ዲያብሎስ በደረሰውና በፈጠረው እምነት ውስጥ ያላችሁ ሁሉ መጥረጊያው የማያልፋችሁ መሆኑን ላስገነዝባችሁ እወድዳለሁ፡፡ አይቀሬ መሆኑንም አረጋግጥላችኋለሁ፡፡

ኢትዮጵያና ተሰዳጅ ወገኖቻችንን ስናስብ ደግሞ እጅግ የሚያም ውርደት ሆነ!— በዛሬው ወቅት በተለይ በሳኡዲ አረቢያ በወገኖቻችን ላይ የተፈፀመው ግፍና በደል ማንም ኢትዮጵያዊ እጅግ የሚያመው እንደሆነ በግልፅ አይተናል፡፡

ተዘዋዎቹ ወገኖቻችን በአሁኑ ወቅት በሳኡዲ ብቻ ሳይሆን በሌሎችም ሃገሮች በተለይም በአረብ ሃገራት ሃበሻ ጠላታችን ነው ብለው የሚሰሩት ግፍ ወሰን አጥቶአል። ዓለም በየትኛውም ሥፍራ የሃበሻን መበተን መስካሪ ናት። ይሁንና እንደ ከፉ ጠላት/እንደ እባብ/ መቀጥቀጥ በምን ምክንያት ይታለፋል በምንም አይታለፍም። እዚሁ ላይ ላረጋግጥላችሁ የምወድደው በሺ እጥፍ ዋጋ ትከፍሉበታላችሁ። ይህ ፍፁም የማይቀር ነው። የልኡል ባሪያ ይሆን ተናግሬአችኋለሁ።

የእግዚአብሔር ባሮች ይሆን ሁሉ ግፍ በየባኢታቸው ሆነው በቁጭት እያዩት ነው ። መንስኤው በኛ እምነት ምሽግና መጠለያ የምትሆናቸውን አንዲቷን የተዋህዶ እምነት ጥለው ከሥጋ ገበያ መፍትሄ ሲፈልጉ የተጎዱ መሆናቸው ግልፅና የማሻማ እውነት ነው።

በኢትዮጵያዊነት ላይ በተዋህዶ እምነት ላይ የዘመታችሁ የዓረብ ሃገራት ሁሉ ፤ እናንተም ፤ በመላው ዓለም ያለውም የዘመኑ ትውልድ ሃበሻን /ኢትዮጵያዊ /ተዋህዶ ኦርቶዶክስ እምነትን ባነሱ ቁጥር ፤ እጅግ እንደሚጠሉን እናውቃለን ። ግን ዛሬ ልናበስራችሁ እንወዳለን መጪው ዘመን የእኛ መሆኑን በመቃብራችሁ ላይ ታላቂቱ ኢትዮጵያና ተዋህዶ እምነቷ በመላው ዓለምም ፀንቶ እንደሚቆም እወቁ! አዋጁም ይህንኑ ሊያበስርና ሊገልፅ የታወጀውንም ሕግጋት ሊያፀና እጅግ ብዙዎች ጠላቶቻችን ከምድረ ገጽ ሊጠራርግ በታላቅ የእሳት ማእበልና ኀርፍ ተጭኖ መጥቶልሃል። ማምለጫ የለም መሸሻ መደበቂያ በምድር ላይ የለም። በተለያዩ የአፍሪካ ሃገራትም ተመሳሳይ ግፍ ይፈፀማል ። እንደነጂቡቲ እንደነሱዳን እንደነኬንያ የመሳሰሉ ሃገራት ኢትዮጵያዊውን እንደውሻ በሙቁጠር ባለበት በደረሰበት እያነቁ ለሚገለው መንግሥት ሲሰጡትና ሲያጠፉት እያየን ነው ። እናንተም ከለው ዲያብሎሳዊ የኢትዮጵያ መንግስት ጋር አብራችኋልና አብራችሁ ትከደናላችሁ። ትጠረጋላችሁም! ይህ ሁሉ በደል ሲፈፀም ከምንም ያልቆጠረው የኢትዮጵያ መንግሥት ተብዬው በየበረሃ ለወደቁት በባሕር ለሰጠሙት በአረብ ሀገራትና በአፍሪካ ሀገራት በእኖራለሁ ጥረት ወጥተው ለቀሩት ሁሉ ሙሉ ሃላፊነትዋን ይወስዳታል። እነሱ በእመፅ አልፈዋል። የቆመው መንግሥትና ከጀርባው ሆነው ሁሉን እቀፍ ድጋፍ ያደረጉለት እያደረጉለትም ያሉ አለም አቀፍ የኢትዮጵያና የኢትዮጵያዊነት የተዋህዶ እምነታችን ጠላቶች ሁሉ ልብ በሉ ልብም አድርጉ እስከዛሬ የሰፈራችኋት ግፍና በደል በሺ ዕጥፍ ትከፍሏታላችሁ የልኡል ባሪያ ይህንን አረጋግጥላችኋለሁ። ቃል ወጥቶአል ተፈፃሚነቱ እንዳይቀር ደግሜ በልኡል ሥም አረጋግጥላችኋለሁ።

ኢትዮጵያ ውስጥ ያሉ ሰላማዊ ተቃዋሚዎችና ጦር የጨበጡ ተቀዋሚዎች ሁሉም በድምሩ ያለውን መንግሥት ሊጥሉ እየደከሙ ለመሆናቸው እየሰማን ነው። በዓላማቸው ዲሞክራሲን እናሰፍናለን የሚሉ ናቸው። ይህ ፍልስፍና ከእውነተኛው የተዋህዶ እምነታችን ጋር ፍጹም የማይገናኝና የሚፃረር ነው። ዲያብሎስ ያረቀቀው ይህ ድርሰቱ ሁሉም ሃይማኖቶች እኩል ናቸው የሚል አባበል ያለው ሲሆን ሰዶምነትንም እንደመብት ከሚቆጥሩት ምእራባውያን ጋር የተመሳሰለ ነው። ብዙ ቅኖች በዚህ ውስጥ ተሰላፊ ሆነዋል። ለኢትዮጵያ አገራቸው ያላቸውን ቀናኢነት ስለሁሉም ተቃዋሚዎች አከብሮት ቢኖረንም በተለይ በሰላማዊ ትግል የተሰለፉት ውስጥ የሚበዙ ሆድ አደሮች እንደሞሉበት የሚታወቅ ነው ። ዛሬም በሕዝብ መከራ የሚነግዱ ከለየለት እውሬው ፐ.ቢ ቡድን ጋር በሕዝብ ደም የሚነግዱ ሁሉ ማረፊያቸው ቀሰብ ከሚሰፍርላቸው መንግሥት ተብዬ እንደማይለይ ሊያውቁት ይገባል። ሌሎች ደግሞ በበረሃ ጠመንጃ ተሸክመው ሕይወታቸውን ሊሰው ለወደዱት ስለወገንና አገራቸው ኢትዮጵያ ያላቸውን ፍቅር ብናከብርም የሁሉም ዳኛ ልኡል እግዚአብሄር ለሁሉም እንደመንገዱና እንደቅን ልቡናው ስለሚፈርድ የሚያምናቸውን የወደዳቸውን ያከበራቸውን ልጆቹን ሲያነግሥ ሁሉም በየእጣ ክፍሉ ይቆማል። በዚህ ጉዳይ ከዚህ የዘለለ ሊባል የሚችል ነገር የለም ሁሉንም የሚለየው የልኡል ቅን ፍርድ ብቻ ስለሆነ!

ልኡል እንዲህ ብሎአል፦— በአንዲት ከተማ እግዚአብሔርን የማይፈራ ሰውንም የማያፍር አንድ ዳኛ ነበረ። በዚያችም ከተማ አንዲት መበለት ነበረች ። ወደ እርሱም እየመጣች ከባላጋራዬ ፍረድልኝ ትለው ነበር ፤ አያሌ ቀንም አልወደደም ከዚህ በኋላ ግን በልቡ ምንም እግዚአብሔርን ባልፈራ ሰውንም ባላፍር ይህች መበለት ስለምታደከመኝ ፤ ሁልግዜም እየመጣች እንዳታውከኝ እፈርድላታለሁ አለ። ጌታም አለ — ዓመፀኛው ዳኛ ያለውን ስሙ ። እግዚአብሔር እንኪያስ ቀንና ሌሊት ወደ እርሱ ለሚጮሁ ለሚታገሳቸውም ምርጦቹ አይፈርድላቸውምን ? እላችኋለሁ ፈጥኖ ይፈርድላቸዋል። ነገር ግን የሰው ልጅ በመጣ ጊዜ በምድር እምነትን ያገኝ ይሆንን ?

የሉቃስ ወንጌል ም 18 ፡ 2 - 8

ከላይ የልኡልን ቃል ልብ ብላችሁ ተመልከቱ ! በዛሬው ዘመን ወንጀለኛ ዳኞች በመላው ዓለም በፍርድ ወንበር ተቀምጠው ፍርደ ገምድል ዳኝነታቸውን ሲሠጡ እንደሚውሉ እንደሚያድሩ በግልፅ እንረዳለን! እግዚአብሔርን እያምኑም አይፈሩምም ይልቅስ በወንበሩ ላይ የጎሊታቸውን የፖለቲካና ጠመንጃ የጨበጠ ባለሥልጣንን ይታዘዛሉ ያከብራሉ ። የሆዳቸው ጌታ ስለሆነ ፡ በዛሬው ዘመን በአገራችን የነገሱ ዘረኛና ፍፁም እጥፉ ገርፎች በዚች አገራችን ላይ እየሰሩ ያሉትን ግፍ የተሸከመው ሕዝብ ያውቀዋል። ይህ ሁሉ እየሆነ ደግሞ እውነተኛ የእግዚአብሔር ምርጦች እግዚአብሔርን ፍረድልን ብለው ይጮሃሉ ያባሉ ይንንም ዛሬ በአገራችን ፍንትው ብሎ የምናየው ሀቅ ነው። እነሆ መምጣቱ እውን ሆነ ። ቃዲያ በእርግጥ በእምነት ውስጥ ነኝ ብለን እራሳችንን ብንጠይቅ መልሱን እናገኛለን ። በጣት የሚቆጠሩ ብቻ በእምነታቸው እንደሚገኙ እርግጥም ነው። እነሆ በዚህ እዋጅ መታወጅ ባለድል መሆናቸው ተረጋግጦአል ። ድልን ለጨበጣችሁ እውነተኛ የልኡል ምርጦች እንኳን ደስ አላችሁ ። ከፉዎች ደግሞ መጣባችሁ ጨለመባችሁ ዳግም ላይነጋላችሁ ሆነ !

ከእንግዲህ ወዲኋላ እአምሮአችሁን እንዲያስብ አድርጉት የዘራችሁትን አመፅና ከፋት ታዩታላችሁ ፤ የታመናችሁበት ዲያብሎስ ወርውሮአችሁ ሲታላቁ እሳት ዳርጓችሁ ሄዶአል፡፡ ያመኑት ፈረስ በደንደስ እንዲጥል ፈረሳችሁ ዲያብሎስ ለእሳት ጥዶአችሁ ሄደ፡፡ በመሆኑም ከዚህ በኋላ የፍርዱ ማረፊያ ስለሚወሰን ጠብቁ! ስለፍረደ ገምድሎች አንድ ምሳሌ እናንሳ

በአንድ አገር አንድ ፍርደ ገምድል ዳኛ ነበር ይባላል፡፡ ይህ ዳኛ በመሰለው የሚፈርድ ስለሆነ በዘመኑ የሱ ፍርድ አስጨናቂና ንዑሆችን የሚጎዳ ነበር ፡፡ በሱ ፍርድ ከጉዳዩ ጋር ምንም ግንኙነት የሌላቸው ሰዎች ሲጎዱ ታይተዋል፡፡ አንድ ቀን አንድ ጉዳይ ከተሰየመበት ችሎት ደረሰ ፡፡ ጉዳዩ ሲገለፅ ከሳሽ እንዲህ ብሎ አቀረበ ፤ – ጌታው ክቡር ዳኛ እግዚአብሔር ያመልከትዎ ! ወንድሜን አንድ ጎበዝ ጉልበታም በመንገድ ጠብቆ ቀጥቅጦ ገደለው እንሆ ፍርዶን እሻለሁ የወንድሜን ደም ሕግ ይፋረድልኝ አለ ፡፡ ዳኛውም ወንጀለኛው / ነፍሰ ገዳዩ /ተይዞ እንዲመጣ አዘዘ፡፡ ተይዞም መጣ! ዳኛው እንዲህ ተብለህ ተከስሃል ብሎ ወንጀሉን ነገረው እሱም ነውረኛ ስድብ ስለሰደበኝ ደሜ ፈልቶ ገድየዋለሁ አለ ፡፡ ዳኛውም በጣፍ ገለኸዋልና በስቅላት ትቀጣለህ ብሎ ፈረደ ፡፡ መስቀያው ተዘጋጀ ወደዚያም ተወሰደ ወንጀለኛው እጅግ ረጅም ስለነበረ መስቀያውን በእንገቱ ሲያገቡ መሬት ላይ ቆሞ ከመስቀያው እኩል ሆነ ፡፡ ሰቃዮቹም ወደ ዳኛው ሄደው ከመስቀያው መርዘሙንና መሰቀል አለመቻላቸውን ገለፁለት ፤ ፍርደ ገምድሉ ዳኛ እንዲህ ብሎ አዘዘ ፡፡ የወንጀለኛውን የቅርብ ዘመድ ፈልጉ ቁመቱም አጠር ያለ ይሁን እሱን በሱ ፈንታ ስቀሉ ብሎ አዘዘ ፡፡ አንድ የከሰተበት ዘመዱ ተገኘና በአጥረቱ ምክንያት ተሰቀለ፡፡

የዘመኑ ዳኝነት ወንጀለኛውን ሳይሆን ከወንጀሉ ያልተገናኙትን ፈልጎ ማጥፋት ነው፡፡ ዛሬ በፍርደ ገምድሎች ቤቱ ያልፈረሰ ንብረቱና ገንዘቡ ያልተወረሰ የለም፡፡ በማናቸውም የአስተዳደር የዳኝነት ሂደት ውስጥ በሃሰት መክሰስ የውሸት ምስክር ማሰናዳት ያውም በራሱ በመንግሥት የሚከናወን የዘወትር ትእይንት ነው፡፡

የኢትዮጵያ አገራችን ችግር እጅግ ተበራክቶና ገዝፎ እየታየ ያለው በሁሉም ኢትዮጵያዊ ሕይወት ውስጥ ያለው የመንግሥት ችግር ፈጣሪ እጅ ነው፡፡ ፍርደ ገምድሎችን በየቦታው ሰግስጎ ያነገሰው ይህ ዲያብሎሳዊ መንግሥት ዛሬም አልተማረም፡፡ በቁጥር 4 መልእክት ማስጠንቀቂያ የደረሳቸው የቀድሞው ባለራእዩ መሪ ቅርብ አዳሪ ሆነዋል ይታረሙ ተብለው ለንስሐ ተጋብዞ ፡ ትእቢት መጥፎ ናትና በታላቅ ቁጣና ትእቢት ተሞልተው ፎከሩ ! ምን ዋጋ አለው ብዙም ሳይቆዩ ሙጥፎው እድል ገጠማቸው፡፡ የእሳቸው አባረና ተዋህዶን እያወቁ የናቁት ፓትርያርከም ተከትለው ሄዱ ለሁለቱም የደረሰው ማስጠንቀቂያ ተቀባይ ስላጣ ውሳኔው ተግባራዊ ሆነ ፡፡ ዛሬም የምናያቸው ደግሞ ከበፊቱ የከፋ ጥፋትን እየፈፀሙና እያስፈፀሙ በመሆናቸው የመጣውን ሁሉ በሃላፊነት ይሸከማሉ፡፡ ከተከሰተው አልተማሩምና!

ኢትዮጵያ ውስጥ ያለውን ጥፋት ዘርዝረን እንጨርሰውም ፡፡ በመላው ዓለም ያሉ ታላላቅ የተባሉ አገሮች በመሪያቸው ዲያብሎስ በሚገባ የተሳሉ የጥፋት መሣሪያዎቹ ስለሆኑ በምድር ላይ ያለውን መጪ የልእል ፍርድ እጅግ ስለሚፈራና ስለሚጨነቅ ሁሉንም ባሮቹን ስለአደጋወና ስለጥፋቱ ይነግራቸዋል፡፡ በተቻላቸው መጪውን ጥፋታቸውን እንዲቋቋሙ የሚያስችል ሥራ ሥሩ ይላቸዋል ፡፡ ከዚህ የጨለማው መንፈስ በመነሳት እነሱም ሲደከሙ እናያለን! ምን ምን ጥረት ያደርጋሉ እንዳንዱን እንየው

- አትዮጵያ ውስጥ ያለው መንግሥት የታመነ የዲያብሎስ አገልጋይ በመሆኑ ሁሉም መንግሥታት ትልልቆቹም ትንንሾቹም ባላቸው አቅም ሁሉ ከሥልጣኑ እንዳይወርድ እንዲያደርጉ ቀጭን የዲያብሎስ ትእዛዝ ወርዶላቸዋል፡፡ በመሆኑም ፓዝብ ብድር መሳሪያ ምክር ምንም አይነት ሕግ ሳያግዳቸው የሕዝባቸውንም ጩኸት ችል በማለት ይረዱታል፡፡ የሚቃወሙትን ተቀዋሚዎች ያሳድዱሉታል ካመቸም ይዘው ይሰጡታል፡፡ ለዚህም ነው ዛሬ በኢትዮጵያ ያለው መንግሥት በሙሉ ልብ ያሻውን የሚያደርገው ፡፡
- በመላው ዓለም ያለውን መፃኢ ሁኔታ የሚያረጋግጠውን ከልእል የታዘዘውን ለዘጠኝ አመት የተላለፈን መልእክት ከኢትዮጵያ ተነስቶ እስከ መላው ዓለም ድረስ እንዲደርስ ቢደረግም በአንዲትም የመንደር ጋዜጣም እንኳን አልተገለፀም ፡፡ ይህም የዛሬው አዋጅ ነጋሪ ሲገለፅ ከዚህ የተለየ እንደማይሆን ግልፅ ነው፡፡የሰው ልጅ ብርቱ ሞገደኛ ነው የሚባለውም በዚህ መንስኤ ነው፡፡ ምድራቱም የተሸፈኑችው በዲያብሎስ ተጠዋሪዎች መሆኑ እስከአሁን እየተደረገ ያለው ሁኔታ ያረጋግጥልናል፡፡
- በኢትዮጵያ ያሉትን በልእል የተወደዱትን እሱም የሚወዳትን ያፀናትን እምነት ተዋህዶን የጨበጡትን በማሳደድ በመግደል ታቦታቱን በመዝረፍ ፤ ቅርሳቸውን በማሸሽ ፤ ቤተ እምነታችንን ገዳማትን በማፍረስ መጠመዳቸውን የምናየው እውነት ነው፡፡ ግንም የውጪ መንግሥት ተዋህዶ እምነት ላይ ዘመቻ ሲካሄድ የተነፈሰ የለም ምክንያቱም አዝማቾቹ እራሳቸው ዓለም አቀፍ የዲያብሎስ ተቋማት በመሆናቸው ነው፡፡

ስለወቅቱ የዓለም ሁኔታ!

ዓለማችን በቀደሙት ተከታታይ አምስት መልእክቶች በመዳኘት ላይ መሆኗን እያስተዋልን ነው ፡፡ የአለማቱ ገዢዎች

መልእክቶቹ ዓለማትን ሁሉ መዳኘታቸውን እያወቁ ፤ የመጥፋታቸውን ፍርድ በመገለፁ ምክንያት በአንድም ቀዳዳ እንዳይነገር የተቻላቸውን ሁሉ አድርገዋል፡፡ በግል ብዙዎች እንዳገኙት ይታመናል፡፡ ከመልእክቱ መውጣት በኋላ ዓለማችን በየደረጃው በእሳቱ ወንፊት በመበጠር ላይ ነች ፡፡ እንደትእቢቷ መጠንም እሳቱና የእሳት ወንፊቱ በሰባት እጥፍ እየተባዛ ማድቀቃቸውንና ማከሰማቸውን ይቀጥሉበታል፡፡ ዓለም ሁሉ አሜን ብሎ እስከሚንበረከክ ድረስ!

ሽሽጉትአልሽሽጉትም መልእክቶቹ ውስጥ የተጠቀሰት ፍርድና ቅጣቶቹ በታዘዙት ጊዜና ሰአት ስራቸውን ያከናውናሉ እንጂ ከፍርድና ቅጣቱ እንዳች የሚቀር ነገር የለም።

በመልእከት ሁለት እንደተጠቀሰውና ፡ በመልእከት ሦስት እንደተመለከተው አፈፃፀም፤ ሁሉም አርምጃዎች ወረፋቸውን እየጠበቁ ይከናወናሉ። እየተከናወኑም ነው። የዓለም ሙቀት ይጨምረል እየጨመረ ነው፤ የምድር ሰሜንና ደቡብ ጫፎች ያሉ የበረዶ ግግሮች ይቀልጣሉ የውቅያኖስም ከፍታ ይጨምራል ይህም እየተፈፀመ ነው፤ በዓለም ጦርነትና ፍጅት ይነግሣል ይህም ሁላችንም የምንመሰከረው እውነት ሆኖአል። የተፈጥሮ አደጋ፤ የትራንስፖርት አደጋ የመሬት ነውጥ ፤ የሃይማኖትና የዘር ግጭትና ፍጅት ሁሉም ዕየተከናወነ ነው። በየትኛውም የዓለም ገፅታ መሪዎች ተረጋግተው በሰላም የሚገዙበት የሚወጡበት ጊዜ መጥፋቱ ከመልእከቱ መዳኘት ጀምሮ እየተከናወነ ነው ። ዓለም ከፈጣሪዋ የተጣላችና የካደች በመሆኗ እየደቀቀች ወደ ከፋው ድቀትና ሞት እየገሰገሰች ነው። አርምጃው መጠንና ሃይሉን በሰባት እጥፍ እያባዛ ያለምንም ፋታ ይቀጥላል ። ሰውና ትእቢቱ ፤ ንቀቱና ውሸቱ ፤ አብረውት ያሉት የዲያብሎስ አምልኮና ባሕርያት ሳያጠፋት እንደማይቀር እውነት ሆኖአል።ዛሬም እፊቱ ቆሞ ዓለም የጨለማ ሃይላትና ሰራዊቱንም ፍፁም ከምድረ - ገጽ ሊያስወግድ በዓለሙ ሁሉ ፊት ቆሞአል።

ዛሬ ደግሞ የግድ ጨለማው ተጠርጎ የብርሃኑ ዘመን ይተካና የእግዚአብሔር ሕዝቦችም በምድራቱ ይነግሡ ዘንድ ልኡል በገባው የማይታጠፍ ቃሉ መሰረት ተፈፃሚ ሊያደርግ ገገር የሆነውን አዋጅ እነዲታወጅ ሆኖአል።

ዓለም ምን ይበጅሃል ተመከረህ ነበር አልሰማህም ! ተቀጥተህ ነበር አልደነገጥከም! ግሳጼውም አልመለሰህም ሁሉም ጥረቶች በአንተ እንደሞኝነት ተቆጠሩ ። አልፈህ ተርፈህ ልኡልን ፍፁም ካድከ ዲያብሎስንና ትምህርቱን እነገሥህ ፤ ምን ቀረህ ምንም የቀረህ የለም ። በየደረጃው እየጨመረ የሚተምመውን ጥፋትህን ልትለማመደው ትሞከራለህ ፤ ሳይንሳዊ መፍትሄም አበጅሊታለሁ ትላለህ እንጂ ከንቀትህና ከህደትህ እንዲሁም ትእቢትህ የሚመልስህ ብልሃትም ዘዴም አልተገኘም። በስተመጨረሻ የዛሬውን መደምደሚያህ የሆነውን ውሳኔ ወለደልህ። ታከትምና ከምድራቱም ፊት ትጠረግ ዘንድ ፤ በቦታህም ብርሃን ይነግሥ ዘንድ የልኡል ፈቃድ ሆኖ እነሆ በመቃብርህ ላይ እውን እንዲሆን ታወጀ!

የዛሬውን የአለም ጥፋት በመዘከር እንጨርሰውም ፡ ሁሉም ነገር በመመሲቃቀል ላይ ሲሆን እንደተነሰነለ ልቃቂት ውልና መጨበጫው ጠፍቶአል።

አንዳንድ አገሮች ወደመጥፋት ደርሰዋል። የእመፃ ሰራዊቶች መናኸሪያ ሆነዋል። ታላላቅ የተባሉ ሃገሮች ችግር መፍታት አቅጦአቸው እራሳቸው የችግሩ አካል ሆነዋል። ዩክሬን ፤ ኢራቅ ፤ ሶሪያ ሌሎችም የሃያላን ሃገሮች የእቅም መፈታተኛ ሆነዋል። ውሾች እርስ በእርስ ቢጣሉ ጅብ እስከሚመጣ ድረስ ነው ፤ እሱ ከመጣ እጣቸው ሁሉንም የሚያጠፋ ስለሆነ በጋራ ይጮሃሉ ። በጋራም ይሸሻሉ ። የዛሬው ዓለም ታላላቅ ተብዬ ሃገራት እርስ በእርሳቸው በመፋጀት ላይ ሲሆኑ እነሱን የሚያስተሳስሩ ዓለም አቀፍ ድርጅቶች / የተባበሩት መንግሥታት ፤ የአረብ ሊግ ፤ የአፍሪካ ሕብረት/ በአባሎቻቸው አለመግባባት መወሰን አቅቶአቸዋል። መከራና መጠረጋቸው በላይ በላዩ እየተደመረ በመሄድ ላይ ሲሆን ሳያከስማቸው እንዳይመለስ እርግጥ ሆኗል ። ዛሬ እኛም የልኡል ባሮች መፈፀሚያቸው መድረሱንና መቆረጡን ልናረጋግጥላቸው እንወዳለን።

ልኡል እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስን ሌትም ቀንም ሲሰድቡትና ሲያቃልሉት የሚውሉና የሚያድሩት የዲያብሎስ ደቀመዛሙርቶች ላንዴም ለሁሌም እንዳይመለሱ ሆነው ይከደናሉ።

ከኔ ጋር ያልሆነ ይቃወመኛል፤ ከኔ ጋርም የማያከማች ይበትናል፤
ስለዚህ እላችኋለሁ ሃጢያትና ስድብ ሁሉ ለሰዎች ይሰረይላቸዋል
ነገር ግን መንፈስ ቅዱስን ለሰደበ አይሰረይለትም ፤ በሰው ልጅ ላይ
ቃል የሚናገር ሁሉ ይሰረይለታል፤ በመንፈስ ቅዱስ ላይ ግን የሚና
ገር ሁሉ በዚህ ዓለም ቢሆን ወይም በሚመጣው አይሰረይለትም።

የማቴዎስ ወንጌል ምእራፍ 12፡ 30 – 32

ቃሉም እንደሚያረጋግጥልን ዛሬ በአለማችን በልኡል ቃልና ፈቃዱ ላይ ያልዘመቱ የሉም። የውሸት ድርሰት ደርሰው በመላው ዓለም ሃሰትን ያነገሱ እምነቶችን ፈጥረው ፤ ዛሬ ዓለምን ሁሉ የሚመለከተውን የሚያስተምረውን የሚወቅሰውን እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስን መሰደባቸው አይደለምን? አዎን ነው። ስለዚህ ፍርዱን ይሸከሙታል። ሳይውል ሳያድር በሕይወታቸው ይከፍሉታል።

ባለታሪኳይ ዓለም በአሁኑ ሰዐት በቀደሙትም ሆነ እነሆ አሁን በታወጀው አዋጅ እጣ ፈንታዋ በግልፅ ተረጋግጦአል :: አዋጁ እነዚህ ለዘመናት ያለከልካይ እንዳሻቸው ሲፈነጩ መኖራቸው በግልፅ የተረጋገጠላቸውን ሽክሞች ከፊቱ ባስቀደመው መጥረጊያው ፍፁም ሊጠርጋቸው ወጥቶአል:: የተመዘዘ ሰይፍ አይመለስም :: የግድ ሊቆረጥ የሚገባውን ሁሉ ይቆራርጣል:: እንግዲህ ስለዓለም ይህን ያህል ከተረዳን ይበልጥ ደግሞ የቀደሙትን አምስት ተከታታይ መልእክቶች ደግማችሁ አስተውሉ እላለሁ :: ይህ የወጣ አዋጅ የቅጣት አይነቶቹን ሁሉ ይጠቀምባቸዋልና ! የቅጣቶች ዓይነትና ምንነት በቀደሙት መልእክቶች ተገልፀዋል :: እነዚያን ማገናዘብ ያስፈልጋል::

አዋጁ ከፀና እለት ጀምሮ በማናቸውም ሰአትና ጊዜ መጥረጊያው የፅዳት ስራውን ይጀምራል:: በመሆኑም ይህ አዋጅ ነጋሪ መልእክት በእጁ የደረሰው ሰው ሀሊናው ለተቀበለው ሰው ሊሰጥ ይችላል::

ስለድንግል ፍርድ፤

በዚህ አዋጅ ነጋሪ መልእክት ውስጥ ትሰማው ዘንድ አስፈላጊ ከሆነው አንዱ የድንግል ፍርድ ነው:: ዓለም ያለድንግል አማላጅነት አይድንም ሲባልና ይህንን ያለመታከት ለረጅም ዓመታት ሲያውጁ የነበሩና ያሉ የድንግል ልጆች እንደምናምኑቴ ተቆጥረው የሰማቸው–እንደሌለ ራሱ እያንዳንዱ በው ልቡናው ያውቀዋል::

ስለዚህ ለናትኽው ዛሬ ሰማህም አልሰማህም ትርጉም የለውም :: የተሰጠህ ዘመን በከንቱ ጨርሰኸዋል:: ይህ አወጃ ለጠበቀው ፤ ለተሰናዳው ፤ በተስፋና በእምነት ፀንቶ ለቆመው ብቻ ነው ታስቦ የመጣው::

ድንግል ለጠበቋት ልጆቿ ለታመኑባት ወዳጆቿ እንዲህ ፈርዳለች :: —— አንደኛ በዲያብሎስ በሁለመና ሕይወታችሁ እንዳትላወሱ ፤ደከማችሁ ለፍታችሁ ራሳችሁን አሸንፋችሁ ትኖሩ ዘንድ በምትወጡበት በምትወርዱበት ሁሉ በመንቀሳቀስ ድካማችሁን በመንጠቅ ከንቱ በማድረግ ባዶ እጃችሁን በመስደድ የናንተን ድካም ለሌላው ከፉው ሰው በመስጠት እንድትራቡ እንድትጠሙ የተደረጋችሁ ልጆቼ ሁሉ፤—

ሁለተኛ በተለያዩ በሽታዎችና ደዌዎች ተመትታችሁ የዲያብሎስ ማስቃያ ስለባ የሆናችሁ በአልጋ ቁራኛ በደዌ ዳኛ የተያዛችሁ ልጆቼ ሁሉ ፤ ——

ሶስተኛ በጠነከረ የተዋህዶ እምነታችሁ ፀንታችሁ በመቆማችሁ በጠላት የተጋዛችሁ የታሰራችሁ ልጆቼ ሁሉ አዋጁ ከሚፀናበት ከሚያዚያ ሰባት ሁለት ሺ ሰባት ዓመተ ምሕረት ጀምሮ በኔ በእናታችሁ ምልጃና ፍርድ በልጄም ፈቃድ ከ እስራታችሁ ከሕመማችሁ ከረሃባችሁ ተፈትታችኋል :: ለዚህ ያበቃችሁን ልኡልን አመስግኑ!!!

ወዳጆቼ ! ዛሬ አንድ ትንሽ የልኡልና የድንግል ባሪያ በሆንኩት ምስኪን ድሃ በኩል ለእናንተ ታላቁን አዋጅ እና ይህንን አዋጅ ነጋሪ ቃል ላደርስ እድል ተሰጥቶኛል:: ይህ ክብር ለኔ የተገባ አልነበረም የልኡልም የድንግልም ፈቃድ ሆንና በእንደኔ አይነቱ በደለኛ መልእክቶቹንና ዛሬም አዋጁን አበስር ዘንድ ስለተፈቀደልኝ በእደፈ እንደበቴም ቢሆን እምላኬንና እናቴን ከልብ አመሰግናለሁ:: እንተም የታደልከው ወገኔ ባለድል ሆነሃል :: ከትቢያና ከአፂራ ሊያነሳህ ልኡል ዛሬ በከበረው ስሙ ወሰነ :: ሲጠበቅ የነበረው አዋጅም እነሆ ፀና :: ዓለም እስከዛሬ በዲያብሎስ እዝ ሥር ሆነሽ የእግዚብሔርን ሕዝቦች ለረሃብ ለሞት ለስደት ለድህነት ለእስራት ለጭንቀት ለበሽታ ዳረግሽ ነበር :: በጥቅሉ ለከፉዎች ገነት ነበረሽ ለመልካሞቹ ደግሞ ሲኦል ነበርሽ:: ዛሬ እምንነግርሽ ከሕግጋተ - ሥላሴ መፅናት ጀምሮ ተሰንገሽ ለልኡል ባሮች ትገዛለሽ ይህም የልኡል ውሳኔ ነው::

የህንን አዋጅ ነጋሪ ስድስተኛ መልእክት የደረሳችሁ ከመልካሞቹም የተመደባችሁ : በልኡልም ለመልካሙ ቀን ለታተማችሁ ሁሉ አዋጁን ለምን አላገኘነውም ብላችሁ አትታወኩ ይህ የሆነው ለጥንቃቄ ነው እንጂ ልትነፈጉት አይደለም :: ይህንን መልእክት እስካገኛችሁ ድረስ ዋናውንም አዋጅ ታገኛላችሁ :: እናንተ ለበጎው ቀን የተወደዳችሁና የተመረጣችሁ ሁኑ እንጂ! ለዲያብሎስና ለተሰፈኞቹ እንዲሁም ለጨለማው ዘመን መቆየት ዛሬም ለሚደከሙና ለሚያልሙ ግን አዋጅ ነጋሪው መልእክት ቢደርሳቸውም ባይደርሳቸውም የሚጠቅማቸው አይደለም ዋናው አዋጅም ቢደርሳቸው ምን ይጠቅማቸዋል አይኖሩበት እያዩት መልካሙ ዘመን /የትንሳኤው ዘመን/ እያውቃቸውምና :: በተጨማሪም ስለጥፋታቸው ቢሰሙ አይደነግጡም የሚታመኑበት ዓለምና ዲያብሎስ ገና አብረዋቸው አሉና ! እይዞህ ባይ ገፎአቸው በመቃብር እስከሚከደኑ ድረስ እናም ከመቃብሩ አፍ ደርሰውም እንኳን ቢሆን መውረዳቸውን እስካላረጋገጠ እንደማይተዋቸውና በተስፋና በለመደው ማስሪያው ጠፍሮ ይጨርሳቸዋል:: ስለዚህ አዋጁን እያዩትም አይኖሩበትም ብርሃናዊው ዓለምም ፍፁም እያውቃቸውም ::

አቅጣጫዊ ስናጠቃልለው አዋጁ የያዘውን ጥቅል ገፅታውንና ስእሉን ስናየው በመጀመሪያ ከስተት የሚመጣው የሽግግሩ ዘመን ሲሆን በጥቅሉ መፍረስ መናድ መጠረግ መከሰም ሁሉ ይከናወናል ፡፡ ይህ እርምጃ በቁሱም በሰውም ላይ የሚፈፀም ነው፡፡ ምንም የዲያብሎስ ተከል አለመኖሩን ፍፁም መረጋገጥ አለበት፡፡

ዋናው ሕግጋተ - ሥላሴ የፀዳውን መሰረቱም ለልኡል ፈቃድና ትእዛዝ መመቸቱን የሽግግሩ - ህግጋት ካረጋገጠለት በኋላ ዋናው ሕግጋተ ሥላሴም እየተረጋገጠ ይመጣል፡፡ የጧት ጀምበር ማለዳ ከወደ ምስራቅ እንደምትዘልቅ ሁሉ ብርሃናዊው ዘመን መዝለቅ ይጀምራል፡፡

በዚያን ዘመን ይላል እግዚአብሔር ለእስራኤል ወገኖች ሁሉ አምላክ እሆናቸዋለሁ እነርሱም ሕዝብ ይሆኑኛል እግዚአብሔር እንዲህ ይላል፡— እስራኤል ማረፊያ ሊሻ በሄደ ጊዜ ከሰይፍ የተረፈው ሕዝብ ሞገስ አገኘ ፤ እግዚአብሔርም ከሩቅ ተገለጠልኝ እንዲህም አለኝ ፤ በዘለአለም ፍቅር ወድጄሻለሁ ስለዚህ በቸርነት ሳብሁሽ የእስራኤል ድንግል ሆይ እንደገና እሰራሻለሁ ፤ አንቺም ትሰሪአለሽ ፤ እንደገናም ከበሮሽን አንስተሽ ከዘፋኞች ጋር ወደ ዘፈን ትወጫለሽ እንደገናም በሰማርያ ተራሮች ላይ የወይን ቦታዎችን ትተክሊያለሽ አትክልተኞች ይተክላሉ በፍሬውም ደስ ይላቸዋል፡፡

ትንቢተ ሕዝቅኤል ም 31 ፡ 1 – 6

በመጨረሻ ይህን ልናውቅ ይገባል ፤ የምስራች ለልኡል ሕዝቦች ! ምክንያቱም ደግሞ ዛሬ ይህንን አዋጅ ነጋሪ መልእክት እንድትሰሙና ይህንንም እንድታውቁ እንድትረዱ ስለወደድሁ ነው ፡፡ እናንት የእግዚአብሔር ወዳጆች እንኳን ለዚህ ንጋት አበቃችሁ ! በልኡል ምርጫ ፤ በድንግል ምልጃና ፍቅር ተወደዳችሁ ለትንሳኤው ዘመን የሚያበቃችሁንና ባለመብትም ያደረጋችሁን የይዞታ ማረጋገጫ ሰነድ እነሆ ተሠጥቶአችኋል ፡፡ ትኖሩበት ትሰሩበት ትባረኩበት ትደሰቱበት ትወልዱና ትበዙበት ዘራችሁም ሁሉ ይባረክበት ዘንድ ፤ የልኡልም ብሩካን ካህናት አገልጋዮችና እረኞች ትሆኑ ዘንድ የተመረጣችሁበትን የምድሪቱ ወራሽ ትሆኑ ዘንድ መወደዳችሁን የሚያረጋግጠውን መለያችሁን /መታወቂያችሁን/ እነሆ ከአዋጁ መፅናት ጀምሮ ትረከባላችሁ ፡፡ ለዚህ ያበቃችሁ ልኡል የተመሰገነ ይሁን!

እነሆ መርዶ ለጥፋት ሰዎች ! አመፃን ገንዘብ አድርጋችሁ የዚህን ዓለም ትርፍ ታምናችሁ እግዚአብሔርን ከዳችሁ የዲያብሎስን ፈቃድና ሃሳቡን ታምናችሁ በሱ ጥበባዊ ድርሰት ተተማናችሁ ፤ በሃብቱ በገንዘቡ በምድሪቱ ሁሉ ቦርቃችሁ በዲያብሎስ ድጋፍ በናንተም የአመጽ የሃጢያት የትእቢት የክህደት የምንዝርና የጨካኝነት የዘረፋ የነፍስ ገዳይነት የዘረኝነት መውደድ ለተለከፋችሁ እንቁዋን እምነት ተዋህዶን አፍርሳችሁ አሳዳችሁ ገላችሁ በዚህም ተደስታችሁ ! ከዓለም አቀፍ ወዳጆቻችሁ የዲያብሎስ ሹመኞች ጋር በመተባበር ፍፁም ጨለማን አንግሳችሁ ፤ ዛሬም በአገሬ በኢትዮጵያም ሆነ በመላው ዓለም በተዋቀረ እጅና እግራችሁ የእግዚአብሔርን ሕዝብ/ አልጠፋ አላችሁ እንጂ!/ እውቀታችሁ አቅማችሁ ዘዴአችሁን ሁሉ በመጠቀም እለከልካይ የነገሳችሁ የዲያብሎስ ልጆችና ተጠዋሪዎች እንዲሁም ተሰፈኞችና የይቆይልን እድሜ ለማኞች ዛሬ ለናንተም መርዶው ይድረሳችሁ ፡፡ ቢቃ በታላቅ ቁጣ ከምድረ ገፅ ትጠረጉ ፍፁም ወደትቢያነት ትመለሱና ላንዴና ለሁሌም በመቃብራችሁ ትከደኑ ዘንድ ተወሰነ፡፡ አዋጁ እናንተን በመጥረግ ምድሪቱን በማፅዳት ብርሃናዊው መልካሙና የትንሳኤው ዘመን ይዘልቅ ዘንድ ተወስኖአልና የተሳካ የጨለማ ጉዞ ያድርግላችሁ ፡፡ የታመናችሁበት ዲያብሎስም በሲኦል እናንተን ወገኖቹን እንግዶቹን ለመቀበል እየተጣደፈ መሆኑንም አረጋግጥላችኋለሁ!!!

ይህን አዋጅ ነጋሪ መልእክት ደርሶአችሁ መስማቱን እድል ለገጠማችሁ ሁሉ መጪው እውነት ይህ ነው ፡፡ ተወደደም ተጠላ አዋጁ ታውጇል ፡፡ አሚመለስ አሚለወጥ ነገር የለም ፡፡ በእግዚአብሔር ውሳኔ መፀፀት የለምና! ተፈፀመ ፡፡

አዲስ ብርሃናዊ ዓለም ፤ መልካም ዘመን ልኡል የሚነግሥበት ብርሃናዊ እገዛዝ የሚሰፍንበት ዘመን ላይ ትደርሱ ዘንድ ለታደላችሁ የልኡልና የድንግል ልጆች ደግሞ እንኳን ደስ ያላችሁ እላለሁ ፡፡

ለእግዚአብሔር አብ !ለእግዚአብሔር ወልድ !ለእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ ከዘለዓለም እስከ ዘለዓለም ክብር ምሰጋና እንደማያቋርጥ ጅረት ይፍሰስለት !!! አሜን ! አሜን ! አሜን !

ለእናታችን ለቅድስተ ቅዱሳን ድንግል ማርያም ምስጋና ይድረሳት!!! የዳንክው ሁሉ የእንባዋ ውጤት ነህና አመስግናት ውደዳት!

ታሪም ፀልተለዩን ለረዱን ለጠበቁን ለአማለዱን ለታገሱን ለተሸከሙን ቅዱሳን ሊቃነ መላእክት ለቅዱስ ሚካኤል ፤ ለቅዱስ ገብርኤል ፤ ለቅዱስ ሩፋኤል ፤ ለቅዱስ ፋኑኤል ፤ ለቅዱስ ኡራኤል ፤ ለቅዱስ ራጉኤል ፤ ለቅዱስ ሳቁኤል፤ ለቅዱስ አፍንንኤል ፤ ለቅዱስ ሰላትያል ፤ ለቅዱስ ሰዳኪያል፤ ለቅዱስ ራሙኤል፤ ለቅዱስ ሱሪያል ሁሉ ምስጋና ይድረሳቸው!!

ለሰማእቱ ጊዮርጊስ ለሰማእቷ አርሴማ በምልጃቸው ለተራዱን ሁሉ ለሁሉም የልኡል ቅዱሳን አባቶቻችን ሁሉ ምስጋናችን ይድረስ!!

ይህ አዋጅ ነጋሪ መልእክት በዛሬው እለት በአሥራ ዘጠኝ እለተ ክብረ ገብርኤል ቀን በታሕሳስ ወር ሁለት ሺ ሰባት ዓመተ ምህረት ተፅፎና ተዘጋጅቶ ወጣ !!!

የልኡልና የድንግል ባሪያ የቅዱሳን መላእክትም አገልጋይ ከሚሆን ታናሽ

ባሪያ ተላከ!!!

# ኢትዮጵያ የዓለም ብርሃን

ኢየሱስ ክርስቶስ ካህኑ ለዓለም ንጉሠ ፅዮን ወንጉሠ ነገሥታት ዘኢትዮጵያ
ድንግል ማርያም እሙ ወእምነ ንግሥተ ፅዮን ወንግሥተ ነገሥታት
ዘኢትዮጵያ







## ኢትዮጵያ የዓለሙ ገዢ

መግለጫ:-

በግንባርና በመጨረሻ ገጽ ያሉ ሥእሎች መግለጫ

## በግንባር ያለው ስእል ምንን ይናገራል ?

- ሰንደቅ ዓላማው የኢትዮጵያ ሕዝብ መለያውና ምልክት መሆኑን በተለይም በመነሻነት ከልኡል ጋር ቃል ኪዳን መፈፀሙን የሚያረጋግጥ መሆኑን ይገልፃል ::
- ኢትዮጵያና ተዋህዶ እርቶዶክስ እምነት የማይነጣጠሉ መሆናቸውን ያመለክታል ::
- በአረንጓዴ ቢጫ ቀዩ ሰንደቅ ዓላማችን ላይ ባእድ ምልክት መለጠፍ በኢትዮጵያዊነት በተዋህዶ እምነት ላይ እና በሃገረ ድንግል ላይ የሆነ የጠላት ጥቃትና ብርቱ ወንጀል መፈፀሙንያመለክታል :: ከአንበሳው ስር ያለው ሉል ዓለምን ይወክላል :: መልእክቱም በዓለም ሁሉ ላይ ተፈጻሚ ይሆናል
- አንበሳው የዘለዓለሙን ንጉሥ ጌታችን መድሃኒታችን እየሱስ ክርስቶስንና የምድሩም የሰማዩም ገዢነቱን ያሳያል :: መስቀሉም /በአንበሳው እናት ላይ ያለውና በበትረ መስቀሉ ጫፍ ላይ ያለው/ የመዳናችን የመሰረታዊ እምነታችን እንዲሁም ሃይላችን መስቀሉ መሆኑን ያረጋግጣል :: ዘውዱ በሰማይም በምድርም ሥላሴ ገዢ ፈጣሪ መሆኑን ፈቃዱም ሃሳቡም ትእዛዙም ማንም የማያግደው ተፈፃሚ መሆኑን ያረጋግጣል ::
- ሰንደቅ ዓላማውን የያዘው የብረት ዘንግ ጫፉ መስቀል ያለበት ሥልጣንና ሃይልን የሚያሳይ ሲሆን በኢትዮጵያ ምድር የሚፀና ከዚህም ማእከል ተነስቶ መላውን ዓለማችንን የሚገዛ የሚነግሥ መሆኑን ያረጋግጣል :: የተዋህዶ እምነታችን የኢትዮጵያዊነታችን ጽኑ መገለጫ መሆኑን ያሳያል ::

## በጀርባው ያለው ስእል ምንን ያመለክታል ?

- በስእሉ ውስጥ ከእናቱ ላይ ያለው ሥላሴ በመንበራቸው ሆነው ሲሆን ሃያ አራቱ ካህናተ ሰማይ በግራና በቀኝ በመንበሩ ዙሪያ ሆነው ሁሌም ያለማቋረጥ የሚያመሰግኑት መሆናቸውን የሚገልፅ ነው :: መንበሩንም አርባእቱ እንስሳ ሱራፌል ኪሩቤል ተሸክመውት ይታያል :: ከመንበሩ ሥር ሰባቱን ሊቃነ መላእክትን ያሳያል ::
- በመሃል ጌታችን መድሃኒታችን እየሱስ ክርስቶስን ያሳያል :: በዙሪያውም የቤተ ክርስቲያንን ሰባቱን ባሕሪያት የሚገልፁትን ሰባቱን መቅረዞች የሚገልፅ ሲሆን በዮሃንስ ራእይ የተገለፀውን ማለት ነው / ሌላው : በእጁ መፃፊያና ሰሌዳ የያዘውን አባት የሚያሳይ ሲሆን ከሥላሴ መንበር የሚፈሰውን መልእክት ትእዛዝና ፈቃድ ለሰው ዘር ለማድረስ ሲከትብ ይታያል :: የዓለም ካርታውም ከልኡል የሚፈሰው መልእክት በመላው ዓለም ላሉ ሰዎች ሁሉ የተላከ መሆኑን ያመለክታል::

## በጥቅሉ ፡

ሥላሴ አክብረው ለፈጠሩት የሰው ልጅ በየዘመኑ ይናገራሉ :: ሰው አያስተውልም እንጂ :: ሰማያትም ፡ ምድርም ፡ እንስሳትም ደቂቀ ነፍሳትም ግዑዙ ዓካልም ሁሉም ይናገራሉ :: ላስተዋለው የልኡልን ፈቃድ ፡ ትእዛዝ ፡ ሃሳብ ፡ ውሳኔ ሁሉ ፡ በየእለቱ በሚከውኑት የሕይወት መስተጋብራቸው ይናገራሉ :: ለማን ? — ለሰው ልጅ !! ማስተዋልን ፡ አስቦ ማድረግን ፡ አውጥቶ አውርዶ መወሰንን የሚችል አእምሮ የተሰጠውን እምሳለ ልኡልን የሆነውን የአዳምን ዘር ይመለክታል ::

""""""""""""""""""""""""""""""""""""""""""""""""""

ታኅሣሥ 21 ቀን 2011 ዓመተ ምሕረት

ተፃፈ ፡ በአንድ ታናሽ የልኡል ባሪያና

ከኢትዮጵያ ተዋህዶ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ምእመን አንዱ

አዲስ - አበባ

ኢትዮጵያ

ለሁሉም የአዳም ዘር!

ከሁሉም በላይ ለተወደዱት ፀንተው ለተገኙት ለእግዚአብሔር ሕዝቦች የተላከ!

ማሳሰቢያ፡ —

- ወገኖቼ ! መልእክቱን ይገባዋል ብላችሁ ላመናችሁበት ሁሉ አድርሱ !
- ቢያንስ ለ3 ሰው ብታደርሱ መልካም ነው !
- በማስተዋል አንብቡ !
- የቀደሙትን 6 መልእክቶች ብታነቡ ይበልጥ ለግንዛቤአችሁ ይረዳል !
- ይህንን መልእክት ካደረሱላችሁ ስለቀደሙትም መልእክቶች ብትጠይቁ ሊረዱአችሁ ይችላሉ !

.............................................................



መልእክት ስምንት ቀን ታኅሣሥ 21 ቀን 2011 ዓ.ም

በስመአብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ አሜን !!

የፍጥረት ሁሉ ጌታ የአባቶቻችን አምላክ ስሙ የተመሰገነ ይሁን !!

ቅድስተ ቅዱሳን ድንግል እናታችን ስሟ የተመሰገነ ይሁን !!

ወገኖቼ ሕዝበ ክርስቲያን !!

ወገኖቼ መላው የአዳም ዘር !!

ማሳሰቢያ :—— ይህን መልእክት ለማንበብ እድል የገጠማችሁ ወገኖቼ !! የእምነት ሰዎች ከሆናችሁ ፤ በየትኛውም የእምነት ተቋም ውስጥ ብትሆኑም በዚህ መልእክት በእጃችሁ መገኘት የመጀመሪያችሁ ከሆነ ልትገረሙ ወይም ልትረበሹ ትችሉ ይሆናል ። ሆኖም ምንም አይደለም ። ይልቅስ የቀደሙትንም 6 መልእክቶች አግኝታችሁ የ13 ዓመቱን ሂደት ብትገነዘቡበት የግል ውሳኔ ለመውሰድ ይረዳችኋል ብዬ እገምታለሁ ። ለማታምኑበት ለምታላግጡት ከነጠላው ፍርድ ይልቅ ድርብ ፍርድን በራሳችሁ ባትጋብዙ መልካም ነው ። እንኳን ለተደራረበ ፍርድና ቅጣት ለአንዱም የመሸከም አቅም የላችሁም ። ስለዚህ እንብባችሁ ከምታፈዙና ለብርቱ ቅጣት እራሳችሁን ከምትጥሉ ባታነቡት ይሻላል ብዬ እመክራችኋለሁ ።

የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል —— እነሆ ክፉ ነገር ከሕዝብ ወደ ሕዝብ ይወጣል ። ጽኑም አውሎ ነፋስ ከምድር ዳርቻ ይነሳል ። በዚያም ቀን የእግዚአብሔር ግዳዮች ከምድር ዳር ጀምሮ እስከ ምድር ዳር ድረስ ይሆናሉ ። አይለቀስላቸውም ፤ በምድር ላይ እንደ ጉድፍ ይሆናሉ እንጂ አይከማቹም አይቀበሩም ። ትታረዱና ትበተኑ ዘንድ ቀናችሁ ደርሶአልና ! እንደተወደደም የሸክላ ዕቃ ትወድቃላችሁና እናንተ እረኞች አልቅሱ ! ጩኹም ! እናንት የመንጋ አውራዎች በአመድ ውስጥ ተንከባለሉ ሽሽትም ከእረኞች ማምለጥም ከመንጋ አውራዎች ይጠፋል ። እግዚአብሔር መሰማሪያቸውን አጥፍቶአልና ! የእረኞች ጩኸት ድምፅ የመንጋ አውራዎችም ልቅሶ ሆኖአል ። ከእግዚአብሔር ጽኑ ቁጣ የተነሳ የሰላም በረት ፈርሶአል ። እንደአንበሳ መደቡን ለቅቆአል ፤ ከአስጨናቂውም ሰይፍና ከፅኑ ቁጣው የተነሳ ምድራቸው ባድማ ሆናለችና ትንቢተ ኤርሚያስ ም 25 ፤ 32 — 38

ይህ የመልእክቱ መግቢያ የልኡል ቃል ! መልእክቱ ለምን እንደመጣ ጥቅል የሆነ ግንዛቤ እንዲኖራችሁ ታስቦ ነው መግቢያው ላይ የሰፈረው ።

ወገኖቼ በብዙዎች ዘንድ ይህ መልእክት ለምን መጣ ? አዋጁ ታውጆ አብቅቶ የለም እንዴ? ለምን ሁሉም ነገር ተደበላልቆ አይጠናቀቅም ? የሚል ስሜት በብዙ ወገኖች ዘንድ ይነሳል ። አንዳንዶችም ጊዜ ለመስጠት በመዘግየቱ የቀረ የማይሆን መስሎአቸው ከእምነታቸው ጎለው ጠላት በሚፈጥረው መልከ ብዙ ሴራና እጅግ የረቀቀ ጥበቡ ፤ በዓለም በዘረጋው የፕሮፓጋንዳ ፤ ሚዲያ ፕሬስ ፤ ሶሻል ሚዲያ ፤ ቴሌቪዥን ፤ ሬዲዮና ሌላም ተመሳሳይ የስርጭት መረቡ ፤

ተስፋ አስቆራጭ ፤ ድርጊትና ንግግሩ ፤ በአታቸውን ስለለቀቁ ፤ ለአሁኑ መልእክትም ያላቸው ቅቡልነት ደካማ እንደሆነ እረዳለሁ ። አንዳንዶች አሁንም ትላንት ከተቃኙበት የጠፋና ክንቱ አቋማቸው

በመነሳት መልእክቱን የሚነቅፉ አሉ ፡፡ ብቻ ሁሉም እንደ ታየው እንደመሰለው አስተያየት ይሰጣል ብዬ አገምታለሁ ለደከማችሁት የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ይላል ——

——ያእቆብ ሆይ እስራኤልም ሆይ መንገዴ ከእግዚአብሔር ተሰውራለች ፍርዴም ከአምላኬ አልፋለች ፡፡፤ ለምን ትላለህ ፤ ለምንስ እንዲህ ትናገራለህ ፤ አላወቅህምን ፤ አልሰማህምን ፤ እግዚአብሔር የዘለዓለም አምላክ የምድርም ዳርቻ ፈጣሪ ነው ፡፡ አይደክምም አይታክትም ማስተዋሉም አይመረመርም ፤ ለደካማ ሃይልን ይሰጣል ጉልበት ለሌለውም ብርታትን ይጨምራል ፡፡ ብላቴኖች ይደክማሉ ይታክቱማል ፤ጎበዛዝቱም ፈጽሞ ይወድቃሉ ፡፡ እግዚአብሔርን በመተማመን የሚጠባበቁ ግን ሃይላቸውን ያድሳሉ ፡፡ እንደንስር በክንፍ ይወጣሉ ይሮጣሉ አይታክቱም ይሄዳሉ አይደክሙም ፡፡ ይላል ልኡል እኔም ገና በመልእክቴ መግቢያ አይዞህ ደከምክም ወደቅህም ትነሳለህ !!! እኔም ይህንኑ እልሃለሁ ! አይዞህ ! ትነሳለህ

ትንቢተ ኢሳኢያስ ፤ ም ፡ 40 ፡ 27 — 31

ከሁሉም በላይ፤ ወገኖቼ ! በእርግጥ ልታውቁ የሚገባው ቁም ነገር አለ ፡፡ ዛሬ ይህ መልእክት የመጣው በዋናነት ፤ የደከሙትን ለማፅናት ፤ የበረቱትንም ፤ ይበልጥ እንዲተጉ ለማድረግ ነው፡፡ እናም አልደረሰም ፤ ዘገየ የት አለ ? ለሚሉት ለሚያፌዙት አሁን ! በአንገታቸው ላይ ስለሆነ ከፌዛቸው ይጠግቡታል ፡፡ ስለነሱ ገድዶኝ አይደለም ፤ ይህ መልእክት የማደርሰው ። እነሱ ትቢያ ናቸው ወደተጠበቀላቸው እሳት ይገባሉ ፡፡ የእግዚአብሔርን ሕዝቦች ! ከፊታቸው የደረሰው የቁጣው እሳት ! እንደሚታሰበው ሳይሆን ፤ ከሰው ሕሊናና ግምት በላይ ስለሆነ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ; እንዳይታወኩ ፡ ለማፅናት ነው ፡፡ የምነግራችሁም — የልኡልን የአባታችንን የእናታችንን የድንግልን የማይናወፅ ቃል ነው ፡፡ ሁለቱም ቃላቸው ባጭሩ ይሕ ነው ፡፡ ልጆቻችን አይዞአችሁ ደርሰናል ! ፡፡ አትፍሩ አትታወኩ ! ፡፡ ፅኑ ! ፡፡ አትደንግጡ ! የነጣውን ለብሳችሁ ! በጥፋት ማእበል ውስጥና መሀል ብትገማለሉ ፤ አንዲቷን ፀጉራችሁን እንኳን የሚነካ የለም ፡፡ ልጆቻችን ዙሪያችሁ በእሳት የታጠረ ነው ፡፡ ሊጎዳችሁ ያሰበ ገና ሃሳቡ በአእምሮው ሲፈጠር እናንተም ጋ ሳይደርስ ይወገዳል ! አሁን ደርሳችኋል ስለአመፀኞች ጥፋት ፤ ስለፍርዳቸው አፈፃፀም ተመልካችና ተደማሚ ናችሁ እንጂ ማን ጥጋችሁ ይደርሳል ? ሁሉም ተመዝኖአል ዋጋው በእጄ ነው እንደ እጣ ክፍሉ ይከፈለዋል፡፡ ይላል የሁለቱም / አባት እናታችሁ /ቃል ፡፡

እንደምን ከረማችሁ ! የሠራዊት ጌታ ስሙ የተመሰገነ ይሁን ! አኑሮን ጠብቆን ዘመንን እያቀዳጀ ለዚህ ቀን አድርሶናል ፡፡ የእግዚአብሔርን ቸርነት ትእግሥትና ፍቅሩን የተረዳ ሁሉ ዛሬ ላይ ሆኖ ልብ ያልተነፈገው ማስተዋልን ገንዘቡ ያደረገና ጥበብን የለበሰ የፈጠረውን ጌታ ከልቡ ያመሰግናል ፡፡ በመልእክቶቹና በ6ኛው መልእክት ከተገናኘን 4 ዓመት ሆኖአል ፡፡

ሁላችሁም እንደምታስታውሱት 6ኛው መልእክት ዋናው መልእክቱ የነበረው በ7ኛው መልእክት የወጣውን አዋጅ ለመግለፅ ነበር ፡፡ አዋጁ እንዲነበብ አልተፈቀደምና አልተሰራጨም ነበር ፡፡ በዛሬው መልእክቴ ስለአዋጁ ጥቂት ላስታውሳችሁ የወደድኩት አለምክንያት አይደለም ፡፡ አዋጁ ከታወጀበት ከሚያዚያ 7/ 2007 ዓ.ም ጀምሮ ራሱን ለመትከል እንደ ልኡል ፍርድ ዓለምን በየደረጃው እያበጠራት ይገኛል ፡፡ ለዚህ ምስክሩ አገራችን ኢትዮጵያ ዛሬ ያለችበት ሁኔታ ነው ፡፡ ቀድማም ነፃ የምትወጣውና በአዋጁ የተገለፀው የሽግግሩም ሆነ ቋሚው ሕግጋተ ሥላሴ በመጀመሪያ የሚፀናው እዚህ ኢትዮጵያ አገራችን ላይ ነው ፡፡ የእግዚአብሔር ሕግጋተ - ሥላሴ በአገራችን ዙሪያ ባሉ አገሮችም ጭምር የሚፀና ለመላው ዓለም እንደፀሐይ የሚያበራ ሆኖ ይቆማል ፡፡ ይህንን ለማየት በውስጡም ለመኖርና እድሚን ለመቀዳጀት የሚታደለው ማን እንደሆነ የሚያውቀው ማንም አይደለም ልኡልና ድንግል በግንባሩ

ያተሙበት ብቻ ነው ። ለዛሬው ከሃዲ ተውልድ ይህ ተረት ነው ። ለዚህ ነው አዋጁም የማይገለፀ ው ፤ ወገኖቼ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ፡ በእምነት አኗግራችሁ ለማየት የታደላችሁ ፡ ወንድም እህ ቶቼ እናንተ ተስፋችሁ የፀና የማይናወፅ ነው ። ራሳችሁን ከዚህ ዓለም ጉድፍ ስለጠበቃችሁ ሕይወታችሁ ሥጋዊ ኑሮአችሁ በከፍተኛ ችግር ውስጥ እንደሆነ እኔም የምመሰክረው ነውና ፅኑ እንጂ አትናወጡ ።

የሚጠፋው ጠፍቶ ፤ የሚቫገረው ደግሞ የተፈቀደለት ብቻ ይሆናል ። የመከራው ክብደት ተስፋን ያጨልማል ሥጋ ነንና እንደከማለን እንወድቃለን ፤ ነገር ግን የምንታመንበት አምላክ የምንወዳት እናታችን ቢቃላቸው የታመኑ ስለሆኑ ብንወድቅ ያነሱናል ።

፤ ብንቆስል ብንንዳ ይጠግኑናል ። ስለ ወገኖቼ የእግዚአብሔር ሕዝቦች በአንድ ርእስ ወደኋላ ስለምናየው ለመግቢያ ያህል ያልኩትን በዚህ ልግታና ወደጉዳዩ ቀጥታ ልግባ ።

እግዚአብሔር ማዳኑን አስታወቀ ፤ በአሕዛብም ፊት ጽድቁን ገለጠ ፤

ለያእቆብ ምህረቱን ፤ ለእስራኤልም ቤት እውነቱን አሰበ ።

መዝሙረ ዳዊት ፡ 97(98) 2–3

የዛሬው መልእክት አዲስ ነገር አዝሎ የመጣ እንዳይመስልህ ። የተውከው የረሳኸው እየፈጩኸ ፤ እየቆላህ ፤ እንደፍርዱ ፤ እያካተተህ የመጣውን ፤ የፍርድ ቃል ፤ ሊያጠናቅቅህ ከአጠገብህ ተሰድሮአልና መለስ ብለህ እንድታይ የመፈፀሚያ ጉዞ መጀመርህን እንድትረዳ ፤ ያለህበት ሰአት ምን እንደሚመስል እንድታውቅ እጣህንም እንድትገነዘበው ለማድረግም ነው ።

ለ13 ዓመት ለ6 ጊዜ የተላለፉትን መልእክቶች ለመሆኑ ታስታውሳቸዋለህ ? ትዝስ ይሉሃል ወይ ? ማንን ፈርተህ ! እንኳን ልታስታውሰው ዛሬ በዚህ መልክቴ ስላነሳሁብህ የምን መልእክት? የምን እግዚአብሔር? እያልክ እንደምታፌዝ ሳይታለም የተፈታ እውነት ነው ። ዛሬ ትውልዱ የጠፋ በተለያዩ ባእድ አምልኮቶች ፤ ሱሶች ፤ ፍጹም የረከሰ ጠባይ እንዲሁም ከእንስሳም ያነሰ የሶዶምነት ባህሪይ የተጠመደ መሆኑ ማንም የማያስተባብለው ሃቅ ነው ።

በኔ በታናሽ ባሪያው በኩል ልኡል ለሁሉም የአዳም ዘር ሲያስተላልፍ የቆየውን የፍርድ ቃል ፤ ምክር ፤ ግሳጼ ፤ ተስፋ ስትሰማው ቆይተሃል ። የናቅኸው ናቅህ የተቀበልከው ተቀበልህ ። ምርጫህ ነው ፤ መልካም አደረግህ ። ውጤቱንም ከዚሁ መልእክትም ሆነ ከቀደሙት የፍርድ ቃል መልእክቶች ስምተኸዋል ዛሬም የመፈፀሚያህን መርዶና የተዘጋጀልህን ማጠናቀቂያ ትበስራለህ !!

የልኡል ሃይለ ቃል እንዲህ ይላል ፤

መጽሐፈ - ምሳሌ ምእራፍ 1 ፡ 22 -33

ፊዘኞች ፌዝን ይፈቅዳሉ ፤ ሰነፎችም እውቀትን ይጠላሉ ። ወደ ዘለፋዬ ተመለሱ እነሆ መንፈሴን አፈስስላችኋሁ ፤ ቃሌን አስተምራችኋለሁ ፤ በጠራሁ ጊዜ እምቢ ስላላችሁ እጄን በዘረጋሁ ጊዜ ማንም ስላላስተዋለ ፤ ምክሬን ሁሉ ግን ቸል ስላላችሁ ፤ ዘለፋዬንም ስላልፈቀዳችሁ ፤ እኔም ስለዚህ በጥፋታችሁ እስቃለሁ ፤ ጥፋታችሁም በመጣ ጊዜ አላግጥባችኋለሁ ። ድንጋጤ እንደጎርፍ በደረሰባችሁ

ጊዜ ፤ ጥፋታችሁ እንደ አውሎ ንፋስ በመጣ ጊዜ ፤ ጭንቅና መከራ በወረደባችሁ ጊዜ ፤ የዚያን ጊዜ ይጠሩኛል እኔ ግን አልመልስም ። ተግተው ይሹኛል ነገር ግን አያገኙኝም ፤ እግዚአብሔርን መፍራት አልመረጡምና ፤ ምክሬን አልፈቀዱምና ፤ ዘለፋዬንም ሁሉ ንቀዋልና ፤ ስለዚህ የመንገዳቸውን ፍሬ ይበላሉ ። ከራሳቸው ምክር ይጠግባሉ ፤ አላዋቂዎችን ከጥበብ መራቅ ይገድላቸዋልና ። ሰነፎችንም ቸልተኛ መሆን ያጠፋቸዋልና ፤ የሚሰማኝ ግን በእርጋታ ይቀመጣል ። ከመከራም ስጋት ያርፋል ።

---

ተጠበቅህ ፤ ተዘለፍህ ፤ ተመከርህ፤ ተገሰጽህ እንኳን ልትሰማ ፤ ከላይ የልኡል ቃል እንደሚነግርህ ፤ አፈዝህ ፤ ናቅህ ፤ እውቀቴንም ሁሉ ጠላህ ይላል የልኡል ቃል ። ይህንን እውነትስ ወዴት ታደርገው ፤ ሰማይንና ምድርን ፤ አንተንም ፤ ማንም የማይመረምረውን ዓለምም የፈጠረን አምላክ የምታቃልል አንተ ማነህ ? አቧራና ብናኝ ሆነህ የምትቀረው ልኡልን ልትገዳደር የደፈርከ እኮ አንተን ማን አንበልህ ? ሁላችን እንደምናየው ልቡና ያለው ሰብአዊ ፍጥረት ሁሉ እንደሚመሰክረው ትእቢትህ ከምድሪቱ አልፎ ሰማይን ዘለቀ ። እሱ በሰጠህ አእምሮ መልሰህ ስሪህን ልትንቅ ልታቃልል ልታፌዝ የደፈርከ ፤ ቅዱስ መንፈስን በትእቢት ተሞልተህ የተሳደብህ እኮ ማን ትባል ?

እንደ አንተ ዓይነት ደፋርን በምን ቃል እንግለፀው ? ለነገሩ ሁሉም ስላበቃ ፤ መዋቀሻ ጊዜም ስላልሆነ ፤ ወደሚሆነው እናትኩር ። አሁን ከቃሉ እንደሰማኸው ፤ መከራህ እንደጎርፍ ደርሶአል ፤ ጭንቅና መከራህ ተደርበውብሃል ሌሎችም የመከራና የጥፋት ዓይነቶች እኔ ልቅደም እኔ ልቅደም ወረፋ ይዘዋል ። አንተን ከመጥፋት ! የሚያስጥልህ የሚታደግህ የለም ። ከአንግዲህ ልኡልም ድንግልም ብትጠራቸው አይሰሙህም ፤ ተግተህም ብትፈልግ አታገኛቸውም ፤ ስለሆነም ውጤትህን ከፈጻሚዎቹ ታገኛለህ ።

ዛሬ እንደቃሉ ዓለም በምን ሁኔታ ውስጥ ነች ? ለ13 ዓመት ያ ሁሉ መልእክት ሲፈስ ወንድሜ ወዴት ነበርክ?

—ዓለምና የፍርድ ቃሉ ትናንት ዛሬና ነገስ ፤ ምን እንጠብቅ ?

— አገራችን ኢትዮጵያና የፍርድ ቃሉ ትናንት ዛሬስ ነገስ ?

— የዚህ መልእክት ዋናው ዓላማ የእግዚአብሔር ሕዝቦችን ለማፅናት ፤ የታላቁን የቁጣ ቀን መድረሱን ለመግለጽ ሲሆን ፤ የተዋህዶ አርበኞች ወዳጅ ወገኖቼ እናስ ምን ማድረግ ይጠበቅባችኋል ?

---

የልኡል ሃይለ ቃል እንዲህ ይላል ፤

አባቱን የሚረግም ፤ እናቱንም የማይባርክ ትውልድ አለ ፤

ለራሱ ንፁህ የሆነ የሚመስለው ፡ ከእርኩሰቱ ያልጠራ ትውልድ አለ ፤

ከፍ ከፍ ያሉ አይኖች ያሉት ፡ ሽፋሽፍቶቹም ወደላይ የሚያዩ ትውልድ አለ ፤

ድሆችን ከምድር ላይ ችግረኞችንም ከሰው መካከል ያጠፉና ይጨርስ ዘንድ ፤

ጥርሶቹ ሰይፍ መንጋጋዎቹ ካራ የሆኑ ትውልድ አለ ፤

አልቅት — ስጠን ስጠን የሚሉ ሁለት ሴቶች ልጆች አሉት ፤

ሶስቱ የማይጠግቡ አራቱም በቃን የማይሉ ናቸው ፤

እነርሱም - ሲኦልና ፤ የማትወልድ ማሕፀን ፤ ውሃ የማትጠግብ ምድርና፤

በቃኝ የማትል እሳት ናቸው ።

በአባትዋ የምታላግጥን ፡ የእናቷን ትእዛዝ የምትንቅን ዓይን

የሸለቆ ቁራዎች ይነጠጉጡኢታል አሞራዎችም ይበሉኢታል ።

መጽሐፈ ምሳሌ ፡ ም ፡ 30 ፡ 11 – 17

አንተ እጅግ የከፋህ ትውልድ ፤ ጨካኝ ዘረኛ ሆድ አምላኩ አረመኔነትን ነውረኝነትን ፤ አታላይነትን ንቀትን ትእቢትን እንደ ጌጥ የለበስክ ትውልድ !! በውኑ አንተን የመሰለ የዲያብሎስ መገለጫ በምድር ታይቶ ያውቃል ? በፍፁም !!

ዲያብሎስን ፈቅደህ ፡ በራስህ ላይ ያነገስህ ትውልድ ፤ ከንቱ የከንቱዎች ሁሉ ቁንጮ የሆንክ በእውቀትህ በሰበሰብከው ሃብት ንብረት ገንዘብ ሥልጣን የተመካህ ፤ ድሃውን ሕዝብ በዘር ከፋፍለህ በተለያየ እምነት አቧድነህ አርቲፊሻል ድንበር ፈጥረህ ጨካኝ አውሬነት የተላበሱ ስራዊት አደራጅተህ ዓለምን የምትፈጭ የምትቆላ የሉሲፈር አሽከር ፤ በአገራችን ኢትዮጵያ ከጌቶችህ ከአለቆችህ ከነአሜሪካ ከነእንግሊዝ ከነአረብ የዘይት አለቆች ተጣምረህ የእባብነትህ ን ቆዳ ቀይረህ ህዝቡን ልትገዛ የተገሰልክ ፤ ጨካኝ ዘረኞችን ሸክፈህ ያለህ ዘረኛ ትውልድ በቃሉ ላብስርህ አላጋጭ ነህና ከፉ ጥፋትን አሟሟትን ትሞታለህ የቁራዎች የአሞራዎች ቀለብ ትሆናለህ ። ይህ ደግሞ ሳይውል ሳያድር የሚመጣብህ ፍርድህ ነው። በጀርባህ ያዘልከው የተሸከምከው ነውርህ አጠንብቶሃልና ከንቱ ትውልድ ገና ብዙ ጉድህ አለና ፍፃሜህን አድምጥ !!! ዛሬ ያለሃፍረት በመንግሥት ቅየራ ሥም አንዱን ዘረኛ በሌላው ዘረኛ ተክቶ ጋላቢውን ሳይሆን የደከመውን ፈረስ በሌላ መልክ የቀየረ ፈረስ ሰይማችሁ ያንኑ የሺዎች ዘመን ሙት የዲያብሎስ አገዛዝ ለመተካት የምትደክሙ ከንቱዎች ናችሁ ። የምትደሰኩሩለት ዲሞክራሲ በጌቶቻችሁ ሕይወት እየተመስከረና እየታዩ ነው ። ዛሬ የሕይወትን ጣእም ከልኡል የተሰጠውን ጥሎ ፤ በዲያብሉስ ተክቶ የሚኖረውን የከረፉ ፍፁም

የጠፉ ትውልድና የነፈገን ዓለም ለሁሉም ነገር መድሃኒት ነው ብላችሁ የምትወተውቱ በአርማ ነው የምትገሬችሁ አብሬችሁ ትጠረጋላችሁ የምትታመኑባቸውም እንእንግሊዝ አሜሪካ ፈረንሳይ ጀርመን ቻይና ሳኡዲ አረቢያ ኤሚሬትስ ሌሎችም የትላንቱም ደጋፊዎች የዛሬውም አዋላጆች ከእንግዲህ በኢትዮጵያ ሲደረስው ጥፋት ሁሉ ተጠያቂዎች በመሆናችው ይጠረጋሉ ::

አስተድሜ በመግቢያዬ ስለመጨረሻ እጣችሁ የተናገርኩት እንደከፋታችሁ እንደጭካኔያችሁ እንደ ትቢታችሁ ! እስካሁኗ ሰአት ድረስ በፀና የጥፋት ተግባር ላይ ስለሆናችሁ ነው ፤ ፍርዳችሁ እንደ ፀሃይ የወጣው ! ይህ መልእክት እየደረሰም እንኳ ከመጥፎ ሥራችሁ የማትገቱ ናችሁ :: እጥፊያችሁ እናንተን ለመጥረግ በፈጣን እሩጫ ላይ ነው :: ጅማሮውንም እያያችሁት ነው ::

ዛሬ ስለዓለም ስናነሳ ትላንት ምን እንደነበር ካልቃኘነው ለዛሬው መንደርደሪያ አናገኝም :: ዓለማችን ለብዙ ዘመናት /በሺ ለተቆጠሩ/ ስትመከር ስትግገር ፤ ስትገሰፅ ፤ ስትቀጣ ኖራለች:: ብዙ የእግዚአብሔር አገልጋዮች ፤ ከችሩ አምላካችን ቅዱስ ትእዛዙን በመቀበል ፤ ለመምከር ለመገሰፅ ለማስተማር በመላው ዓለም ተሰማርተው የታዘዙትን ለመፈፀም በብርቱ ደከመዋል ነገር ግን እጅግ ጥቂቶች ሰምተው ንስሃ ገብተው የተጠቀሙባቸው ሲሆን ፤ በአንፃሩ ደግሞ እጅግ በቁጥር የበዙት አለመቀበል ብቻ አይደለም አሳደዋቸዋል ፤ አስረዋቸዋል ፤ ገለዋቸዋል ::እኔም የቅርቡ የልኡል ታናሽ መልእክተኛ ለ 13 ዓመት ከዚህ መልእክት ጋር ሰ7 ጊዜ የታዘዝኩትን መልእክት ለማድረስ ሞክሬአለሁ :: እንደ አባቶቼ ባይሆንም የእቅሜን ዋጋ ከፍያለሁ :: ይሁንና ይህም ሆኖ ተንድተንም ቢሆን ምን አለ ትውልዱ በመልእክቱ ተጠቅሞ ቢሆን ነበር በማለት ዛሬ ላይ ሆነን በታላቅ ቁጭት እናዝናለን ::

ዓለም ገና ከጅምሩ አምላኳን የሰቀለች የናቀች ፤ ድንግልን የናቀች የካደች ያቃለለች ከመሆ ኗ በላይ የሄደችበት መንገድ የቀደመው አባብ በቀደደላት ጎዳና ስለነበር የማንንም የልኡል መ ልእክተኛ ምክርም ሆነ ጩኸት አልሰማችም :: በራሷ ፈቃድ ዲያብሎስን አነገሰች እንጂ የሁ ሉንም ቅን ምክር አልተቀበለችም :: በመካዷና በጥላቻዋ በንቀቷ ብቻ አልቆመችም :: ብዙ የእግዚአብሔርን ሕዝቦች ገደለች አሳደደች አሰቃየች ፤ ድርጊቷን ከልጅ ወደ ልጅ እያሸጋገረች እንደመልካም ነገር እያወራረሰች ኖረች :: ብዙ የውሸት እምነት ፈለፈለች ኮተኮተች አሳደገች የምድርን ገጽ ሁሉ ከደነች :: እነካቶሊክ ፤ እነእስላም ፤ እነቡዲሂዝም ፤ እነሺንቶኢዝም ፤ እነ ፕሮቴስታንት እንዲሁም በራሺያ በቡልጋርያ በሩማንያ ጆርጂያ ወዘተ ››› በግሪክ በምስራቅ አውሮፓ የተንሰራፋው እርየንታል ኦርቶዶክስ / ውስጡ በምስጥ እንደተበላ እንጨት በካቶሊኮች በዲያብሎስ ስውር ሰራዊቶች ተበልተው ያለቁት / እነሂ ሁሉ እምነት ተብዬዎች ምድርን ሸፍነው ፤ እነሱም አንስው ፤ አንድም ሰው ወደ እግዚአብሔር ፊቱን እንዳይመልስ አድርገው የአዳም ዘርን በሙሉ ቀይደው ለዛሬው የመጨረሻ የልኡል የቁጣ እርምጃ ላይ እንዲደርስ አብቅተውታል :: ዲያብሎስ የፈጠራቸው መንግስታት በየዘመኑ የየድርሻቸውን የሃጢያት አዝመራ አምርተው ውጤቱንም ተቀብለው በፍርድ ተካተዋል :: ዛሬም ያሉት የዲያብሎስ ሃያል መንግስታት ፤ /የሉሲፈር አገልጋዮች ታማኞች / ፤ እግዚአብሔርን ሊዋጉ ተዘጋጅተው ፤ በሙሉ ጉልበታቸው ቆመዋል :: ዓለም በዚህ ሁሉ እድሜዋ ያላየችውን የጥፋት መሳሪያ ዓይነት ሰርተው ምድርንም ሰማይንም የውጊያ ወረዳ ሊያደርጉ ማሚሟቅ ጀምረዋል :: ልብ በሉ ሊዋጉ ነው: ዝግጅታቸውም ለዚሁ ነው :: ማንን? የፈጠራቸውን ምድርንም ሰማይንም ፍጥረትን ሁሉ እውን ያደረገውን

አምላካችንን ፤ እንግዲህ ዓለማችን ፤ በነማን ለጥፋት እንድትቆም እንደተደረገች ስላለፈው የትላንት ጉዞዋ የተገፉትን ማገንበብ ስለሚቻል በዚህ ጊዜ አናጠፋም ። ስለዲያብሎስ ሥውርም ገሃድም ተግባር ብዙ መገሕፍት ተፅፈዋል።

የሃያላኑ ሴራ በኢትዮጵያ ላይ ፤ ስለኢሉሚናቲ አሰራር አደረጃጀት ፤ ምድርን እንዴት እንደተቆጣጠሯት የሚነግሩን ስለሆነ ማገንበቡ አስፈላጊ ነው ።

እጅግ በትንሹ በእኔ በታናሽ ባሪያው በኩል ልኡል ያስተላለፈውን ፤ የትላንቱን የመጀመሪያ የፍርድ ቃል ብናይ እንዲህ የሚል ሃይለ - ቃሎች እናገኛለን ።

የመጀመሪያው መልእክት በሕዳር 7 ቀን 1998 ዓ ም ወጣ!

በእጅ ጽሕፈት 21 ገጽ በኮምፒዩተር 11 ገጽ ያለው ነው ።

አንዱ አንቀጽ እንዲህ ይላል ፤——

መልእክቱ አራት ክፍሎች አሉት

- ሰዘመናችን ጥበበኞች ፤ ገዢዎች ባለጠጎች ፤ የሃጢያት ባለሃብቶች ፤ አመንዝሪዎች ግብረ ሰዶሞች ነፍስ ገዳዮች ፤ ዘራፊዎች ነጣቂዎች ድሃ አጥፊዎች ፤ በጥቅሉ የቀደመው እባብ /ዲያብሎስ/ ልጆችና አገልጋዮች በግልጽ በእግዚአብሔር ሕግና ሥርዓት ላይ የማፍረስ ሥራ በመሥራት ፍጹም የጨለማን ሥራ ላነገሡ የዘመኑ አባቦች ፤ ዘንዶዎችንና ጊንጦችን ይመለከታል ።
- በእምነት ካባ ተጠልለው በተለያየ የእምነት ተቋም ራሳቸውን ያደራጁትን ማለትም እንደ ካቶሊክ ፤ ቤ/ክ ፤ ፕሮቴስታንት ፤ ኦርቶዶክስ ፤ አንግሊካን እናም ሌሎችን በክርስትና ስም ራሳቸውን ያደራጁ ተቋማትን ይመለከታል ። ሙስሊም ፤ ቡዲሂዝም ፤ ኮንፊሺያን ፤ ሂንዱኢዝም ፤ እናም ቁጥራቸው የበዛ የእምነት ተቋማትን ይመለከታል ።
- ምድሪቱ ላይ በሰፈነው ብርቱ ሃጢያትና ማእበሉ ዘወትር እየተሰቃዩ ላሉ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ይመለከታል ።
- ኢትዮጵያና ሕዝቦቿን ገዢዎቿን መጪውን እድሏን ይመለከታል ።
- ባጠቃላይ ዓለምን በሥራና ተግባሯ ተመስርቶ የሚጠብቃትን ቅጣትና ፍርድ ከዚያም ያለውን መፃኢ ሁኔታ የያዘ መልእክት የምታገኙ ሲሆን ይህንን መልእክት ለመስማት ባትወዱትም ወይም ባትፈቅዱትም የማይቀር ስለሆነ ፍርዱ በራሳችሁ ላይ የሚያርፍ ይሆናል ። የምትታመኑበት እውቀት ጥበብ ብልፅግና ፤ ወይም የሃሰት አባታችሁ በፍጹም አያድኗችሁምና !! ለበደለኞች የሞት ፍርድ መርዶአቸውን የሚሰሙበት ፤ ለመልካሞቹ የእግዚአብሔርን ታዳጊነትና የታመነ አባትነቱን የሚያረጋግጡበት ነው ።
- ከላይ ያያችኋቸው በመልእክት አንድ ውስጥ ከመጀመሪያው ገጽ ላይ የሚገኝ ቃል ነው ። መልእክቱ በ ሕዳር 7 ቀን 1998 ዓ ، ም የዛሬ 13 ዓመት ገደማ የተገፈ ነው ። መልእክቱ በእጅ ፅሑፍ በ21 ገጽ በኮምፒዩተር ፅሑፍ 11 ገጽ ያለው ነው ። መልእክቱ የልኡልን ትእግሥት አልቆ የመጀመሪያው የፍርድ
- የተገለጠበት ነው ።

## መልእክት ሁለትስ ?

ይህ መልእክት ግንቦት 27 ቀን 2000 ዓ.ም የተገፈ ነው ። ይህ መልእክት የሰው ልጅ በፍርድ ሂደት ሲሚገት በሂደቱም ቢረታ እንደገና ይግባኝ ብሎ ስለፍርዱ ቅሬታውን የሚገልጽበት ነው ። ልክ እንደዚሁ እንደሰውኛው የፍርድ ሂደት ሁሉ በልኡልም ፊት የመጀመሪያው መልእክት እንደወጣ ሰዎችም ቅዱሳን መላእክትም በምልጃ ምህረትን የጠየቁበት ነው ። ሆኖም የሰው ልጅ በፍርዱ ከመደንገጥ ይልቅ ወደማፈገዝ ወደመናቅ ወደትእቢት

ሄደ እንጂ ደንግጦ ወደ ንስሃ አልገባም ፡፡ በመሆኑም ልኡል ዳግም ውሳኔውን አፀና በዚህም መሰረት ይህ ሁለተኛው መልእክት ወጣ ፡፡ 19 ገጽን የያዘው ይህ መልእክት ያልዳሰሰው ነገር የለም ፡፡ ለአብነት ያህል አንድን አንቀጽ እንመልከት

በዚያ የመጀመሪያ መልእክት የሚገጥማችሁን በግልጽ ተነግሮአል ሥራችሁም ተገልፆአል የእሳት ባሕር ይጠርጋችኋል ፡፡ ይህም የዓለምን የሙቀት መጠን መጨመር እየተመለከትነው ነው ፡፡ በሳይንስ ትመልሰዋለህ ጠብቀው ፡፡ ለሚያስተውል ራሱንና ወገኑን የት እንዳሉ የሚያይበት መነጽር ነው ፡፡ አሁን ያ ወቅት ሳትጠቀምበት አልፎአል ፡፡ 2ኛ ዓመቱን አጠናቋል ፡፡ መጪው ምንድነው የሚለውን መመልከት ተገቢም አስፈላጊም ነው ፡፡ በመጀመሪያውም ሆነ በዚህ በሁለተኛው መልእክት የተገለፀው ሁሉ ይፈጸማል ፡፡ አንዳችም የሚቀር ነገር የለም ፡፡ ዓለም በተለያየ መጠን ባለው ችግር ውስጥ ወድቃለች ፡፡ ሙቀት ጨምሮአል ፤ ረሃብ ነግሶአል ፤ ግጭት በዝቶአል ፡፡ የአየር ንብረት ተለውጦአል ፡፡ ምድር ባህርይዋን ለውጣለች ፡፡ ይህ ሁሉ ልክ ነው ፡፡ ይኸው ጥፋት በብዙ መቶ እጥፍ በከፍተኛ መጠን ይጨምራል ፡፡ የዲያብሎስ ልጆች በእሳት ባሕር ለመጠረጋችሁ መጠራጠር የለባችሁም ፡፡ የቻይናን ምድር ያንቀጠቀጠና ያፈረሰ ፤ በርማን የጠረገ የቁጣ ምልክት ምን ይመስላችኋል ? እናንተ ጋ አይመጣም ? የሚያግደው አለ በሺ እጥፍ ይመጣልሀል ፡፡ እናንተ ሞት ሲውጣችሁ ብቻ ነው የሚገባችሁ ፡፡ስለዚህ ጠብቁት ይላል በዚህ መልእክትም ያለውን ሁሉ ለመጥቀስ ስለሚያስቸግር ፊልጋችሁ አንብቡት ፡፡

ወደ ሶስተኛው መልእክት ስንሄድ ፤ ———

ይህ መልእክት በሌላኛው አጠራሩ የአፈጻጸም መልእክት ተብሎ የሚጠቀስ ነው ፡፡ የወጣው በመጋቢት 19 ቀን 2001 ዓ.ም ነው ፡፡ ይህ አፈፃፀም 95 ገጽ የያዘ ሲሆን ፤ በመላው ዓለም ያሉ ሃገሮችን እጣ ፈንታ / በሁለቱ መልእክቶች አንፃር ምን እንደሚከናወን / የሚገልጽ ና ፡፡ ይህንን መልእክት ማግኘት ትናንት ዛሬ ነገም የሚሆነውን ከልኡል የተቆረጠውን ፍርድና አፈፃፀሙን መመልከት የሚያስችል መሆኑ ነው ፡፡

ቁጥር አንድም ቁጥር ሁለትም አብረውት የተካተቱበት መጽሐፍ አካልም ነው ፡፡

በዚህ መልእክት ውስጥ የዋና ዋና የእምነት ተቋማትን ምንነትና የሚገጥማቸውንም እጣ ፈንታቸውን የተብራራበትና የተገለፀበትም ነው ፡፡ በዚህ መልእክት ውስጥ ሰለሰው ባሕርያት ፤ ስለኢትዮጵያ የዓለም ብርሃናዊ መንግሥትነትና መሪነት የሚያረጋግጥም ነው ፡፡ በመላው ዓለም እንደአገር የሚታወቁ አገሮች ሁሉ ፍርዳቸው የተገለጠበት ነው፡፡ ይህንንም ፊልጎ ማንበብ ይጠቅማል ፡፡

አራተኛው መልእክትን ደግሞ ስናይ ——

ይህ መልእክት በአብዛኛው የሚያተኩረው በኢትዮጵያ ጉዳይ ላይ ነው ፡፡

የወጣው የካቲት 1 ቀን 2002 ዓ . ም ነው ፡፡

በዚህ መልእክት ስለተዋህዶ እምነታችንና በእምነታቸው ፀንተው ስለቆሙ የተገለፀበት አንዱ ሲሆን ከሁሉም በላይ በወቅቱ የአገሪቱ ዘረኛ መሪ በቀጥታ ለግላቸው የተፃፈላቸውን ሶስት ደብዳቢዎች የያዘም ነው ፡፡ ለሳቸው የተፃፈው ደብዳቤ ከሥልጣናቸው ስለመወገዳቸው ከልኡል የተሰጠውን ውሳኔ የሚገልጽላቸው ሲሆን

በተጨማሪ የቤተ / ክ መሪ ለነበሩት ፓትርያርክ በላያቸው ላይ ዲያብሎስ በሥጋቸው እንዲሰለጥን የታዘዘውም ሌላው ውሳኔ የተገለፀበት ነው ። ይህ መልእክት የዘረኛውን ጨካኝ መንግሥት ያፍረከረከና ዛሬም ወደውድቀታቸው እየነዳቸው ያለ ለመሆኑ ይህ መልእክት ሲወጣ የነበረውንና አሁን የደረሰበትን በግልፅ የምናይበት ነው ።

ከዚሁ አራተኛው መልእክት ለማስታወሻ ያህል አንድን አንቀፅ ላንሳ

በዛሬው መልእክቱ ይላል —

1ኛ የምትፅናኑበትን የምታርሙትን መሰረታዊ ጉዳይ በማንሳት ለመምከር

2ኛ ጊዜው በማለቁና በመፈፀሙ ሁለንተናዊ ዝግጅት እንድታደርጉ ለማሳሰብ

3ኛ በአሁኑ ሰአት አገዛዙን አክብዶ ያለው የኢትዮጵያ መንግሥት እድል ፈንታው መጠናቀቁንና ይህንንም የእግዚአብሔር ወዳጆች እንድታውቁ በዝርዝር ለማሳወቅ የተዘጋጀ የመጨረሻ የመሰናዶ መልእክት ነው ። ይላል ። በተረፈ በቂ ግንዛቤ ለመጨበጥ የምትፈልጉ ፈልጋችሁ ማንበብ ይጠቅማችኋል ።

አምስተኛው መልእክትስ ምን ይላል ፡——

አምስተኛው መልእክት በመስከረም 21 ቀን 2004 ዓ . ም ነው የተፃፈው ። 41 ገጽም ያለው ነው ።

መልእክቱ ለመላው የአዳም ዘር የተፃፈም ነው ። መልእክቱ ቀደም በወጡት መልእክቶች የታዘዙትን ቅጣቶች ወደ ከፍተኛ ደረጃ እንዲያድግ የታዘዘበትም ነው ።

ለማገናዘቢያ እንዲረዳ ከመልእክቱ አንድን አንቀፅ እናነሳለን ።

አመፃ ትእቢትን ትቀድማለች ። በትእቢት ፤ በንቀት ፤ የተሞላችሁ የዘመናችን ገገርዎች አለቆችና ጭፍሮች የልኡልን ምክር ፍርድና እርምጃ ንቃችሁ ፤ ዛሬም እንቋቋማለን በሚል የአባታችሁ የዲያብሎስን ምክር ሰንቃችሁ እጅግ ወደከበደው እሳትና ጨለማ እየተንደረደራችሁ ትገኛላችሁ ። የእግዚአብሔር እጅ አይዝል አይደክም በከንቱ ትፍረመረማላችሁ እንጂ እየደቀቃችሁ ከመፈፀም አንዳች የሚታደጋችሁ የለም የሰው ዘር ልብ ልትል ሲገባህ በአመፃህ ገፍተህበታል ። በወቀሳው አልተፀፀትክ ፤ በፍርዱም አልደነገጥህ የፍርዱ የአፈፃፀም የመጀመሪያ ደረጃ እርምጃ ዓለምን ሲያናውጥ ያንተ ድንጋይ ልብ ግን ዛሬም በልኡል ቁጣ ነዳጅን ያርከፈከፋል ።

ለማስታወሻ ያህል ከላይ ያነሳሁት አንድን አንቀጽ ብቻ ሲሆን ሁሉንም ብታነቡት ስለመልእክቶቹ በቂ ግንዛቤ እንዲኖራችሁ ያደርጋል ።

ወደ ስድስተኛው መልእክት ስንዘልቅ ደግሞ ፡ ——

ስድስተኛው መልእክት፡ — ይህ መልእክት የወጣው በ ታህሣሥ 19 ቀን 2007 ዓ.ም ነው ።

መልእክቱ በዋናነት አዋጅ ነጋሪ ነበር ። አዋጁ በመጪው የትንሳኤው ዘመን ዓለምን በበላይነት የሚያስተዳድረውን የሽግግር ሕግጋት - ሥላሴ እና ቋሚውን ሕግጋት - ሥላሴ ለማወጅ የተዘጋጀ ነው አዋጁ ለሕዝብ አልተገለፀም ምክንያቱ ደግሞ ፤ የተዘጋጀውም የሚገለጠውም ለትንሳኤው ዘመን ለሚደርሱትና በዚያው ዘመን ይኖሩበት ዘንድ እድሉ ለተቸራቸው ብቻ ነው ።

ዛሬ የምናየው ትውልድ / በመላው ዓለም ያለው ሁሉ / ፈጣሪውን የካደ ፤ በተለያዩ የዲያብሎስ ድርሰት እምነቶች ውስጥ የሰመጠ ፤ አመንዝሪ ግብረሶዶም ፤ ትእቢተኛ ፤ ውሸታም ፤ ኢታላይ ከሃዲ ፤ ጨካኝ ፤ ነፍሰ ገዳይ ፤ ዘረኛ ፤ አምልኮ ባእድ የሚወድ ፤ ተብታቢ ፤ ሌባ ወዘተ ...... ነው ።

ይህ ትውልድ ደግሞ ቢነግሩት የማይሰማ ፤ ቢወቅሱት ቢገስፁት የማይለማ ከእንስሶች በታች አድርጎ ራሱን የጣለ ነው ።

ከላይ ከ 1 – 6 የተጠቀሱት መልእክቶች ሁሉም ይህን የጠፋና በድቅድቅ ጨለማ ውስጥ የወደቀ ትውልድ ለማዳን ፤ ከመጣበት እሳትና ቁጣ እንዲድን ለመምከር ነበር ሲገለጹ የኖሩት ። ግን ሁላችሁም የልኡል ባሮች እንደምትመሰክሩት በመላው ዓለም ሰፍሮና እየኖረ ያለ ትውልድ በፍፁም የማይደነግጥ የታበየ ከሃዲ የቁስ አምላኪ ውሸታምና ዘረኛ ትውልድ ነው ። ፈጣሪውን ከናቀና እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስን የሚሳደብ ለጥፋቱ የሚተጋ ትውልድ በመሆኑ ለዛሬው የመጨረሻው ሰዓት ደርሶል ።

እንግዲህ ስለቀደመው ዓለማችንና ስለመልእክቱ ፤ የሰው ልጅ በንቀት ሳይጠቀምበት በመቅረቱ የመጣውን ይህን የመጨረሻ ቁጣ ለማየት የሚያስችል መጠነኛ ግንዛቤ አግኝታችኋል ብዬ እምናለሁ ።

ወገኖቼ የእግዚአብሔር ሕዝቦች !!

በጥፋቱ ጎዳና በመገሥገሥ ላይ ያላችሁ የአዳም ዘር ሁሉ !!

ዛሬን በምንም መልክ እንየው በምንስ እንመስለው ለሁላችንም የሚታይ የሚዳሰስ ፤ ያልተሸፈነ እውነት የምናይበት የምንመሰክረው እነደሆነ ከርክር የሚያስነሳ አይደለም ።

ዓለም ዛሬ ምን ላይ ነች ? ወዴትስ እየገሰገሰች ነው ? በምድሪቱ የተበተነው የአዳም ዘር ሁሉ ዛሬንም ነገንም እንዴት ያያል ? የዓለማችን መንግስታት ፤ ታላላቅ ነን ባይ እምነቶችስ ምን ይሰራሉ? ስለወቅቱስ ምን ይላሉ ? ለሚከተላቸው ሕዝብስ ምን አስጨብጠውታል ? ይህን ሁሉ ከዳሰስን በኋላ ፤ ስለእውነተኞቹ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ጥቂት እንስተን ዓለም ከሚሸነግሉአት ይልቅ ለፈጣሪያችን ቅርብ ከሆኑና ከታመኑ የልኡል ባሮች በኩል የልኡል እርምጃ ምንድነው ፤ የሚለውን እንሰማለን ።

ጩህ የሚል ሰው ቃል ምን ብዬ ልጩህ አልሁ —ሥጋ ለባሽ ሁሉ ሳር ነው ።

ከብሩም ሁሉ እንደ ምድረ በዳ አበባ ነው ። የእግዚአብሔር እስትንፋስ ይነ

ፍስበታልና ! በእውነት ሕዝቡ ሳር ነው ። ሳሩ ይደርቃል ፤ አበባውም ይረግ

ፋል ። የአምላካችን ቃል ግን ለዘለአለም ጸንታ ትኖራለች ።

ትንቢተ ኢሳኢያስ ም ፤ 40 ፡ 6 – 8

ወገኖቼ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ፤—— ልኡል ሊያደርግ የወሰነውን ነገር ለልጆቹ ሳይገልፅ አንዳች ነገር አድርጎ አያውቅም / እነአብርሃም ፤ እነኖሕ ፤ እነሙሴ ወዘተ ››› / ቋሚ ምስክሮቻችን ናቸው ።

ታሪክ እራሷን ትደግማለች ይላሉ አንዳንድ ፀሐፍት ፤ አባታችን ኖሕ ስለጥፋት ውሃ መምጣት ለሰው ልጅ ሁሉ በመግለፅ ሲሯሯጥ ሰሚው ጠፊ ትውልድ ሃጢያት ያጠለቀው ትውልድ እንኳን ሲሰማው ቀርቶ ፤ ለራሱና ሲደት ለተፈቀደላቸው መጠለያ መርከብ ሲያበጅ ሲመለከቱ በድርጊቱ በመደነቅ ዛሬ እንደምናየው/ ሲኒማና ትያትር ሳይከፍሉ/ ይዝናኑና ይስቁ ነበር :: እጅግ ተደስተውም ያፌዙ እንደነበር ሁላችሁም ከልኡል ቃል የሰማችሁት እውነት ነው ::

ኖሕ አባታችን በፌዛቸው ሳይደነቅ ስለአጠፋፋቸው በማዘን ዘወትር ተመለሱ በማለት ብዙ ዓመታትን አሳልፎ ነበር :: ዛሬስ ? ብዙ ኖሆች ፤ ብዙ አብርሃሞች ፤ ብዙ ኤልያሶች የዛሬውን / ለመጨረሻው ጥፋት የደረሰውን ትውልድ/ ጩኸኝ ስብእናውን ከእንስሳ በታች የጣለ ፤ የጠፋ ዘር ለመመለስ ያልጣሩት ያልደከሙበት መንገድ አለ የለም? :: ማን ይስማ ፤ ራሱ ልኡል ቢመጣ ያልተመለሰ ትውልድ ልኡልም ድንግልም ቅዱሳን መላእክትም ፤ ሰማእታትም ቢጨመሩበትም አልሰማም :: እንግዲህ ሥላሴም ድንግልም ለሰው ካላቸው ፍቅር ተነስተው በጉጉት አንድ ቀን ይጸጸታል በማለት ያልታገሱበት የዘመን ክስተት የለም አልነበረምም ::

አባታችን ኖሕ ቁጣው ሲመጣ ጠፊዎቹ ቢያፌዙበትም እሱ ግን ከመንገዱ ፈቅ ሳይል እነሱም ከእልቂታቸው ሳይድኑ ለአንዴም ለመጨረሻውም ተከደኑ ::

ወገኔ የዘመናችን ትውልድ ስትመከር ሥትገሰፅ ስትቀጣም የማትሰማ አላጋጭ ፌዘኛ ትውልድ ከጠፋው የኖሕ ዘመን ትውልድ በብዙ እጥፍ የምትበልጠው ከንቱ ትውልድ ምን ይበጅሃል ? ልኡል እጁን ዘርግቶ ና ልጄ ብሎ በታላቅ ትእግስት ስንት ዘመን ጠበቀህ ? ታውቀዋለህ ? 2011 የምህረት ዘመን 5500 የሕገ ልቡናና የህግ ዘመን በጥቅሉ ከ 7500 ሺ ዓመታት በላይ ጠበቀህ ፤ ታገሰህ ፤ መከረህ ፤ገሰጸህ ፤ ቀጣህ ብትመለስ ብሎ እጅግ ውድ ዋጋ ከፈለልህ :: ልጆቹን ስትጨርስ ፤ ስትገል ስታሳድድ ፤ ስታስር እየቆሰለ ታገሠኋል ተስፋ እስከሚቆርጥበት ድረስ እድሜን እየሰጠ ታገሰህ :: ይህ ሁሉ ሆኖ መቼ ፍንክች ልትል ዲያብሎስን ታምነሃላ ! ምድርን ቅራቅንቦህን አለኝ እምትለው ጥበብህን እሱው በፈጠረልህ አእምሮ ተጠቅመህ በሰራኸው ሰው ጨራሽ መሳሪያ ፤ እንዲሁም በሕዋ ላይ በሰቀልከው ሳተላይት ልትወጋውም ወስነሃል እንግዲህ መልሱ ምን ይሁን አንተም ታውቀዋለህ ወገብህን ታጥቀህ መጠበቅ ነው :: ታየዋለህ እኛም የልኡል ባሮች በሱ ታምነን ያለን ሁሉ ፤ ከአንተ ጥፋት እንዴት እንደሚታደገን እንዴትስ ልጆቹን እንደሚያከብር ወደከፍታውም እንደሚያወጣ ትመለከተዋለህ :: አንተንም የዲያብሎስ ታማኝና ተስፈኛ እንዴት እየቀቀለህ በእሳት ባሕር እየጠረገ ከታመንክበት ኩታንኩትህ ጋር ወደትቢያነት እንደሚቀይርህ ታየዋለህ!

አሁን የመዋቀሻ ፤ ተመለስ አትመለስ ፤ ተገሰፅ ተወቀስ ፤ ተለመን ተብሎ የሚጠየቁበት የሚዘከሩበት ጊዜ አይደለም :: ይህም ሁሉ አልፎ ለ13 ዓመት ፍርድ ተሰጥቶ ተጠብቆ ውጤት ጠፍቶ ከተደመደመ በኋላ ከልኡል እንደ እሳተ ጎሞራ ከሚነደው ቁጣው መሃል የሚቆም የሚሸመግል የሚዳኝስ ማነው ? ሁሉ ሰማያዊውም ምድራዊውም ዘዴና መፍትሄ አልቆአል :: መላው የልኡል ባሪያ ሁሉ እግዚአብሔር ወደመራው መጠለያው ተሸሽጎአል :: ለራሱ ፈርቶ ሳይሆን ያንተ የዲያብሎስ ተስፈኛ አጠፋፍ እጅግ አስደንጋጭ በምድራችን ታሪክም ያልታየ ያልተሰማ በመሆኑ መመልከቱም መስማቱም ስቅጣጭ ሕሊናን የሚሰቅዝ እጅግ የሚያብረከርክ በመሆኑ እንደኖሕ አባታችን ቤቱን ዘግቶ መከተት ብቻ መሆኑን አውቆ የተቀመጠ ነው ::

በሶዶም ዘመን ልኡል ሶዶምን ሲጎበኝ ደፋሮቹ ሶዶማውያን በሎጥ ቤት የተገኙትን ቅዱሳን መላእክትን ሎጥ እንዲያወጣላቸው የጠየቁ ጉዶች ነበሩ :: ወዲያው የመጣው መልስ ምን እንደ ነበር ታውቃላችሁ ሁሉም ሶዶማዊ የእሳት እራት ሆኖአል :: ትውልድ እንዲማርበት ዛሬ ድረስ ያ ቦታ የዮርዳኖስ ሸለቆ ተብሎ በውስጡም ያለው የሙት ባሕር ተብሎ ይታወቃል

የወቅቱ ሶዶማውያን እንደ ፈፀቸው ፤ እንደ አርኩሰታቸው ፤ እንደጥጋባቸው እሳት በላቸው ፡ ሎጥና ልጆቹ ግን ከቁጣው አምልጠዋል ::

አንተስ የዘመናችን ሶዶም ሶዶማዊ !! ሌዝቢያን አመንዛሪ ፤ ከእንስሳ ቤታች ሰብእናህን ያወረድክ ማን ያስጥልሃል ? በወንጀልህ ሶዶምን ያጸደቅህ እኮ ነህ !! እነሱስ ሶዶማዊ ነበሩ አንተ ግን እነሱ የተኮነኑበትን እንደ አንድ ትንሽ ጉዳይ ደርበኸዋል :: ሶዶምነት በሕግ አፅድቀሃል ፡ ያልተከተሉህን አገሮች አስገድደህ እንዲቀበሉ አድርገሃል :: ምንዝርናን ኢንዱስትሪ አድርገሃል :: የሰውን ልጅ እንደሸቀጥ ቆጥረሃል :: ክቡሩን የሰው ልጅ ለምትታመንበት ዲያብሎስ ዘወትር መስዋት / ጭዳ/ አድርገሃል :: በተረት እምነቶችህ ፤ በፍልስፍና የተሸሞነሞኑ ሃይማኖትህ ፤ በግልጽና ቅንጣት ሃፍረት ባጣ ትእቢትና ክህደትህ ዲያብሎስን የሚያሞግሱ የሚያወድሱ የሚያስመልኩ ስመ ብዙ ዓለም አቀፍ ድርጅቶችን ፈጥረሃል አሁንም ድረስ ታምነህበታል አንግሰሃል ፤ ሕዝብና ሕዝብን አፋጅተህ ዘረኝነትን በየዘርፉ ተክለህ ሕዝብና ሕዝብን ታጫርሰሃል ዛሬም መጠንና ዓነቱን አራቅቀህ ተግብረሃል ፤ ያንተ የዛሬው ትውልድ ጉድ ተዘርዝሮ ማለቂያ የሚበጅለት አይደለም ይህን በዚህ ገታ ላድርግና !! ስለአባታችን ሙሴ እንመልከት ::

በዘመነ ሙሴ ልኡል የእግዚአብሔር ሕዝቦችን እስራኤላውያንን ሲታደግ ፤ እጅግ በሚደንቅ ትድግናው እስራኤልያውያንን ከፈርኦን ሰንሰለት ነፃ አውጥቶአቸዋል :: የነሱ ነፃ መውጣቱ ብቻ ሳይሆን የሚደንቀው የፈርኦን አለቃና ምንዝሩ የደረሰባቸው ጥፋት ትእቢትና ልበ ደንዳናነት እንዲሁም ጣኦት አምላኪነት በእግዚአብሔር ፊት ምን ያህል ዋጋ እንደሚያስከፍሉ ከመሰረት እንደሚነቅሉ የታየበት የታሪካችን ክስተት ሆኖ አልፎአል :: ያንን ሁሉ ድንቅ የማዳን ሥራ ደጋግመው ሲንቁ ሲያቃልሉ የነበሩ እስራኤላውያን ለኛ ለዛሬው ትውልዶች ምን ትምህርት እንደሚሰጡን የሁሉም ሕሊና ይመርምረው :: እስራኤላውያን ነጻ ከወጡበት የግብጽ ምድር ሲወጡ በአስፈሪነት በምርኮ በሃብት በብር በወርቅ ስጦታ ታድለው ነው :: ልኡል ከዚህም በላይ የኤርትራን ባሕር ከፍሎ እነርሱን አሻግሮ በትእቢቱ እንደገና ገንፍሎ የመጣውን የፈርኦን ጦር በኤርትራ ባሕር አስጥሞ የአምላክነቱን የታዳጊነቱን ሃይል አሳይቶአቸዋል ::

ጠማማው የእስራኤል ሕዝብ ግን ለክህደት ጊዜ አልፈጀበትም :: እንደገና ግብጽን ተመኘ ፈጥኖም ወደግብጻውያን አምልኮ ባእድ ተመለሰ :: ልብ በል ወገኔ ታአምሩን ትድግናውን ቸርነቱን ያየው ያ የእስራኤል ሕዝብ በክህደቱ የልኡልን ትእግስት በብርቱ በመገዳደሩ ልጆቹ የተገባለትን ምድር ወረሱ እንጂ እሱ ግን በበረሃው ቀረ :: ጧትም ማታም ከልኡል ፈቃድ ጋር መጋጨት ስራው ነበርና ፍጻሜው በበርሃ መቅረት ሆነ :: እግዚአብሔርን የሚገዳደር የሚፈትን ትውልድ ፍፃሜው በበርሃ መቅረት ነው :: ልክ የዛሬው ትውልድ መጥቶ መጥቶ ከገደሉ አፍ ላይ እንደቆመ ሁሉና በትእቢት ተሞልቶ መገፍተሩን እንደሚጠብቅ ሆኖ ላለነው የመጥፋት ምንነት ምስክር ሊሆን ቀርቦአል ::

እንግዲህ ወገኔ ስለስንቱ እናንሳ ስለኢያሱ ፤ ስለኤልያስ ፤ ስለንዳዊት ሁሉንም ታውቃቸዋለህ ፤ ልብ ብለህ አድምጥ ! ምንም መጥፊያህ ላይ ብትደርስም በሞትህ ጉዞ ውስጥ እውነትን እየሰማህ ወደመደምደሚያህ መድረስ አለብህ :: ባንተ ቀሪው የልኡል ሕዝብ የሚማርበትን ታሪክና ገድል ከአንተ ተሞክሮን ይጨብጣል :: ለሕይወቱና ለልጆቹ ማስተማሪያ ግብአት እንዲሆን ወደትንሳኤው ዘመን ይዞትም ይሻገራል :: አንተም እንደ እስራኤላውያን አባቶች በጥመታቸው በክህደታቸው በየበረሃው ወድቀው እንደቀሩት ትሆናለህ :: መላው የአዳም ዘር ! አንተ የዛሬው ትውልድ ምን እንበልህ ምንም ማለት አንችልም በቃ ! አከተመ ! ተደመደመ ! ስለአንተ ማሰብም መስማትም የማይቻልበት ፍፁም የሚዘገንንበትም ወቅት ላይ ደርሰናል :: እንግዲህ ዲሞክራሲህን ፤ የዲያብሎስ ድርሰትህን የታበይክበት ሥልጣኔህን የከመርከው መሳሪያና ሃብትህን ሁሉም ላይታደጉህ ሲተኑ አንተም ዘር ማንዘርህም ከአባትህ ከዲያብሎስ ጋር አሁኑኑ ስትካተት ታየዋለህ :: እውነቱ ይህ ነው ::

የእግዚአብሔር ሕዝብ መፋረጃ ነው ። ብትወደውም ብትጠላውም እንዳንተው ሰው ነው ልዩነቱ እሱ በፈጠረው አምላኩ ይታመናል አንተ ደግሞ በፍጡሩ ዲያብሎስ ትታመናለህ ትመካለህ ። ልብ በል የእግዚአብሔር ሕዝብ ፤ በልኡል ፊት የከበረ የሚወደድ ነው ። ቁጥር በእግዚአብሔር ዘንድ ትርጉም የለውም ። በዘመነ እስራኤል በኤልዛቤልና በአክዓብ ንግሥና ዘመን የእስራኤል ሕዝብ ፤ እግዚአብሔርን እንዲያገለግሉ የተመረጡት ካሕናት ሁሉ እግዚአብሔርን ክደው ቡኤል ዘቡኤልን አንግሰው በሚያመልኩበት ዘመን የታመነው የእግዚአብሔር አገልጋይ ኤልያስ ብቻ ነበር፤ በአደባባይ ወጥቶ በአምላኩ በሠራዊት ሁሉ ጌታ ስም የተፋለማቸው ። ታዲያ እግዚአብሔር ቁጥር ገደደው በፍፁም ! ቢቃሉ የታመነው አምላካችን ከኤልያስ ጎን ቆመ እንጂ በቁጥር ምድርን ከሸፈኑት እስራኤላውያን ጎን አልቆመም ። እግዚአብሔር እውነት ነው ስሙም ያው እውነት ነው ፤ ቅንም ነው እውነተኛ ዳኛም ነው ለማንም ፊት አይቶ የማያዳላ ነው ። ፍቅርም ነው ስሙም ያው ፍቅር ነው ። / እንዲያ በመሆኑ ነው 7500 ዓመታትን የተሸከመን/ ቸር ነው እየበደልነው ተሸክሞ አኑሮናል ከዘመን ዘመን አሸጋግሮናል ።

ወገኖቼ !! የእግዚአብሔር ሕዝብ ውሃ ልክ ነው መፋረጃም ነው ። መለኪያ ነው ። ስለመርዶኪዎስ ስለነዳንኤል ስለነሕዝቅኤል ስለነዳዊት ወዘተ »»»»» በእግዚአብሔር ቃል ውስጥ መንፈሳዊ ሕይወታቸው እንደከዋከብት የሚያበራ ሆኖ ተመዝግቦአል ። የእግዚአብሔር ሕዝብ ውሃ ልክ ነው ። ለሌላው የአዳም ዘር ሁሉ እኩል የተዘራውን የእግዚአብሔር ቃል የሰማ ቢሆንም በትክክል የተቀበለው እንደቃሉ ሆኖ በተዋህዶ ኦርቶዶክስ እምነት ፀንቶ ፤ ከመላው ዓለም ሕዝብ አንፃር በቁጥር ኢምንት ቢሆንም በልኡል ፊት ግን የተወደደ ሆኖአል ። ብዙ እምነት እንደጎርፍ የሚፈስባት ምድራችን ሁሉንም አንግሣ የተዋህዶ እምነትን ብቻ እንደጠላት ስታሳድድ ኖራለች ። ያ የምታሳድደው ሰው ደግሞ እግዚአብሔርንና ቃሉን በሕይወታቸው አንግሰው በእለት ተእለት ሕይወታቸው የሚመላለሱ ናቸው ። ብርሃናቸው በሰው ሁሉ ፊት እንዲበራና ምሳሌም እንዲሆን ተደርጎ በልኡል የተቀረፀ በመሆኑ ዛሬም በእግዚአብሔር በስስት የሚታዩ ልጆቹ ናቸው ።

ኖሕ ምድርንና በወቅቱ የነበረውን አመፀኛ ሕዝብ በእምነቱ ፅናት እየኮነነ እግዚአብሔርም በዚህ በእውነት ላይ በቆመ ውድ ባሪያው በኩሉ ለማይታዘዘው ለአመጸው ትውልድ ፍርዱንና ወቀሳውን ሲያስተላልፍ ኖሮአል ። ውሃ ልኩ ኖህ በጽድቅ ሥራው ዓለምን ኮንኖአል ።

የልኡል ባሪያ ታማኙና ቀናኢው ኤልያስ በዘመኑ ውሀ ልክ ሆኖ አልፎአል ። ኤልያስ እስራኤላውያን እጅግ ባመፁበት ዘመን ስለእግዚአብሔር ቃል ፀንቶ በመቆም እንደ ፀሐይ ያበራ የእምነት ጀግና ነው ። በጽድቅ ሥራው እንደፀሀይ በሚያበራ ሕይወቱ ልኡልን በሕይወቱ ያነገሰ ጀግና ነው ። ኤልያስ በዚያ ክፉ ዘመን ስደቱንም ረሃቡንም ሁሉንም የጠላት ጥቃት የተቀበለ የልዑል ባሪያ ነው ።

እስራኤላውያን በዘመናቸው ሁሉ በእግዚአብሔር ላይ ማመጽን የሚያዘወትሩ ነበሩ ። በንግሥት ኤልዛቤልና በንጉሥ አካብ ዘመን ሁሉንም ካሕናት ጨምሮ መላው የእስራኤል ሕዝብ አምላኩን ክዶ ነበር ። እግዚአብሔር በስውር ከጠበቃቸው የታመኑ ልጆቹ በስተቀር ሁሉም እስራኤላውያን ቡኤል ዘቡኤልን የሚያመልኩና ንጉሱም ንግስቲቱም በዚሁ ጣኦት ፍቅር የተለከፉ ነበሩ ።

የልኡል ቃል በመጽሐፈ ነገሥት ቀዳማዊ ፤ ምዕ ፤ 18 ፡ 15 – 40 እንዲህ ይላል!!

ሆኖም የእግዚአብሔር ባሪያ ኤልያስ ስለአምላኩ ታላቅ ቀናኤ ነበርና በስሩ ከሚያገለግለው አንዱ የሆነውን አብዲዩን ኤልያስ እንዲህ አለው ፤—— በፊቱ የቆምሁት ሕያው እግዚአብሔርን እኔ ዛሬ ለእርሱ እገለጣለሁ / ለአክአብ/ አለ ።

ዓብዱዩም አክአብን ሊገናኘው ሄደ ፤ ነገረውም ። አክአብም ኤልያስን ሊገናኘው መጣ ። አክአብም ኤልያስን ባየው ጊዜ – እስራኤልን የምትገለባብጥ አንተ ነህን ፡ አለው ። ኤልያስም — እስራኤልን የምትገለባብጡ

የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ትታችሁ በአሊምን የተከተላችሁ አንተና የአባትህ ቤት ናችሁ ፡ እንጂ እኔ አይደለሁም ። አሁንም ልከህ እስራኤልን ሁሉ በኤልዛቤልም ማእድ የሚበሉትን አራት መቶ ሃምሳ የበአልን ነቢያት አራት መቶም የማምለኪያ አፀድን ነቢያት ወደ እኔ ወደ ቄርሜሎስ ተራራ ሰብስብ አለ ።

አክዓብም ወደ እስራኤል ልጆች ሁሉ ልኮ ነቢያቱን ሁሉ ወደ ቄርሜሎስ ተራራ ሰበሰበ ። ኤልያስም ወደ ሕዝቡ ሁሉ ቀርቦ — እስከመቼ ድረስ በሁለት ሃሳብ ታነክሳላችሁ ፤ እግዚአብሔር አምላክ ቢሆን እርሱን ተከተሉ ፤ በአል ግን አምላክ ቢሆን እርሱን ተከተሉ አለ ። ሕዝቡም አንዲት ቃል አልመለሱለትም ። ኤልያስም ሕዝቡን አለ — ከእግዚአብሔር ነቢያት እኔ ብቻ ቀርቻለሁ ፤ የበአል ነቢያት ግን አራት መቶ ሃምሳ ሰዎች ናቸው ። ሁለት ወይፈኖችን ይስጡን እነርሱም አንድ ወይፈን ይምረጡ እየበለቱም ይቁረጡት በእንጨትም ላይ ያኑሩት በበታቹም እሳት አይጨምሩ ፤ እኔም ሁለተኛውን ወይፈን አዘጋጃለሁ በእንጨቱም ላይ እኖረዋለሁ ። በበታቹም እሳት አልጨምርም እናንተም የአምላካችሁን ስም ጥሩ እኔም የእግዚአብሔርን ስም እጠራለሁ ስምቶም በእሳት የሚመልስ አምላክ እርሱ አምላክ ይሁን ። ሕዝቡም ሁሉ —— ይህ ነገር መልካም ነው ብለው መለሱ ።፤

ኤልያስም የበአልን ነቢያት —— እናንተ ብዙዎች ናችሁና አስቀድማችሁ አንድ ወይፈን ምረጡና አዘጋጁ የአምላካችሁንም ስም ጥሩ በበታቹም እሳት አትጨምሩ አላቸው ። ወይፈኑንም ወስደው አዘጋጁ ። ከጠዋትም እስከ ቀትር ድረስ —— በአል ሆይ ስማን እያሉ የበአልን ስም ጠሩ ። ድምጽም አልነበረም ፤ የሚመልስም አልነበረም ። በሰሩትም መሰዊያ ዙሪያ እያነከሱ ያሸበሽቡ ነበር ። በቀትርም ጊዜ ኤልያስ —— አምላክ ነውና በታላቅ ቃል ጩሁ ምናልባት ሃሳብ ይዞታል ፤ወይም ፈቀቅ ብሎአል ። ወይም ወደ መንገድ ሄዶአል ። ወይም ተኝቶ እንደሆነ መቀስቀስ ያስፈልገዋል ። እያለ አላገጠባቸው ።በታላቅም ቃል ይጮሁ ፤ እንደ ልማዳቸውም ደማቸው እስኪፈስስ ድረስ ገላቸውን በካራና በቀጭኔ ይቧጭሩ ነበር ። ቀትርም ካለፈ በኋላ መስዋእተ ስርክ እስኪደርስ ድረስ ትንቢት ይናገሩ ነበር ። ድምጽም አልነበረም የሚመልስና የሚያደምጥም አልነበረም ።

ኤልያስም ሕዝቡን አለ — ወደ እኔ ቅረቡ አላቸው ሕዝቡም ሁሉ ወደ እርሱ ቀረቡ የነበረውንም የእግዚአብሔር መሰዊያ አበጀ ። ኤልያስም — ስምህ እስራኤል ይሆናል የሚል የእግዚአብሄርን ቃል እንደ ደረሰለት እንደ ያእቆብ ልጆች ነገድ ቁጥር አስራ ሁለቱን ድንጋዮች ወሰደ ። ከድንጋዮቹም ለእግዚአብሔር ስም መሰዊያ ሰራ ፤ በመሰዊያውም ዙሪያ ሁለት መስፈሪያ እህል የሚይዝ ጉድጓድ ቆፈረ ። እንጨቱንም በተርታ አደረገ ወይፈኑንም በብልት በብልቱ ቆረጠ ። በእንጨቱም ላይ እኖረና — አራት ጋን ውሃ ሙሉ በሚቃጠለው መስዋእትና በእንጨቱ ላይ አፍስሱ አለ ። ደግሞም ድገሙ አለ ። እነርሱም ደገሙ ። እርሱም ሶስተኛ አድርጉ አለ ። ሶስተኛም አደረጉ ፡ ውሃውም በመሰዊያው ዙሪያ ፈሰሰ ። ደግሞም ጉድጓዱን በውሃ ሞላው ።፤ መስዋእተ ሰርክ በሚቀርብበት ጊዜ – ነብዩ ኤልያስ ቀርቦ —— አቤቱ የአብርሃምና የይስሐቅ የእስራኤልም አምላክ ሆይ ፤ አንተ በእስራኤል ላይ አምላክ እንደሆንህ እኔም ባሪያህ እንደሆንሁ ይህንንም ሁሉ በቃልህ እንዳደረግሁው ዛሬ ይገለጥ ። አንተ አቤቱ አምላክ እንደሆንህ ልባቸውንም ደግሞ እንደመለስህ ይህ ሕዝብ ያውቅ ዘንድ ስማኝ አቤቱ ስማኝ አለ ። የእግዚአብሔርም እሳት ወደቀች ። የሚቃጠለው መስዋእቱንም እንጨቱንም ድንጋዮቹንም አፈሩንም በላች በጉድጓዱ ውስጥ ያለውንም ውሃ ላሰች ። ሕዝቡ ሁሉ ያንን ባዩ ጊዜ በግምባራቸው ተደፍተው እግዚአብሔር እርሱ አምላክ ነው ፤ እግዚአብሔር እርሱ አምላክ ነው አሉ ። ኤልያስም ከበአል ነቢያት አንድ ሰው እንዳያመልጥ ያዙ አላቸው ። ያዙአቸውም ኤልያስም ወደ ቂሶን ወንዝ ወስዶ በዚያ አሳረዳቸው ።

ይላል የልኡል ቃል ! የእምነት አርበኛው ኤልያስ ማን እንደነበር በጥቂቱ አየን ።

ወገኖቼ ! የእግዚአብሔር ሕዝቦች ! ይህ መልእክት ስለእናንተ ተፃፈ እንጂ ስለ ጠፋው የዛሬው ትውልድ አይደለም ። ቢመከር ቢዘከር ፤ ቢወቀስ ቢገሰፅ ፤ ቢቀጣ ቢመታ ፤ ምንም መስሚያ ያጣ ጉደኛ በሰው ታሪክ

ያልታየ ትውልድን ከእንግዲህ ለመመለስ ታስቦ አይደለም ። ያሁሉ ሆኖ አልፎአል ። ስለ ውሃ ልኩ የእምነት አርበኛው ኤልያስ ቢነገር ቢነገር አይጠገብም ። ወገኖቼ ! ያ ሁሉ ነቢያት አልቆ ብቻውን የቀረው የእምነት አርበኛው ኤልያስ ሥፍራውን አለቀቀም መላው የመንግሥት ሃይል ሁሉ ቢሰማራበት እንደ የእስፈላጊነቱ የመንፈሳዊ ውጊያ ስልቱን በመቀያየር ሲበረታ ለማጥቃት ሲደክም የመከላከል ሥፍራ በመያዝ ጠላቱን ሁሉ ሲፋለም አሳልፎአል በመጨረሻም የድል ባለቤት ሆኖአል ። እምንታመንበት አምላክ ከቃል ኪዳኑ አይዘንፍም ፤ እርግጥ በኛ እሳቤ የዘገየ ይመስለናል አይደለም ቀድሞም ባላትና ፈቃዱ ባፀናት ሰዓት ይደርሳል ። አሁንም እነሆ ደርሶአል ።

ወገኖቼ የእግዚአብሔር ምርጦች አንዱን የእምነት አርበኛ ላንሳ ! ብዙውን እንደምሳሌ የማነሳቸው የእምነታችን አርበኞች ለዛሬው ለምናየው መከራና ፈተና በምሳሌነት ይመስላል ያልኩትን ብቻ እንጂ ሁሉን ለማንሳት በዚች አጭር ጽሑፍ አይቻልም ። መርዶኪዎስን ላንሳውና ወደ ሌላ ጉዳዮችን እንመለስ ።

መርዶክዮስ የእስራኤል ሰው አይሁዳዊ ነበር ። በዘመኑ እስራኤላውያን በናቡከደነፆር ተወረውና ተማርከው ተበትነውም በከባድ ሕይወት ውስጥ ይኖሩ ነበር ። መርዶክዮስ የተማረከው የእስራኤል ንጉስ ወታደር ነበር ። ከተማረኩትም ወታደሮች አንዱ እሱ ነበር ። እናትና አባቷን በወረራው ያጣችው ሀደሳ/ አስቴር / በአጎቷ በመርደኪዮስ እጅ ያደገችም ነበረች ። መርደኪዎስ ኑሮውን በዚያው አድርጎ ነበር ። ንጉስ አርጤክስስ በአንድ ወቅት ሚስቱ ስለናቀችው እሷን ካስወገደ በኋላ ልጃገረዶች ሲመለመሉ አስቴር እድል ገጥሞአት ተመልምላ ገባች ። ንጉሱ ባያት ጊዜ ከዚያ ሁሉ ልጃገረዶች ወደዳት ። ባጭሩ ንግሥት ሆነች ሆኖም አይሁድነቷ አይታወቅም ነበር ። መርዶኪዮስ ከአደባባዩ የማይጠፋ ስለአስቴርም የሚከታተል ነበር ። በዚህ ወቅት ንጉስን ለመገልበጥ ገቢታና ታራ አሲረው ነበር ፤ ቀድሞ ጉዳዩ ለመርዶኪዮስ ደርሶ ስለነበር መርዶኪዮስ ለአስቴር ነግሮ አስቴርም ለንጉሱ ነግራ ጉዳዩ ተመርምሮ እውነት ሆኖ በመገኘቱ ሰወቹ በስቅላት ተቀጡ ይህም በንጉሱ መዝገብ ሰፈረ ።

ከዚህ በኋላ ንጉስ አርጤክስስ ሀማን ከፍ ከፍ አደረገው በሁሉም ላይ ከፍ አድርጎ አስለጠነው ። በአደባባይም ሁሉ ለሃማ የማይሰግድ አልነበረም ከመርደኪዮስ በስተቀር ። ሆኖም አብረውት በአደባባዩ የነበሩት ጓደኞቹ ለሃማ ለምን አትሰግድም ብለው ቢጠይቁት እንደማይሰግድ በማወቃቸው ስለአይሁድነቱና ስለአለመስገዱ ለሃማ ነገሩት ሃማም እጅግ ጠላው ሊሰቅለውም ወሰነ ። መላውን አይሁድ ሁሉ ሊያጠፋ ወሰነ ።

ሃማ ለንጉስ አርጤክስስ አይሁድ ለሕጉ እንደማይገዙና እንደማይታዘዙ በመንገሩ ሁሉም አይሁድ እንዲገደሉ ንጉሱ ወስኖ በሃማ እጅ ትእዛዝ /አዋጅ / አወጣ በሱሳ ግንብም ታወጀ ። መርደኪዮስ ወዲያው ለንግሥት አስቴር እንዲነገራት አደረገ እሱም በታላቅ ሃዘን በፆም በፀሎት ወደቀ ሁሉም አይሁዳዊ በሃዘን ውስጥ ወደቁ ። አስቴርም የአዋጁ ቅጂና የሆነውን ሁሉ ከአጎቷ በመልእክተኛዋ ተረዳች ። ወደ ንጉሱም ልትገባ ወሰነች ገባችም ። ንጉስ ሳይጠራ መግባት ክልከል ነበርና አደጋውን ብታውቅም ስለ ሕዝቧ የመጣውን ለመቀበል ወስና ገባች ንጉስ ሲያያት ደነገጠ አብዝቶም ወደዳት ዘንጉንም ዘረጋላት ። አስቴርም በንጉሱ እጅግ ተወዳ ነበርና ንጉስ ንግሥት ሆይ ምን ፈለግሽ የምትሽውን ሁሉ አደርጋለሁ የመንግሥቴን እኩሌታም ቢሆን አላት ። እሷም ንጉሥ ቢወድድ ወደማዘጋጀው ግብዣ ከሃማ ጋር ይምጣ አለች ። ንጉሥም ደስ አለው ሊሄድም ወሰነ ። ሀማ በአስቴር መጠራቱ አስደስቶት ነበር ። ነገር ግን ጠላቴ የሚለው መርደኪዮስ ከአደባባዩ ባለመናወፅ ተቀምጦ ሲያየው ስለማይሰግድለትም ወደ ቤቱ እንደደረሰ ለቤተሰቡ ስለመርደኪዮስ ነገራቸው ስቀለው ብለው መከሩት መስቀያውን አዘጋጀ ለማስፈቀድም ወደንጉሡ ገባ ። ንጉሥ ሌሊቱን እንቅልፍ ከልክሎት ነበርና እሱን ከግልበጣ ስላዳኑት ሰዎች ምን ተደረገ ብሎ ባለሟሎቹን ጠየቀ ። እነሱም ምንም እንዳልተደረገ ነገሩት ሃማን ጥሩልኝ ብሎ ሲናገር ንጉሥ ሆይ ሃማ በአዳራሹ ቆሟል አሉት ። እንዲገባ አዘዘ ።፤ ገባ ንጉሥ ለሃማ እንዲህ አለው ለመሆኑ ለንጉሥ መልካም ላደረገ ምን መደረግ አለበት ሲል ሃማ ከራሱ በላይ ማንም የለም ብሎ በማሰብ ለንጉሥ እንዲህ አለ። ንጉሥ ሆይ ለዚህ ሰው የንጉሥ ልብስ የንጉሥ ፈረስ

የንጉሥ ዘውድ ተደርጎለት በአደባባዩ አዋጅ እየተነገረ ንጉሥ ለወደደው ላከበረው እንዲህ ይደረግለታል አለ :: ንጉሥም በል ያልከውን ሁሉ በሱሳ ግንብ በአደባባዩ ለተቀመጠው ለመርዶኪዮስ ምንም ሳታጎድል አድርግለት ብሎ አዘዘው :: ሃማም በድንጋጤ ተውጦ የተባለውን አደረገ :: ወደቤቱም ሮጦ ሄደ ለሚስቱና ለቤተሰቡ የሆነውን ነገራቸው እነሱም በፊቱ መውደቅ የጀመርከለት ሰው ከአይሁድ ወገን ስለሆነ ትወድቅለታለህ እንጂ አታሸንፈውም ብለው ነገሩት ::

የአስቴር የግብዣው ሰዓት በመድረሱ እንዲደርስ ሃማን አስቸኮሉት :: ሃማም ደረሰ :: ንጉሡ በግብዣው ተገኘ ፤ አስከትሎም ለአስቴር ምንድነው የምትሸው የመንግስቴም እኩሌታም ቢሆን ይደረጋል ሲል ተናገራት :: ንግሥት አስቴርም ንጉሥ ሆይ በፊትህ ሞገስ አግኝቼ ከሆነ እነሆ በአይሁድ ላይ የታወጀው የሞት አዋጅ ይገልበጥ ቤተሰቤና ዘመዶቼ ሁሉ ይሞቱ ዘንድ እንዴት ይሆንልኛል አለች :: ንጉሥ አርጤክስስም እነሆ ሃማንና ቤተሰቡን ቤቱንም ባንቺና በመርደኪዮስ እጅ እንዲወድቅ አዝዣለሁ :: ስለወገኖችሽ ግን ሌላ ደብዳቤ ይዘጋጅ ይገልበጥም ብሎ ወሰነ :፤ ሃማም ደነገጠ ቤቱ ባዘጋጀው ግንድም ተሰቀለ :: አይሁድም ሞታቸው ተገልብጦ በመላው አገሮች ላይ ሁሉ በበላይነት ሰለጠኑ ::

ስለመርደኪዮስና አስቴር ጀግንነት የእምነት ፅናት በአጭሩ ባቀረብኩት ፅሁፍ ተገንዝባችኋል ብዬ አስባለሁ :: ዋናው ነጥቤ ግን እንዲህ ልግለፀው :: ወገኖቼ መርዶኪዮስ ለየት ያለ የእምነት አርበኛ ነው :: አገሩ ፈርሶበት ተዋርዶ ፤ ህዝቡንና አገሩን ባፈረሱ ጠላቶቹ ተማርኮ በአደባባያቸው የውርደት ኑሮ እየኖረ ፤ በሕይወቱ እምነቱን ወገኑን ፈጣሪውን የሚወድድ ነበር :: በመጣበት አደጋ ቢያዝንም በፆም በፀሎት አመድ ነስንሶ በመውደቅ ወደፈጣሪው አመለከተ :: አስቴርም ስለወገኖቿ ህይወቷን ለአደጋ አጋልጣ ሰጠች እግዚአብሔር ግን ሁሉንም ውርደታቸውን ሞታቸውን ገለበጠ :: ለክብር ለታላቅነት አደረገው :: ወገኖቼ እግዚአብሔርን ማስደሰት የሚቻለው በአንድ ነገር ብቻ ነው :: ከዚህ ውጪ ሌላ መንገድ የለም ፤ እሱም እምነት ነው :: መርደኪዮስ የእምነት አርበኛ ነው :: አስቴርም እንዲሁ ፤ ስንቱን እንዘርዝር እነኢያሱ ለፈጣሪው የታመነ የእምነት ተዋጊ ፤ ከሃዋሪያት እነጴጥሮስ እነዮሐንስ እነጳውሎስ እነማቴዎስ ወገኖቼ ስንቱን ላንሳ ስለማይዘልቀው ልግታው :: እነዚህ ሁሉ የልኡል ባሮች ከጨለማ ብርሃንን መርጠው ፤ ከእሳቱ ይልቅ ወደውሃው እጃቸውን ሰደው ፤ ከጨለማ ይልቅ ብርሃንን አንግሰው ለሁሉም የእውነት የፍቅር የተስፋ የፅናት ምሳሌ መለኪያ ውሃ ልክ ሆነው አልፈዋል ::ልኡል ለአመንበት የሃጢያት ደመወዝ ሞት ነው የሚለውን ከባድ ሸክም ከላያችን ላይ አንስቶ ጣለ :: ህይወትን የዘለዓለሙን ሰጠ :: የመንግስቴ ወራሽ የክብሬ አወዳሽ ከዘለዓለም እስከዘለዓለም ጌጤ ሁኑ አለ :: ፍቅሩን እስከሞት ድረስ ሄዶ ገለጠ :: ወገኖቼ ከዚህ በላይ ምን ይደረግ ? ከሞት በፊት ያ ሁሉ መቀጥቀጥ መሰቀል መወጋት መቸንከር በዚህ ሁሉ ውስጥ ስለኔና አንተ ፍቅር መጨከን ሞትን መጎንጨት መቀበር ይህ ነበር የፍቅር ዋጋ ልኡል ስላንተ የከፈለው ፤ ተሰቅሎ እየተቀጠቀጠ ልጆቼን አለእናት አልተውም ብሎ በሞት ጣር ውስጥ ሆኖ የሚወዳት እናቱን ለእኛ ለልጆቹ እናት በረከት አማላጅ መፅናኛና ለሁሉም ፍላጎታችን መልስ ትሁን አለ :: ወገኔ ለዚህ አባትህ ለዚህ አምላክህ ለድንግል ለእናትህ ምን አደረግህ ? እምን አይካድ ጠላሃቸው ካድካቸው ነቀፍካቸው ስደብካቸው በትዛዛቸው በፍቅራቸው ላይ ዘመትክባቸው ይሕን ሁሉ አድርገህ ታገሱህ ተሸከሙህ ጠበቁህ ከ2000 ዓመት በላይ መታገስ ከዚ.ህስ በላይ ምን ይደረግ ? እኔና አንተ ግን ሌላ አምላክ አቆምን ፤ዲያብሎስን አምላክህ አደረግህ እሱ የሰጠህን ድርሰት እምነቴ አልክ እውነተኞቹን ልጆቹን ገደልክ አጠፋህ አሳደድክ ዛሬ ድረስ በጥፋትህ እየጨመርክ እያዘመንክ አዳዲስ የሃጢያት ማምረቻ እየፈጠርክ ዓለሙን ሁሉ ይዘኸው ጠፋህ !!

በመልካም ፈንታ ክፉን ፤ በወደድኋቸውም ፋንታ ጠላትነትን መለሱልኝ ፤ እንዲል ፤

መዝሙረ - ዳዊት 108/109/ ፤ 5

የዛሬዋ ዓለማችን ምን ትመስላለች ፤

ዛሬ ዓለማችን በሃጢያት ባሕር ሰምጣለች ። በክህደት ተውጣለች ። የእግዚአብሔርን ሕግ ከምድር ሁሉ ሽራለች የዲያብሎስ የሆነውን ሁሉ አንግሳለች ። የእግዚአብሔር ሕዝቦች እንኳን በነፃነት ሊያመልኩ የሚረግጡትን ምድር እንኳን ተነፍገዋል ።

- በመላው ዓለም ሰዶማዊነት ከመስፋት አልፎ ሴቱም ከሴት ወንዱም ከወንድ እንዲጋባ ፡ በአሜሪካና በእንግሊዝ በፈረንሳይ ፊት አውራሪነት በየምክር ቤታቸው እንዲወሰን በማድረግ ሁሉም አገሮች በሕጋዊነት ሥራ ላይ እንዲያውሉ በማስገደድ እንዲተገብሩ አድርገዋቸዋል ። እርዳታ ብድር የሚሰጠው ይህን ለፈፀሙና ለሚያስፈጽሙ ብቻ እንዲሆን ደንግገዋል ። በዚህም መሰረት ሁሉም መንግስታቶች ለጌቶቻቸው ተንበርክከዋል ። ምንዝርና ኢንዱስትሪ ሆኖአል ።፤ በየትኛውም የዓለም ክፍል ምንዝርናን እንደስራ የማይተገብር የለም ። በአገራችንም ተስፋፍቶ የሚታይም ሆኖአል ። በአውሮፓና በአሜሪካ እግዚአብሔር የፈጠረውን ፍጡር በእያንዳንዱ ዜጋቸው ላይ የኮምፒተር ቺፕስ /ሴል/ በገላቸው ውስጥ እንዲቀበር በምክር ቤት ወስነው ለተግባሩም እየተንደረደሩ ነው ።
- ዓለማችን በጥቂት ሞኖፖሊስቶች ቁጥጥር ሥር ሆናለች ። የምድሪቱ ሃብት ንብረት ሁሉ በቁጥር 100 የማይሞሉ ሞኖፖሊስቶች የያዙት ሆኖአል ። እነዚህ ሞኖፖሊስቶች ኢሉሙናቲ ፤ ጀሲዩት ኦርደር ፤ ፊሪሜሶን ወዘተ የሚባሉ በግልጽ ሰይጣንን ለማምለክ የተቋቋሙ ዓለም አቀፍ ድርጅት ከመሰረቱና ሁሉንም ኢኮኖሚ ገንዘብ ሥልጣን በአባሎቻቸው ቁጥጥር ሥር እንዲሆን ካደረጉ ከ500 ዓመታት በላይ አስቆጥረዋል ። የዛሬዎቹ ሞኖፖሊስቶችም የነዚሁ ድርጅቶች አባላት ናቸው ። በአሁኑ ወቅት ሙሉ በሙሉ ዓለማችንን የተቆጣጠረው ይኸው አይነተ ብዙ የዲያብሎስ ድርጅት ነው ። በየትኛውም ዓለም የዲያብሎስ ድርጅቶች ከዋናው ማእከላቸው ሆነው የማይቆጣጠሩት መንግሥትና አገር የለም ።
- ዓለም እጅግ ሰልጥናለች / ሰይጥናለች/ ኢንዱስትሪው ፤ መገናኛው ፤ የጦር መሳሪያ አይነቱና ብዛቱ ፤ የማጥፋት አቅሙ ከግምት በላይ የሆነ ጥፋት የሚያመጣ መሆኑ ፤የዘመናዊ ከተሞች መብዛት የኤሌክትሮኒክስ መሳሪያው መርቀቅ ፤ ዓለማችን ላይ የሚርመሰመሰው የተሽከርካሪ ብዛትና ዓይነት ፤ በምድርም በሰማይም የሚራወጠው ባቡር አውሮፕላን የከተሞች ሕንፃና ዓይነቱ ብዛቱ እጅግ ብዙ ነው ። በህዋው ላይ የሚርመሰመሰው የሚዲያው የመገናኛው የምርምሩ የስለላው የአጥቂው ሳተላይቶች ፡ ብዛት ሰማዩን አጣበውታል ። የመገናኛው መርቀቅ የሕንፃው ብዛት ዓይነት የኢንዱስትሪው ብዛት ዓይነት ዓለም መንደር ሆናለች ። ዛሬ ያሉ ዋና ዋና በአለምም ተወዳዳሪ የሆኑ ኢንዱስትሪና ስፔሻላይዝድ የማምረቻ ተቋሞች ከ200 ሺ በላይ አልፈዋል ። ወገኖቼ በመጨረሻው ገጾች አካባቢ ከ168 በላይ ዓለምን በሁለመና አቅማቸው የተቆጣጠሩትን ኩባንያዎች አስፍሬላችኋለሁ ። ታውቋቸው ዘንድ እናም እንደትእዛዙ ፍርዳቸው ሲከናወን እንድታዩ /ለታደሉት/
- ወገኖቼ የአዳም ዘሮች ሁሉ !! በውኑ እግዚአብሔርን ምን ያህል እንደበደልነው ይታወቀን ይሆንን ? በፍፁም አልተገነዘብንም ! በዘመኔ ሁሉ ሲገርመኝም ሲያስደምመኝም የኖረ እውነት ቢኖር የእግዚአብሔር ፍቅሩና የትእግሥቱ እርቀት መለኪያው ማንኛችንም ያላወቅነው መሆኑ ነው ። ልብ በሉ ወገኖቼ 7500 ዘመናትን ሁሉ የሰውን ዘር ከነክፋ በደሉና ሀጢያቱ ያለመታከት መሸከሙ፤ ያም ብቻ አይደለም የከበደ እዳውንና ሸክሙን ሞትን እስከመሞት ድረስ ሄዶ ነፃ ማውጣቱ ፤ እድሜን ሰጥቶ አኑሮ አብልቶ አጠጥቶ ዘርን ሰጥቶ ይህ ልጄ አንድ ቀን ይመለሳል ብሎ ሁሌም በጉጉት መጠበቁ እነዚህን ሁሉ እናንተም እኔም ስንመለከተው በውኑ ሕሊና ላለው አያስገርምም ? ዓለም በለፀገ ተጠበበ ሃብቱንም እንደ ተራራ ከመረ ፤ ከምድር አልፎ በሰማዩም ሮጠበት እንደእንቦሳ ዘለለበት በዚህ ሁሉ ልእል ምንም ዓላለም በፈቃዱ የሰጠውን ምድር መጠቀማችን ቅር አላለውም ያ አይደለም ያስከፋው ምላሻችን እንጂ !!
- ወገኖቼ ለምን? በውኑ ለምን? ምን በደለንና? ምን ነፈገንና በምንስ አጎደለብንና? ምድርን ለእንግድነታችን ዘለዓለማዊ ሕይወትን በክብሩ ዙሪያ እንደከዋክብት መድመቅን ለዘለዓለም መኖርን በመስጠቱ ምላሹ እንዲህ



Scanned by CamScanner

ይሁን ? —— ክህደት ፤ ሌላ አምላክ ማምለክ ፤ ትእዛዙን ማፍረስ ጭርሱንም ስሙን ሁሉ ከምድር ለማጥፋት መትጋት ቤቱን ማፍረስ የታመኑበትን ማጥፋት ፍጹም ጨለማን ማንገስ ፈጣሪነቱን ክዶ እሱ የፈጠረውን ማምለክ በብርቱ እንዲቀና ማድረግ የዛሬው ትውልድ መገለጫ ሆኖአል ። ስለዚህ ወገኖቼ በዚህ ዛሬ ከፊታችሁ እንደብርቱ ማአበል ተጭኖ በመጣው የእሳት መጥረጊያው ልንገረም አይገባንም ። እራሳችን ምክርን ግሳፄን ቅጣትን ዘለፋን ሁሉ ንቀንና አቃለን ነው እንጂ ሌላ ማን አመጣው ? በቃ ወገኖቼ !! በቃ ! ትእግስቱም እስከጠርዝ ገፍተን እኛው ቀብርነው ። በቃ ! ተዘጋጅተህ ጠብቅ ! ሁልህም እንደ እጣ ክፍልህ ትቆማለህና እንደምርጫህ ይሰፈርልሃልና !! ወገን ስማ ደግሜ ደጋግሜ አሁንም ልንገርህ በቃ ተደመደመ !!!

- በመሰልጠኑ ልክ ረሃብተኛው ፤ የእርስ በእርስ ግጭቱ ፤ የሃይማኖት ጦርነቱ ፤ ዘረኝነቱ ፤ የድንበር ጦርነት ፤ የመቻቻል ባሕል መጥፋት ፤ ስደት ፤ በየስብሰባው ያለው አለመግባባት ፤ በተለይም የትላልቆቹ አገራት ስግብግብነት ስስት ሰብስቦ አለመጥገብ ሁሉንም የሰው ዘር በራስ ቁጥጥር ሥር ለማድረግ እስከ ኒዩክለር ጨብጦ መዛዛት ፤ የመቻቻል ጉዳይ ከምድሪቱ መጥፋት ፤ የሰው ደም በየምክንያቱ መፍሰስ ፤ በስውርም በግልፅም ሰውን እንደከብት ለዲያብሎስ ግብር ማቅረብ ፤ ሰው ሰውነቱ ተረስቶ እንደእቃና የግል ንብረት መቆጠሩ ፤ ከፈጣሪ በትክክል የምታገናኝ እምነት ተዋህዶ ኦርቶዶክስ ነበረች እሷንም ከምድረ ግፅ አጥፍተው ጨርሰዋል ። በጣም በጥቂቱ ያለችው እዚሁ አገራችን ኢትዮጵያ ሲሆን እሷም እንደተቋም እንዳትቆም የዓለማችን ሃያል የዲያብሎስ እምነቶች ውስጧ ወኪሎቻቸውን ሰግስገው ቅባት ፀጋ ተሃድሶ እያሉ ሸባ አድርገዋታል ። እግዚአብሔርም እምነቷን ከጠፉ አገልጋዮች አንስቶ በምእመኑ ልብ ላይ ተክሎአታል ። ዛሬ ብዙዎች እውነተኞቹ የልኡል ባሮች ከጠላት ጥቃት ብዛት የተሰደዱ ያጡ የነጡ የታሰሩ በተሰፋ መቁረጥ የሚበሳጩ ከፈጣሪያቸው ፍትህ ፍለጋ ጧት ማታ እንባቸውን የሚያፈሱ ሆነዋል ። ዓለም እንደመሰልጠኗ ሁሉ ሙሉ በሙሉ በዲያብሎስ አገልጋዮች ቁጥጥር ሥር ሆናለች ።

- በአገራችን በኢትዮጵያ ስልጥኖ የበላይነቱን የጨበጠው ዲያብሎስና ምንዝር አገልጋዮቹ አገሪቱን የጠፋች አድርገዋታል ። በአገሪቱ ዘረኝነት ጭካኔ ዘረፋ አምልኮ ባእድ ንቀት ጥላቻ ነግሶአል ። የተዋህዶ ኦርቶዶክስ እምነትን ሁሉም ዘሮች ማለት ይቻላል ጠልተዋታል ። ከአንድ ዘር በስተቀር ከሱም ውስጥ የተዋትና ሌላ እምነት የሚከተሉ ብዙ ናቸው ። እንዲህም ሲባል ሌሎችም ብሔር ተብለው በሚጠሩ ውስጥ እግዚአብሔርን የሚወዱ ተዋህዶንም ያመኑና የሚኖሩበት በቁጥር ይነሱ እንጂ አሉ ። እነሱም ውስጥ ተዋህዶ ኦርቶዶክስን እያመኑ እምነቱን መልሰው የዘር እምነት ሊያደርጉት የሚተጉ አሉ ። አንዳንዶች በተዋህዶ ቤ/ክ ሲሄዱ ክርስቲያን ይሆኑና ቤ/ክ/ ለቀው ሲወጡ ዘረኛነትን የሚያራምዱም ናቸው ። እውነተኞቹ የእግዚአብሔር ሰዎች የብሔር ድንበር ፤ የጥላቻ ልክፍት የለባቸውም ። የፀኑ ኢትዮጵያውያንም ናቸው ። በዚህ አይደራደሩም ።

- የዓለም ጥፋት በዚህ አጭር ጽሑፍ ተዘርዝሮ አያልቅም ። የዛሬን እውነት ሁሉም ትውልድ የሚያየው ስለሆነ መንገሩ ለቀባሪው ማርዳት ብቻ ነው ።

- ይህን ሁሉ የዓለም ጥፋት የሚመለከተው እግዚአብሔር በሰው ልጅ አለመመከር አለመገሰጽ አጅግም አበሳጭቶታል ። ክህደትና ጥፋታቸው አንሶ ፤ ሌላ አምላክ እሱም ዲያብሎስ የሰውም የእግዚአብሔር ጠላት የሆነውን አንግሰው ይህም ሳያቆማቸው የእግዚአብሔርን ሕግና ቤቱን ማፍረስ እንደስራ አድርገውታል ። እግዚአብሔር መከረ ዘከረ ቀጣ ማንም አልሰማም ። እንዲያውም ምክሩን ግሳፄውን የተለያየ ምክንያት በመሥጠት ሳይንሳዊ ትርጉም በማቅረብ እግዚአብሔር እንደሌለ በመስበክ የተጠመዱ ናቸው ። ዛሬ ሰው ሁሉ የሚያደምጠው ሚዲያው ፕሬሱ ፤ ሞባይሉ እንተርኔቱ ባጠቃላይ መገናኛው ሁሉ ዓለም አቀፍም ሆነ

የአገር ውስጥ ሁሉም በዲያብሎስ ሰራተኞች ፤አምላኪዎች ተጠዋሪዎች የተያዘ በመሆኑ አንድም የእግዚአብሔር ቃል ፤ መልእክት እንዳይተላለፍ አድርገዋል ::

ዛሬ የሰው ልጅ ጠፍቶአል የምንለው ከምንም ተነስተን አይደለም :: —— እስቲ ስለኳስ እናንሳ !! በምድራችን በተለይም አደግን በሚሉ አገሮች ኳስ ሁሉንም ሰው ተቆጣጥሮታል :: ሁሉም ዓይነት እስፖርቶች ኢንዱስትሪ ሆነዋል :: ለምሳሌ ያህል በቅርቡ በራሺያ የተካሄደውን የዓለም ዋንጫ ብናይ ልብ ብላችሁ አስተውላችሁ ከሆነ ማንኛውም ጨዋታ ሲጀመር ሲል አንድ የታየ የመግቢያ ምስል ነበር :: ምስሉ በቀይና በወርቃማ ቅርፅ ሆኖ ክንፍ ያለው ደራጎን ኳሷን በአፉ ይዞ እየበረረ ከላይ ሆኖ መጫወቻ ሜዳው ውስጥ ይጥላታል :: ከዚያ ጨዋታው የሚጀመርበት ስርአት ይከናወናል :: ጨዋታውም ይካሄዳል :: በሁሉም ጨዋታዎች ይህ ስርአት ተከናውኖአል :: እንግዲህ ወገኖቼ ኳስ ጨዋታ የማነው ማንስ ያሰረፀው ነው :: እንደገናም የአለም አትሌትክስ በፔኪንግ ሲካሄድ በተመሳሳይ ድራጎኑ ከቤቱ ሲወጣ በክንፉ በጨዋታው መከናወኛ ዙሪያ ሲሽከረከር ይታይ ነበር :: ኳስም ሆነ አትሌቲክስ ከ7ቢሊዮን በላይ የሆነው ሕዝብ በእስቴድየም በቤቱ በቴሌቪዥን አፍጦ ሲያይ ይውላል ያድራል :: ዓለም እንኳን ፈጣሪውን ሊያስብ ሊያመልክ ከነመኖሩም ረስቶታል ከሕሊናው ወጥቶአል የኳሱ ንጉስ ዲያብሎስ ነግሶበታል ዓለም ጠፋች ፈጣሪዋን ፍጹም ከሕሊናዋ አወጣች ::

- ወገኖቼ ዓለም እንዲህ ናት :: የዛሬውን መልእክት ጨምሮ ለሰባት ጊዜ በኔ በታናሽ ባሪያው በኩል ልኡል ፍርዱን ግሳፄውን ቁጣውን ነግሮ አስጠንቅቆ ቢናገርም የሰማም የለማም የለም :: ለ13 ዓመት እኔ እንኳን ፍቃድና ምክሩን ትእዛዙን ፍርዱን አድርሻለሁ ማን ሰምቶ እንግዲህ በዚህ አጭር ጽሑፍ የዓለምን ሁሉ ገፅታ ለማየት ስለማይቻል :: ለማገናዘቢያ የሚሆነውን ከላይ ለማቅረብ ሞክሬአለሁ ::

ዓለም ነገስ ምን ትመስላለች ?

እንግዲህ ስለዓለም በእምነት / በተዋህዶ / አንፃር ትላንትን ምን እንደነበረች ፡ ስለእውነተኛይቱ ተዋህዶ እምነት ተጋድሎ በውስጧም እንደኮከብ አብርተው ስላለፉት የተዋህዶ አርበኞች ስለ ስድስቱም መልእክቶች አጠር አጠር ያለ ገላጭ አንቀጽ በመጥቀስ የሞከርን ሲሆን ፤ የዛሬውን ምንነቷንም በመጠኑ ዳስናል ::

በእምነት አካሄድ የነገው መሆናችን ፤ መድረስና መገኘታችን የሚወሰነው በልኡል ነው :: የሱም ውሳኔ እምነታችንን ፤ በእውነትና በመንፈስ እሱን መታመናችን ፤ አካሄዳችንን እምነት ምግባራችንን ያያል ልብን አዕምሮን ይመረምራል ውሳኔም ይሰጣል ::

ይህ መልእክት የመጣው አለምክንያት አይደለም :: የሚሆኑ ነገሮች ሁሉ እድሜ አላቸው ሰከንድም ቅጽበትም ፤ ደቂቃም ሰዓትም ፤ ቀንም ወርም ፤ ዓመት ዓመታትም ይፍጅ እንጂ እንደጅምራቸው ማብቂያ አላቸው :: ሂደታቸውም ሲያልቅ የምናስተውላቸው የማናስተውላቸው አሉ :: ባለቤቱ ልኡል ግን እንደፈቃዱ በወሰነው መሰረት ይጀመራል ያበቃል :: እኛም ሰዎች በዚሁ መልክ የምንከወን ነን ::

በጨለማም ሮጥን ፤ በብርሃንም ገሰገስን ያ ሁሉ በልኡል ዘንድ የተመዘገበ ነው :: እንደምርጫችን ልንኖር ልኡል ከመጀመሪያው ፍቃዱን አስቀምጦአል :: በወደድነው ሄደናል :: በውጤቱ ደግሞ ወይ ተጠቅመናል አሊያም ተጎድተናል ::

ይህ መልእክት የቀደሙትን በማስታወስ የተደከመውን ሁሉ በማሰብ ሰው ምን ያህል ተጠቀመበት ፤ ወይስ አልተጠቀመበትም በሚለው መጠነኛ ዳሰሳ አድርጎአል :: አዎን ዛሬ ላይ ሆነን የትላንቱን ድካም ጥረት የምናስበው ፍርዱም ቅጣቱም ፤ መመስገኑም መባረኩም የሚያርፉበት አላቸውና ያንን ለመግለፅ ግድ ስለሆነ ነው :: ልኡል አባታችን በማይናወፅ ቃሉ ያለውን ስናስብ እንዲህ ነበር ያለው

ዓመፀኛው ወደፊት ያምጽ እርኩሱም ወደፊት ይርከስ ፤ ጻድቁም ወደፊት ጽድቅ

ያድርግ ቅዱሱም ወደፊት ይቀድስ አለ ፡፡ እነሆ በቶሎ እመጣለሁ ለእያንዳንዱም እንደሥራው መጠን እከፍል ዘንድ ዋጋዬ ከኔ ጋር አለ ፡፡ አልፋና ኦሜጋ ፊተኛውና ኋለኛው መጀመሪያውና መጨረሻው እኔ ነኝ ፡፡ የዮሀንስ ራእይ ም፤ 22 ፡ 11 – 13

እንግዲህ የብዙዎች ትርጉም / ከላይ ለተጠቀሰው የልኡል ቃል/ እንደሲጋቸው እንጂ እንደሱ ሃሳብ አለመሆኑን በድርጊታቸው ሲያረጋግጡ ኖረዋል ፡፡ የልኡል ቃል በኛ ሰውኛ የሥጋ ትርጉም የምንለው እንዲህ ነው ፡፡ ዓለም ስታልፍ ሁሉም ሲያበቃ ነው ፍርድ የሚሰጠን ስለዚህ ጊዜ አለን እስከዚያው እንደንስ እናምፅ ከሆነም በመጨረሻ የእድሜአችን ጫፍ ስንደርስ ንስሃ እነገባለን ብለው እንደይሁዳ ቀጠሮ ይሰጣሉ በአመፃቸውም ይቀጥላሉ ፡፡ ጌታ እንደሌባ እመጣለሁ አለ እንጂ የቀን ቀጠሮ አላስቀመጠም ፡፡ የእግዚአብሔር ቃል ዘመንን ሁሉ ይዳኛል እንጂ ይህ ዘመን የኔ ነው ያዘመን የናንተ ነው በሚል እጁን አጣምሮ አይመለከትም ፡፡

በሰውኛው አኗኗር ሰው ያለሕግ ያለፍርድ ቤት ያለወታደር ወጥቶ መግባት አይችልም ፡፡ አማጺኛውን ለመግታት ለፍርድ አቅርቦ ለማስተካከል ለመቅጣት ሁሉም መስራት አለባቸው ፡፡ በመንፈሳዊውም የእግዚአብሔር ቃል ሕጉ ነውና በዚያ ተመስርቶ በደቂቃውም በሰዓቱም በየዓመታቱም በየዘመኑም በፍርድ የሁሉንም ፍጥረት እንቅስቃሴ ይዳኛል ፡፡ በፊቱ የተወደደውንና ፍቃዱ የሆነውን ያጸናል ፡፡ የሚወገደውን ያስወግዳል ፡፡ አዲስ የሚመጣውም ይመጣል ፡፡ የዓለምና የሰው ልጅ እንቅስቃሴ ሁሉ በፍቃዱ ሥር ነውና የሰውን ተግባር ፤ ሃሳብና አፈፃፀሙን በሙሉ ከእይታው ውጪ አይደለም በመሆኑም ፍርዱ አብሮት እንደጥላ ይከተለዋል ፡፡ ይፈፀም ዘንድ ሲታዘዝ ይፈፀማል ፡፡

ወገኖቼ ! ዓለማችን ከዚህ መልእክት መውጣት በኋላ የሚጠብቃት ምንድነው የሚለው ነጥብ ዋናው የመልእክቱ ጭብጥ ነው ፡፡ መልእክቱም እንዲወጣ ግድ የሆነው ዓለምም አገራችንም ወደ ከፋ የጥፋት አቅጣጫ እየሄዱ በመሆናቸው ፤ ይህ ደግሞ የሆነው እየሆነ ያለውም በዓለምም በአገራችንም ከሰራዊት ጌታ ከድንግልም ለረጅም ዘመን የተላለፈውን ምክር ፤ ትምህርት ፤ ግሳፄ ፤ ዘለፋ ፤ ቅጣት ተቀብሎ ለመመለስ ይህ ትውልድ ካለመፍቀዱም በላይ የእግዚአብሔር የሆነውን ሁሉ በማጥፋት ላይ መሰማራቱ ነው ፡፡ በየዘመኑ ሁሉ የተደከመውን ድካምም ሆነ ጥረት እንደከንቱ በመቁጠር ሁሉም የአዳም ዘር ንቆ በገዛ ፈቃዱ ተጓዥ ሆኖአል ፡፡ ጥቂት ልባሞች ምክሩን ሰምተው በተሰጣቸው ምክር አትርፈዋል ፡፡ እንግዲህ እየሆነ ያለው ዓለምንና በእግዚአብሔር ፈቃድ ጸንተው የቆሙትን ፤ ዲያብሎስ ባነደደው እሳት ተለብልበው ተጨፍጭፈው ፤ መቆሚያ መቀመጫ አጥተው በታላቅ ጉዳት ውስጥ በመውደቃቸው በድካምም ዝለው በመገኘታቸው ፤ የግድ ልኡል ልጆቹን መታደግ ነፃ ማውጣት ምድሪቱንም ለልጆቹ ማውረስና እንዲፅናኑ ማድረግ ስላለበት ይህንን ተግባራዊ ለማድረግ ነው ፡፡ ለዲያብሎስ ታማኞችም በፍርድ ተካተው የሚከደኑበትን ሁሉ መደረግ ስላለበት ይህ መልእክት ይሀንኑ ለማረጋገጥና የሚፈፀሙ ቅጣቶችን ወዴት? እንዴት? በምን ደረጃ? በማን ላይ እንደሚፈፀሙ ለመግለፅ ምን ውጤት መምጣት እንዳለበት እስከመቼ እንደሚዘልቁ ለማረጋገጥ የመጣም ነው ፡፡

የዛሬው መልእክት እንደቀደሙት ስድስት መልእክቶች ጊዜ የሚሰጥ አይደለም ፡፡ ጊዜ ዘመን የሚሰጠው ለሚጠቀምበት እንጂ ከከፋ ጥፋት እጅግ ወደከረፋ ጥፋት እንዲሸጋገሩበት አይደለም ፡፡ የቀደሙት ስድስት መልእክቶች 13 ዓመታትን ሲዘልቁ ንስሐ ለሚገባው እንዲገባ እምቢ ያለውም እንደምርጫው እንዲጓዝ ልኡል ጊዜን ሰጥቶ ነበር ፡፡ አልሆነም እንደታሰበው ውጤት አልተገኘም ፡፡ በመልእክቶቹ ምንም ያልተገለጸ ነገር የ ለም ፡፡ ከአለቃ እስከምንዝር እድል አግኝቶ ነበር ፡፡ እምቢ አላውቅህም አለ ፡፡ የዲያብሎስን እምነቶች ፤ ድርሰቶች ፤ የሳይንስ ትንታኔዎች ፤ ፍልስፍናዎች ገንዘቤ ናቸው አለ ፡፡ የእግዚአብሔርን ሕግም ሆነ መልእክቶች ራሱንም የፈጠረውን አምላክ አላቃችሁም አለ ፡፡

የልኡል ቃል እንዲህ ይላል —— የሰው ልብ ከሁሉ ይልቅ ተንኮለኛ እጅግም ክፉ ነው ማንስ ያውቀዋል ፤ እኔ እግዚአብሔር ለሰው ሁሉ እንደመንገዱ እንደሥራው ፍሬ እሰጥ ዘንድ ልብን እመረምራለሁ ኩላሊትንም እፈትናለሁ :: ትንቢተ ኤርሚያስ ም 17 ፤ 9 – 10

ልኡል የምታየውን የሰማኸውን ቃል ይተገብረዋል :: ትመረመራለህ የውጤቱም ባለቤት ትሆናለህ !!

የዛሬው መልእክት የመጣው ክፉ የቁጣ መርዶ ይዞ ነው ::

እንግዲህ አላውቀውም ያልከው አምላክ አምላክነቱን ያሳይሃል :: የታመንክበትን ሁሉ ትቢያ ሲያደርግ አንተንም ወገን ዘርህንም ለእሳት እራት ሲያደርግ እሁን ታየዋለህ እያየኸውም በእሳት ባሕር ውስጥ ትጠልማለህ ::

የሰው ልጅ ልብ ብለህ አድምጥ !! የምድርን ስብ በላህ ፤ ሥጋህ ከምቾቱ የተነሳ ምድርም ጠበበው ሰማዩም አነሰው ፤ ጠገብህ ! ትእቢትህም ስመያትን ነካ :: ልኡል እንዲህ ይልሃል ! ——

ንስር ጫጩቶቹን እንደሚያወጣ ፤ በእነርሱም ላይ እንደሚሰፍፍ ፤ ክንፎቹን ዘርግቶ ወሰዳቸው ፤ በክንፎቹም አዘላቸው ፤ እግዚአብሔር ብቻውን መራው ፤ ከእርሱም ጋር ሌላ አምላክ አልነበረም ፤ በምድር ከፍታ ላይ አውጣው ፤ የእርሻውን ፍሬ በላ ፤ ከአለትም ድንጋይ በሚገኝ ዘይት አጠበው ፤ የላሙንም ቅቤ የመንጋውንም ወተት ፤ከጠቦት ሥጋ ጋር ፤ የባሳንንም አውራ በግ ፍየሉንም ከስንዴ እሸት ጋር በላህ ፤ ከወይኑም ደም ያለውን ጠጅ ጠጣህ ፤ ይሹሩን ወፈረ ረገጠ ፤ ወፈረ ደነደነ ሰባ የፈጠረውንም እግዚአብሔርን ተወ ፡ የመድሃኒቱንም አምላክ ናቀ ፤ በሌሎች አማልእክት አስቀኑት በእርኩሰታቸውም አስቆጡት እግዚአብሔር ላልሆኑ አጋንንት ለማያውቋቸውም አማልእክት በቅርብ ጊዜ ለተነሱ ለአዲሶቹ አባቶቻቸውም ላልፈሩአቸው አማልእክት ሠው ፤ የወለደህን አምላክ ተውህ ፤ ያሳደግህን እግዚአብሔርን ረሳህ ፤ ወንዶችና ሴቶች ልጆችም ስላስቆጡት እግዚአብሔር አይቶ ጣላቸው ፤ እርሱም አለ — ፊቴን እሰውርባቸዋለሁ ፍጻሚያቸው ምን እንደሆነ አያለሁ ጠማማ ትውልድ ያልታመኑም ልጆች ናቸው :: አምላክ ባልሆነው አስቀኑኝ በምናምንቴዎቻቸውም አስቆጡኝ እኔም ህዝብ ባልሆነው አስቀናቸዋለሁ በማያስተውል ህዝብ አስቆጣቸዋለሁ ፤ እሳት ከቁጣዬ ትነድዳለችና ! እስከ ሲኦል ድረስ ታቃጥላለች ምድርንም ከፍሬዋ ጋር ትበላለች የተራሮች መሰረትን ታነድዳለች ፤ መከራን እጨምርባቸዋለሁ ፤ በፍላጾቼም እወጋቸዋለሁ ፤ በራብ በንዳድ ይጠፋሉ ፤ በንዳድና በመራራ ጥፋት ያልቃሉ ፤የአራዊትን ጥርስ ፤ የምድርንም እባብ መርዝ እሰድድባቸዋለሁ :: ጎልማሳውን ከድንግል ሕፃኑንም ከሽማግሌ ጋር በሜዳ ሰይፍ በቤትም ውስጥ ድንጋጤ ያጠፉቸዋል :: እሪት ዘዳግም ም ፤ 32 ፡ 11 – 25

እሳራኤላውያን በከህደታቸው በጥጋባቸው የተሸከማቸውን አምላክ እንዴት በቁጣው እንደሞሉት ከላይ በቃሉ ያያችሁት ነው :: የእግዚአብሔር ቃል የዘመን ሁሉ ዳኛ ነው :: ዛሬ ደግሞ ከቀደሙት እስራኤላውያን የእናንተ በብዙ መቶ እጥፍ አይበልጥም ! እጅግ ይበልጣል :: በመሆኑም በብዙ እጥፍ ያነደድከውን የልኡል ቁጣ ባልታየው ዘርፈ ብዙ የእሳት መጥረጊው ትጠረጋለህ ትደመደማለህ :: እውነቱ ይህ ነው ::

ይህ መልእክት የትእግስት መደምደሚያው ማረጋገጫው ነው :: ስለ እርምጃዎቹ ዝርዝር በመልእክቱ መደምደሚያ ላይ የሚገለፁ ይሆናል ::

አገራችን ኢትዮጵያና የፍርድ ቃሎቹ ትላንት ዛሬና ነገስ !!

አገራችን ኢትዮጵያ በዚህ መልእክት ውስጥ ስንዳስሳት ምን ትመስላለች በሚለው ሃሳብ ተነስተን የቀደመውን በመጠኑ አይተን የዛሬውንም ቃኝተን የወደፊት እጣ ፈንታዋን ተመልከተን ወደ ቀጣዩ አርእስ እንዘልቃለን ፤፤

ከላይ በመግቢያዬ አካባቢ እንደገለጽኩት አዲስ መልእክት የለም ፡፡ የነበረውን ለመግለጽ የጥፋት መጠኑ በብዙ እጥፍ እንደሚጨምር ለማረጋገጥ ይህም የጥፋት ብርታት የእግዚአብሔርን ፈቃድ ፤ ትእዛዝና ለልጆቹ ለወገኖቹ ለየዋሆቹ ለቅኖቹ ለታዘዙት ለጠበቁት ምድርን እስከሚያወርስ እስከሚያስገዛ የሚቀጥል ነው ፡፡ መልእክቱም አዲስ የማይሆነው በቀደሙት ስድስት መልእክቶች ያልተዳሰሰ ጉዳይ የለም ያልተገለፀ መጪ ቁጣ የበትር ዓይነትም የለም ፡፡ ዛሬ ግን እነዚህ ሁሉ ተገልጸውም እርምጃውም ቀጥሎ ባለበት ሰዓት ወንፊቱም የብጠራ ሥራውን ከጀመረ ቢቆይም ፡፤ ውጤቱ ገና የሚፈለገውን እስካላመጣ ድረስ ታይተው ተሰምተው የማይታወቁትን የጠረጋ ዓይነቶች እየጨመሩ ይቀጥላሉ እንጂ የሚበርክ ነገር የለም ፡፡ በዚህም ሁሉ ውስጥ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ፤ ቅን የዋህ ሕዝቦች ፤ የተዋህዶ ልጆች ፤ እውነተኛ የኢትዮጵያ ፍቅር ያላቸው ወገኖች ሁሉ እንዳትደናገጡ ይህ መልእክት ሊያረጋግጥላችሁ ነው የመጣው ፡፡ በሚነደው እሳት ውስጥ ነጭ ለብሰህ በመሃሉ ብትንጎራደድ የሚነካህ የለም ፡፡ የሚታደግህ የሚጠብቅህ ሲድራቅ ፤ ሚሳቅ ፤ አብዲናጎምን የታደገ በሁሉም ዘመን ለቃሉ ታማኝ የሆነው አምላክ ነው ፡፡ እናትህ ድንግል ልጆቿን አሳልፋ አምትሰጥ አይደለችምና አትደንግጥ አትፍራ !!

ኢትዮጵያ አገሬ ! ሚስጥር ናት ፡፡ የሥላሴ ሚስጥር ፤ የአገሮች ሁሉ መለኪያ ውሃ ልክ ናት ፡፡ ዛሬ እሷን ለማጥፋት በተራቀቀ የጥፋት በትር የመበተን ዘዴ  እናጠፋለን ብለው  እጅግ  በሚገርምና በሚያስደነግጥ ሁኔታ እያመሷት ይገኛሉ ፡፡ ግን አይሆንም ፡፡ እነሱ ይበተናሉ እነሱ እንደ ጭስ ይበናሉ እንጂ ምንም ሊያደርጓት አይችሉም ፡፡ በአሁኑ ሰዓት ከመሪዎችም አንደበት ከድርጅቶችም የየዘወትር ንግግር ከአብዛኛውም ሕዝብ የሚወራው የሚነገረው ኢትዮጵያ ልትፈረስ ነው ልትበተን ነው የሚል ነው ፡፡ ——— ማነው የሚበትናት ማነውስ ለጥፋቷ እየተጋ ያለው ሁሉም ይታወቃሉ ፡፡ በሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር ስም ላረጋግጥላችሁ እወዳለሁ ፤ ኢትዮጵያ የድንግል እርስት የስስት ምድር ናት ሁልህም የምትመዘነው የምትለካው ስታንስ የምትጣለው በሷ ውሃ ልክነት ነው ፡፡ ዲያብሎስ ያደነቆረህ ፎቅ ላይ ስቅሎ ሱፍ አልብሶ የሱ ታላቅ ተብዬ አገር ሥልጣን ላይ አውጥቶ በትረ- ዲያብሎስ አስጨብጦ መሪ መሪ እያለ ቢያንቆለጳጵሥህ ምድርና ሰማይን የጨበጥህ መሰለህ ! አይ ሰው ! ዛሬም እወቅ ! አሁንም ቢገባህ ይግባህ —— ኢትዮጵያ የዓለም ብርሃን ናት ፡፡ኢትዮጵያ የዓለም ገዢ ናት ፡፡ ኢትዮጵያ የተወደደች በልኡልም በድንግልም በስስት የምትታይ እንቁ ምድር ናት ፡፡ በሷ መጥተሃል ልታጠፋ ደክመሃል ፤ ይህ ድርጊትህ በልኡልና በድንግል ዓይን መምጣት መሆኑን አሁንም አልገባህም ደንቁረሃል ፡ እምን ! መስሚያህም ማስቢያህም በዲያብሎስ መልከ ብዙ ፕሮፓጋንዳ ዘመንክ በምትባልበት ዘመናዊ ቅራቅንብ ተደፍኖአል ፡፡ አንተን ለመለወጥ ስላልተቻለ ከታመንክበት መልከ ብዙ ጌታህ ጋር ላንዴም ለሁሌም ትቀበራለህ ፡፡ ይህ ሊያጠራጥርህ አይገባም ፡፡

ወገኖቼ የአዳም ዘሮች !! አገሬ ኢትዮጵያ ሚስጥር ናት ፡፡ የልኡል ሚስጥር ፤ የድንግል ሚስጥር ፤ ማንም የማይሰብረው ማንም ሊያየው ያልቻለ ፡፡ አገሬ ሚስጥር ናት ፡፡ሊያጠፏት ያልቻሉ የዛሬው ሃያል ሃገራት ስልታቸውን እየቀያየሩ ቢለፉም ቢሸራርፏትም አልጠፋችም አትጠፋምም ፡ ይልቅስ እጃቸውን ባረዘሙ ስልታቸውን በቀያየሩ ቁጥር የተሳካላቸው ቢመስላቸውም በሚቆፍሩት ሁሉን ዓይነት ጉድጓድ እንደራሳቸው ዓይነትና ብዛት ራሳቸው ይቀበሩበታል እንጂ ሌላ የሚፈጠር ነገር የለም ፡፡

ይህ መልእክት በዝግጅት ላይ እያለ — የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤ/ክርስቲያን የውጪውና የውስጡ በሚል በወያኔ የከፋት ሴራ የተከፈለ ሲኖዶስ እንደገና በአዲሱ መሪ አደራዳሪነትና ግፊት እንዲዋሃዱ መደረጉን ሁሉም የሚያስታውሰው ጉዳይ ነበር ፡፡ እኔ ስለውህደቱ አስተያዬት ለመሥጠት አልሻም ፡፡ ከዚህ ይልቅ ሁለቱ ፓትሪያርኮች በተገኙበት መንበረ ፀባኦት ቅድስት ሥላሴ ቤተ ክርስቲያን ላይ በተደረገው የአቀባበል ዝግጅት ላይ ከውጪ የመጡትን አባት በመወከል ንግግር ያደረጉ አንድ አባት / የአውሮፓ ተዋህዶ ቤ/ከ አባት ስማቸው

እርግጠኛ ባልሆንም አቡነ ኤልሳ የሚባሉት / የተናገሩት እጅግ የሳበኝና የገረመኝ ሁለት ነጥብ ተናግረዋል ። አንደኛው — ኢትዮጵያ የሥላሴ የሚስጥር አገር ናት ። ማንም ይህን ሚስጥር በቀላሉ አይደርስበትም ያሉት አንዱ ሲሆን ሁለተኛው ደግሞ አውሮፓውያን የኛን ተዋህዶ ቤ/ክ እጅግ እንደሚጠሉና ሊያጠፏት ያልተቋረጠ ትግል እንዳደረጉ አሁንም እያደረጉ እንዳለ የሰጡት ምስክርነት ሲሆን እኚህ አባትን በግሌ አከብራቸዋለሁ ። ረጅም እድሜ ከጤና ጋር ይስጣቸው እላለሁ ። ተኩላና ቀበሮ በነገሰበት ሰዓት ጥቂት በቁጥር ያነሱ አባቶች እንዳሉ እያሰብኩ ሁሉንም እግዚአብሔር ይጠብቃቸው ለትንሳኤው ዘመን ያብቃቸው እላለሁ ።

ወገኖቼ !! ዛሬ በመላው ዓለም የሰፈኑትን እምነቶች እነካቶሊክ ፤ እነእስላም ፤ እነፕሮቴስታንት ፤ እነሂንዱኢዝም ፤ ሺንቶኢዝም ሌሎችም ለቁጥር የሚያታክቱ እምነት ተብየዎችን ስናስባቸው የሚያስገርመው ባሕርያቸው ሁሉም ስለመጪው መጥፎም በጎም ዘመን የሚገልጹት እውነት የሌላቸው መሆኑ ነው ። ተዋህዶ እምነታችን እውነት ላይ የተመሰረተች እጅግ ውድ ዋጋ የተከፈለባት ዛሬም እየከፈለች ያለች እምነት ናት ፤ እውነተኛ ልጆቿ ከአምላካቸው ጋር የሰመረ ግንኙነት ያላቸው በመሆናቸው ልኡል ስለፍርዱም ስለወቀሳውም ሊያደርግ ስላሰበውም ቀድሞ ለታመኑት ባሮቹ ይናገራል ። ወደ ሕዝቡም ሁሉ ይልካቸዋል ። ይህም ዛሬ እየሆነ ያለ ነው ። እነአብርሃም ፤ እነኖሕ ፤ እነኤልያስ እነኤልሳ እነዳንኤል እነወንጌላዊው ዮሐንስ እጅግ ብዙዎች በዚህ ሕይወት አልፈዋል ለኛም ምስክር ሆነዋል ። በእውነተኞቹ የእግዚአብሔር ልጆች ዘንድ ዛሬም ሚስጥር የለም ። ልኡል አይደብቃቸውምና !! ስለእውነተኛይቱ እምነታችን ይህን ካልን — ምድርን ስለሸፈኑት ካቶሊክ እስላም መናፍቅ የምስራቆቹ እምነት ሺንቶኢዝሙ ቡዲህዝሙ ሂንዱኢዝሙ እነህ ሁሉ ዘጠና አምስት ከመቶውን ሕዝብ የሸፈኑትን በአገራችን ያሉትም ማሕበርተኞቻቸው እስላሙም መናፍቁም ካቶሊኩም ዋቄ ፈታውም ተብታቢውም መተተኛውም እስቲ ይንገሩን መቼም አዋቂ ነን ባዮች ናቸው ። ትውልዱን ሁሉ በውሸት ፤ በተረት በፍልስፍና በተደረተ የሚያማልል ቋንቋቸውና ንግግራቸው የሰውን ሥጋዊ ፍላጎት በመኮርኮር በተካኑበት ችሎታቸው ። ከፖለቲካውም ከንግዱም ከፍልስፍናውም ከዝርፊያውም ከዘረኝነቱም ከዲያብሎስ አምላኪነቱም ከሁሉም ውስጥ የጠለሙ በመሆናቸው እናውቅም የሚሉት ነገር በፍፁም የለም ። ዛሬ ብቻ ሳይሆን ለ13 ዓመት ለ6 ጊዜ ያሁሉ የልኡል ፍርድ ፤ ሲገለጥ በተግባርም እንደ መልእክቱ ምድር ስትበጠር ዛሬም እጅግ ለከፋው ቁጣ ስትጣድ ለምን ሕዝባቸውን አይታደጉትም ፤ ለምን መፍትሔ ከሚታመኑበት እምላክ እያመጡም ። እኛ እንደምንረዳው ከጧት እስከማታ መስዋእት ዘርግተው በአል ሆይ ስማን እያሉ የጮሁትን የቡኤል ዘቡኤል ካህናትን የተከሉ ናቸው ። ለውጡ በዘመነ እስራኤል በነአካብ በነኤልዛቤል ዘመን መከናወኑ ሲሆን የዛሬውም ከ7 ቢሊዮን በላይ ቁጥር መሸፈኑ በሚሊዮኖች የሚቆጠሩ የዘመናችን የበአል ካህናት ከነኤልዛቤል የበአል ካህናት የወረሱትን እምነታቸውን የዘመናዊነት ካባ ማልበሳቸውና በዛው መንገድ መሄዳቸው ነው እውነቱ ። ወገኖቼ የበአል ካህናት ከጧት እስከ ማታ ቢጮሁ ሰሚ አጥተው በቂስ ሸለቆ ለማለቅ በቅተዋል ። ራሳቸውን እላዳኑ የደገፈቻቸውን ኤልዛቤልንም መንግስቷንም አልታደጉ ሁሉም አልቀዋል ። እውነትን ጨብጦ የተዋጋቸው ሁሉም እንደሚያውቀው እድሜውን በእንክርት በስደት በፈተና የጨረሰው ኤልያስ ነበር ። ዛሬም ኤልያሶች ፤ ኢያሱዎች ፤ ዳዊቶች ፤ የተጉ ቅዱሳን ማንንም ባያውቃቸውም በየትቢያው ላይ ወድቀው በእውነቱ መንገድ ላይ አሉ ። ዛሬ ይህ መልእክት እያስገመገመ መጣብህ በጠበቅኸው የበአል ትምህርትና ትምክህት ጨህ !! ሺዎችን ዘመናት ከንቱ በሆነ ጩኸት አሳልፈሃል ። ዛሬም ያው መስሎህ ከሆነ አትሳሳት ዛሬውኑ እጣ ፈንታህን ትቀበላለህ ። በእንቅልፍ ላይ ይሁን ፤ ወይ መንገድ ሄዶ ፤ ወይም በሌላ ጉዳይ ተጠምዶ በርታና ጩህ በአል ታደገኝ በለው ። ሉሲፈር ፤ የቀደመው እባብ ያላደራጀልህ የድርጅት እምነትና ማምለኪያ የለም ። በዚህ ዘመን እቋቋማዋለሁ የማይለው ነገር የለም ። ስለዚህ የታመንክበት ያድንህ !!

ኢትዮጵያ የተዋህዶ አርበኞች ምድር ፤ ኢትዮጵያ የተዋህዶ እምነት የሚስጥር ምድር ፤ የዛሬ ጉዳቷ ሁሉ የቀደመውን ግዛቷን ብቻ አይደለም የሚመልሰው ከዚያም በላይ ዓለም ሁሉ በምርኮ ተሰጥቶአታል ። እንዴት ይሆናል ? አድሉ የለህም እንጂ በጥፋትህ ሂደት ውስጥ ሆነህ ጫፍ ጫፉን ታየዋለህ ። ተዋህዶ ማለት ብርቱ

የእግዚአብሔር ፈቃዱና ትእዛዙ ቃሉም ዘብ ናት ። ከላይ እነደነገርኩህ በአል ይታደግህ !! እኛ ደግሞ በምንወደው በቅጽበትም በሚሰማን በእሳት አጥር በሚጠብቀን ከፊታችንም ቀድሞ እንደትንታግ እሳት ጠላትን ሁሉ በሚጠርግልን አምሳያ በሌለው የሰራዊት ሁሉ ጌታ በአብ በወልድ በመንፈስ ቅዱስ አሃዱ አምላክ ስም እንመካለን እንታመናለን ። እሱ በሰጠን እጅግ በሚወዳት በእናቱ ለኛም መተኪያ የሌላት እናት በሆነችው ቅድስተ ቅዱሳን ድንግል ማሪያም እንመካለን እንታመናለን ። —— የልኡል ቃል እንዲህ ይላል ——፤

— ክፉ አድራጊዎች ይጠፋሉና ፤ እግዚአብሔርን ተስፋ የሚያደርጉ ግን እነርሱ ምድርን ይወርሳሉ ፤ ገና ጥቂት ኋጢያተኛም አይኖርም ፤ ትፈልገዋለህ ቦታውንም አታገኝም ፤ ገሮች ግን ምድርን ይወርሳሉ ። በብዙም ሰላም ደስ ይላቸዋል ። ኋጢያተኛ ፃድቁን ይመለካከተዋል ጥርሱንም በእርሱ ላይ ያንገጫግጫል ፤ እግዚአብሔር ይስቅበታል ። ቀኑ እንደሚደርስ አይቶአልና !

መዝሙረ— ዳዊት 36(37) ፤ 9 —— 13

የትላንቷ ኢትዮጵያ

ኢትዮጵያ ሀገራችን የዛሬው ገፅታዋን ከመያዟ በፊት የነበራት ማናቸውም ነገሯ ሁሉ ለዛሬው ትውልድ ቢነገረው ተረት እንጂ ፍጹም እውነት አይመስለውም ። የዛሬዋ ኢትዮጵያ ከቀደመው ግዛትዋ ያላት ኢምንት ነው ።

አገራችን ኢትዮጵያ በምድራችን ከነበሩት ቀዳሚ መንግስታት እኩል የምትጠራ የምትታወቅም ነበረች ። በነአቴና ፤ በነሮማገን በነባቢሎን በግብፃውያን ዘመን በነአዝቴክስ ዘመን ኢትዮጵያ በታላቅነቷ የምትታወቅ ነበረች ። በነካሌብ ዘመን ደግሞ ከአፍሪካም አልፋ የመንን ጨምራ በሃይሏ በኢኮኖሚዋ በንግድ መረቧ እጅግ የገነነች ነበረች ። ይህ ደግሞ በታሪክ ጎልቶ ስለተከሰተ ሊሸፍኑት ያልተቻለ እውነት ነው ። የዛሬዋ ኢምንት የትናንቷ ገናናዋ ኢትዮጵያ በእግዚአብሔርም ፊት የምትወደድ ነበረች ። ምድሯም ለምና እጅግ ያማረ ነበር ። ክርስትና ወደኢትዮጵያ ዘልቆ ከገባ በኋላ ኢትዮጵያ በተዋህዶ ኦርቶዶክስ እምነቷ የፀናች በመሆኗ ይበልጥ በልኡል በመወደዷ ጌታም ፤ ድንግልም ፤ የእምነት አርበኞቹ ሃዋሪያትም በፍቅር የተመላለሱባትም ነበረች ። በሙሴ ዘመን ደግሞ በታላቅ ሕዝብነቷ በልኡል የተመሰከረላት ነበረች ።

ወገኖቼ ኢትዮጵያውን ከ2000 ዓመት ወደዚህ ያለውን ከማነሳና የዚህን መልእክት ገጽ ከማጣብብ ቀደምት የሆነውን ባነሳ ይሻላል ። ምክንያቱም በአብዛኛው የተመዘገበና የተፃፈ በመሆኑ ፤ በቀላሉም የተፃፉ መፃሕፍቶችን ማግኘት ይቻላል ብዬ ስላመንኩበትም ነው ።

ኢትዮጵያ አገራችን ዛሬ በምናያት ቅርፅና ይዘት በቀደምቱ ዘመን አልነበረችም ። አህጉረ አፍሪካ ፤ የአሁኑ መካከለኛው ምስራቅ እስከ ሕንድ ያለው ግዛት የኢትዮጵያ መደበኛ የግዛት አካል ነበር ። በ16 ኛው መቶ ክፍለ ዘመን የተሰራ አንድ ካርታ በአሁኑ ጊዜ በፓሪስ ይገኛል በዚህ ካርታ የተመለከተው አፍሪካ በሙሉ እንዲሁም መካከለኛው ምስራቅ የኢትዮጵያ ግዛት መሆናቸውን ያረጋግጣል ። የዛሬው አትላንቲክ ውቅያኖስ የኢትዮጵያ ውቅያኖስ ተብሎ ይጠራ እንደነበር ያረጋግጣል ።

ወገኖቼ! ይህ ስለ ግዛትና ስለሥልጣኔ ስለንግድና ገናናነት ብዙም ባያስደንቅም ፤ ሌሎችም በየዘመኑ የተነሱ ታላላቅ መንግስታት የሄዱበት ሆነውም ታሪክ ሆነው የተደመደሙበት በመሆኑ ብዙን ላይገርመን ይችላል ። የኔ ነጥብ ይህ አይደለም ፤ ስለ ኢትዮጵያ ሀገራችን ሲነሳ የሚደንቀኝ የሚገርመኝ ድብቁ ፤ ነጩም ሌላውም የሚደብቀው እንዳይነሳ የማይፈልገው ታሪኳ ነው ።

ወገኖቼ !



በአሁኑ ወቅት አገራችን ኢትዮጵያ እጅግ ብርቱ ፈተና ላይ ብትወድቅም :: እግዚአብሔር በክብር እንዲሚያነሳት ጠላቷም ወዳጇም ልረዱት ይገባል :: ርስተ ድንግል ኢትዮጵያን ፤ ተዋህዶ እምነትን ፤ መለያዋ አረንጓዴ ቢጫና ቀይ ምንም ያልተለጠፈበት ሰንደቋን ፤ አንድ ሕዝብ አንድ ተዋህዶ ሃይማኖትን አንድ ሃገር መሆኗን — ያልተቀበለ ፤ ያላመነ ፤ ይህንንም እውነት ለማጥፋት የደከመ ፤ ዛሬም ከዚህ እውርነቱ ያልተላቀቀ ፤ በሥልጣን ላይ ተቀምጦ ዛሬም ለዲያብሎስ የዘር ፤ ክልል ፤ የድንበር መለያ እየፈጠረ ሕዝብን ከሕዝብ እያጋጨ የመኖር ሕልም የሚያልም ሁሉ የሞት መርዶውን ዛሬ ይስማ !! በዚች ምድር እንኳን ሊኖርባት ዘሩም ያለምልክት የሚቀበርባት አገር መሆኗን ዛሬ ላረጋግጥልህ እወዳለሁ ::

ዘረኝነትን ያዘልክ ፤ በተለይ ለዚች አገር እጅግ መነሰቆል ከ27 ዓመት በላይ እንደሕዝብ እንደድርጅት ተባድነህ ፤ የዘረፍክ የገደልክ ፤ ያፋጀህ ዛሬም በዚያው መንገድ እየሄድክ ያለህ ለአገሩ ኢትዮጵያ አንድነት የተሰማራውን ኢትዮጵያዊ ወታደር ነፃ ልወጣ ነው በሚል እቅድህ ስትፈጀው የነበርክ ሁሉ ልብ በል እግዚአብሔር የፅድቅ ፤ የእውነት ፈራጅ እንጂ ሸንግለህ የምታልፈው አምላክ አይደለም ስለዚህ ለሚመጣብህ ቁጣና የእሳት ጠረጋ ተዘጋጅተህ ጠብቅ :: አዎን ጠብቅ ! የማታልፈው ፈርጀ ብዙ ሰይፍና እሳት መጥቶብሃል !!

ኢትዮጵያ የድንግል እርስት ! ኢትዮጵያ የተዋህዶ እርቶዶክስ እምነታችን መሰረት ብርቱ ዘብ ተፍጭታ ተቆልታ ተሸርፋ ተሸራርፋ አልጠፋ ብላ ሺዎችን ዘመን ለልኡል እውነት በእቶን ስትቃጠለች ኖራለች :: ዲያብሎስ የየእለቱ የዘመቻው ኢላማ አድርጎአት የኖረችው ኢትዮጵያ በሕገ ልቡና ጊዜ ምን ያህል በእምነት ብርቱ እንደነበረች ወደ ኋላ መለስ ብለን ብናይ ለግዛቤ ይረዳናል ::

ከጠላቶቻችን የነጮች ዓለም የምንሰማውና ያደመጥነው ታሪክ በአብዛኛው አገራችንን የሚያሳንስ ፤ በብዙ መንገድም ምንም የእምነት ታሪክ ፤ የታላላቅ መንግሥታት ታሪክ ወይም ገድል እንደሌለን አድርገው ሲነግሩን ኖረዋል :: ዛሬም የሚነግሩን የተቀመመ ፤ የተደለዘ ፡ የተሸረፈ ፤ የተለወጠ ድርሰታቸውን እንደታሪክ መሰረትና እውነት አድርገው ነው ::

የነጩ ዓለም ሰዎች እጅግ ደፋሮችና ፍጹም የዲያብሎስ ውላጆች ናቸው :: ለዚህም የሚደግፈን እውነት ቢኖር ክቡር የሆነውን መጽሐፍ - ቅዱስን ቀንሰው ከልሰው ዛሬ ላይ ፍጹም ከመሰረቱ የወጣ የተቀነሰ የተዛባ ቅርጽና ይዘት እንዲኖረው አድርገዋል :: የጥቁሩን ታሪክ ስሪነት ለማጥፋትና ለማደብዘዝ ፤ የነጩን ዓለም ለማወደስና ለማንገስ ያልሄዱበት መንገድ የለም :: ደፋሮች ናቸው :: ፈጣሪን የናቁ ናቸው :: የዲያብሎስ ተገዢ ናቸው ::

ስለኛው ታሪክ መለስ ብለን ስንመለከት ፤ እነሱ ጠፍቶአል ብለው የረሱት በኢጋጣሚ ልኡል በፈቀደው መሰረት ከፍርስራሽ የወጡ ታሪኮች በአንዳንድ የተገ የተዋህዶ ልጆች ከሳባ ቋንቋ ወደ ግእዝና ወደ አማርኛ ተተርጉመው ለንባብ በቅተዋል :: ዛሬ የማነሳው የአቶ መራሪስ አማን በላይ ጽሑፍን ሲሆን — የጥንቷ ኢትዮጵያ ትንሳኤ – መጽሐፈ ሱባዬ – በተባሉት የታሪክና እውነተኛ ክስተት የተገለጠበት መጽሐፋቸው ውስጥ ከሳቡኝና ከአስደነቁኝ ታሪኮች የሚከተሉት ናቸው ::

በቀደሙት ዘመናት ልኡል ለአባቶቻችን ራሱን በመጠኑ ፤ እጅጉን በጥቂቱ ነበር የገለጸላቸው :: በዛችው ጥቂቷ የብርሃን ብልጭታ አባቶቻችን እጅግ በመደነቅ በምላት ይፈልጉትና ሊያገኙት ይደክሙ ነበር ::

ልኡል በገለጠላቸው በትንሷ መገለጥ አብዝተው የፈለጉት አባቶቻችን በታሪካችን አስደናቂውን ዘመን ሸፍነው ለኛም የሚገርም ታሪክን ትተው አልፈዋል ::

ከጌታ ልደት በፊት ከ 4500 ዓ.ዓለም ቀደም ብለው ከነገሱት ኢትዮጵያውያን አፄዎች / ንጉሠ ነገሥቶች/ መሃል አፄ ሰንደቅ አልማን ብናይ —— አፄ ሰንደቅ ዓልማ በዘመኑ መላውን አፍሪካ ሩቅ ምስራቅን፤ ኤሽያን ፤

በከፊል አውሮፓን በመዝለቅ 150 አገሮችን ፀጥ አረጭ አድርጎ አስገብሮ ከተማውን ሳባ ብሎ በጊዮን ወንዝ መነሻ ላይ መስርቶ ይገዛ ነበር ፡፡ በሚሊዮን የሚቆጠር የተለያየ ሰራዊት የነበረው ንጉሥ ነበር ፡፡ እኒህን ሁሉ እንዲገዛ ከ450 ዓመት ያላነሰ እድሜ እንዲኖር የፈቀደለት ልኡል አምላካችን ነበር ፡፤

ዛሬ ተረት ቢመስልም ሆኖ ያለፈ የተከናወነ ታሪካችን ነው ፡፡

ንጉሠ ነገሥት ሰንደቅ አልማን አምላካችን አጋዕዛተ ዓለሙ ሥላሴ ምን ያህል ቢወዱት ነው እንዲህ የባረኩት ፡፡ እንዲህም ያጸኑት ፡፡ በዘመኑ ቋንቋው ሳባዊ ነበር ፡፡ በእግዚአብሔር የተወደደው አፄ ሰንደቅ አልማ የሚፀልየው ጸሎትን ብንመለከተው ፤ ልብ በሉ ! በዚያን ዘመን የአለምን ሁለት ሶስተኛ የሚገዛ ንጉሠ ነገሥት በልኡል ፊት ምን ይል እንደነበር ዛሬ ላሉ ትውልዶች አምልኮት ውሃ ልክ / መለኪያ / ስለሚሆን ነው ላነሳው የወደድኩት ፡፡

አፄ ሰንደቅ አልማ በአምልኮቱ ምን ያህል እውነትን እንዳነገሰ እናያለን ፡፡ የምስጋና ጸሎቱ እንዲህ ይላል —
—

- አልፋኤል - ኢኤል ,, የመጀመሪያው እውነተኛው መንፈስ ፤ በአምላክነትህ ታምኜ ማገኛውንም የሰብአዊውን ሥራ ስጀምር ፈጣኑ ሃይልህ ረዳቴ ነውና ለዘለዓለም ከኔ ጋር ይኖራል ፡፡
- የንኤል — ኢኤል ,,, ሥርዓትን በሥርዓት ጊዜን በግዜ የምትቀይርና አዲስን ድንቅ የሆነን የምትሰጥ እውነተኛው መንፈስ ፤ በአንተ ታድሼና አምሬ በዓለም ፊት እታያለሁ ፡፡ ፀጋንና ክብርን በሃይልህ እቀበላለሁ ፤ እውነትህንም እታጠቃለሁ ፡፡
- አማኑኤል — ኤል ,,, እውነተኛው መሪ መንፈስ በአንተ ስላለሁና ስለቆምኩ በሰላምና በክብር ለሕዝብህ ፀጋና ረድኤት እሆናለሁ ፤ በሃይልህም ከፍ ከፍ እላለሁ ፤ በሥልጣንህም የሕዝብን ተቃራኒ ሁሉ ድል አደርጋለሁ ፡፡ አንተ በኔ አድረህ ፈቃድህን ፈፅመሃልና አመሰግንሃለሁ ፡፡
- ኤል — ኢኤል ,,, አድራሽና ፈፃሚ የሆንክ ታላቁ መንፈስ ፤ በአንተ ስላመለኩና ስለፀለይኩ ፍቅሬንና መስተዋድዶን ነፍስ በተሰጠው ሥጋ ለባሽ ልብ ሁሉ ላይ ፃፍላቸው ፡፡ በሕሊናቸው እመላለሳለሁና ነፍሴ በአንተ ከበረ ፡፡
- ኢያስጴድ - ኤል - ኢኤል ,,, ለዘለዓለም ነዋሪና መስረት የሆንከው ረዳቴ ፈጣኑ መንፈስ በአንተ ስለከበርኩና ስለታወቅሁ መንፈሴን በመንፈስህ ምራው በሃይልህም አጠንክረው ነፍሴ ስላንተ ሥራ ደስ ተሰኘ ፡፡
- ኡዱኤል - ኡል ,,, በሰማያትና በምድር በአየርና በባሕር በውስጥና በውጪ የምትገኝ ቅርብ የሆንክ እውነተኛ መንፈስ በአንተ ስለሚኖር ሥጋዬ የፈለገውን የተመኘውን መባውን ሰብስብለት አስገብርለት ነፍሴንም በፀጋህ ደስ አሰኘው ለዘለዓለሙ ከአንተ ጋር በክብር ይኖራልና !

ኤልአቴ - ኡዩኤል ,,,, የሚታይና የማይታየውን ረቂቅ ተንቀሳቃሽ ሁሉ የፈጠርክና ያስገኘህ ለዘለዓለም
- የምትመሰገን የአምላኬ መንፈስ ፤ ወፍ ጎጆዋን ሰው ማደሪያውን እንደሚሰራ እኔንም አንተ ሰርተኸኛልና በሃይልህ አድሰኝ በሥልጣንህም አንፀባርቀኝ ፤ የአንተ ማደሪያህና ማረፊያህ ነኝና አታሳፍረኝ ፤ እውነተኛው መንፈስ ያለበት ሁሉ ለዘለዓለም ፀንቶ ይኖራል ፡፡ ሕያው ሆኖ በአንተ ፊት ይከብራል ፡፡

አውኤል - ኤኋኤል ,,, ክቡርና ምስጉን የሆንከው የታላላቆች ታላቅ እውነተኛው መንፈስ ፍቅርና ሰላምን
- ኢዮሜንና ጤናን አድለኝ እነዚህ ለሥጋዬ ፀጋ ለነፍሴ ክብር ይሰጠዋልና ! ስለዚህ መንፈሴ በአንተ እየተመራ በእውነት ጎዳና ይጓዛል ፡፡

- ኡዋውኤል – ኢዋኤል .... ግሩም መንፈስ በአስደናቂ ሃይልህ ፤ በረቀቀ ሥልጣንህ ለሕይወቴ መኪታ ለነፍሴ አለኝታ ሁነኝ ፡፡ ከሚታወመኝ አድነህ ተቃዋሚዬን ከምድር ፊት አጥፋልኝ በሪጣን ሃይልህ ደምስስልኝ መንፈሴ በአንተ ተጠብቆ ለዘለዓለም ይኖራል ስለአንተ በአንተ ነፍሴ ደስ ተሰኘች ፡፡
- አማኃኤል – አኤል .... መፈፀሚያና መጨረሻ የሆንከን ቅዱስ መንፈስ ለዘለዓለም የምትኖር ተወዳዳሪ የሌለህ ምስጉን ክቡር ነህና ፈቃድህ በአንተ እንደሆነ በኔ በማደሪያህ ይሁን ፡፤ የመንፈሴም የሥጋዬም የነፍሴም ደስታ ስጠኝ ፤ በአንተ እኖራለሁ ፡፤ ለዘለዓለም በአንተ ድል አደርጋለሁ ፡፡ በሥልጣንህም ከፍ ከፍ አላለሁ ፤ አንተ የመንፈሴ መሪ የሥጋዬ ክብር የነፍሴ ሕይወት ነህና ለዘለዓለም አመሰግንሃለሁ ፡፡

የመጀመሪያዎቹ ቃሎች ሳባውኛን ቃል የሚገልፁ ናቸው ፡፡

ወገኖቼ ! አፄ ሰንደቅ አልማ የዓለምን ሁለት ሶስተኛ የገዛ ንጉሠ ነገሥት ፈጣሪውን እንዴት እንደሚያመሰግን እንደሚፀልይና እንደሚያከብር አየን ፡፡ ያውም በሕገ ልቡና ዘመን ! በይበልጥም ልኡል በጥቂቱ ራሱን በገለጠበት ዘመን ! በታላቅ ክብርና ግርማ ላይ ያለ ንጉሥ ይህን ሲል — ዛሬ ላይ ሆነን የዘመናችንን ገገርዎችና ሕዝቦች አምልኮታቸውን ስናጤነው ምን ያህል የወደቅን ምንስ ያህል ከፈጣሪ የተጋጨን እንደሆንን አብዝቶ ይመሰክርብናል ፡፡

እስኪ በተጨማሪ ከአፄ ሰንደቅ አልማ በኋላ የነበረውን እንዲሁ እንደአባቱ የከበረውን የገነነ ንጉሠ ነገሥት አፄ አፊላስን እንመልከት ——

ከ 4589 ዓመተ ዓለም በፊት የዓለም አባት እስከመባል የደረሰው የአፄ አፈላስ ተግባር ምንድነው ነው ፡፡ ከአባቱ ከአፄ ሰንደቅ አልማ በኋላ የነገሰው አፄ አፊላስ በመረዌ በአክሱም ከተማውን አድርጎ ብዙ ነገሥታትን ኦስገብሮ ይኖር ነበር ፡፡ እንዲሁ እንደሱ ብርቱ ባይሆንም በመካከለኛው ምስራቅ በታላቅነቱ የሚታወቀው የባቢሎን ንጉሥ ናቡከደነፆር እንዲሁ በሥሩ ብዙ መንግስታትንና ሕዝቦችን ይገዛ ነበር ፡፡

በአንድ ወቅት አጼ አፊላስ ስርዓተ ንግስናውን በጊዮን ሳባ ከተማ ሲያከብር ለሁሉም መንግስታትና ሕዝቦች በበአሉ እንዲገኙ የክብር ጥሪ አድርጎ ነበር ፡፡ በዚህ ጥሪው መሰረት የተገኙም ያልተገኙም ነበሩ ፡፡ ከተገኙት ውስጥ በናቡከደነፆር ሥር የነበሩ ከአይሁድና ሶሪያ ጎረቤት የነበሩ ሕዝቦች ነበሩ ፡፤ አፄ አፊላስ ላዘጋጀው በአል ጥሪውን አክብረው ተገኝተውም ነበር ፡፤ በአሉ ካለቀ በኋላ እነዚሁ ሕዝቦች ስለአስገባሪያቸው ናቡከደነፆር ጨካኝ አገዛዝና በነሱ በተለይ ያደረሰባቸውን በደል ገልጸው ነግረውት ነበር ፡፡ አፄ አፊላስ በዘመኑ እውነትን ያነገሰ ቅንነትን የሚወድ መንፈሱም እግዚአብሔርን በመፍራት የተሞላ ስለነበረ አዘነ ፡፡ በዚህ ብቻ አልቆመም ለናቡከደነፆር ደብዳቤ ፃፈ ፡፡ ደብዳቤውም እንዲህ የሚል ነበር ፡፡

በዚያን ጊዜ ሃያላን የሆኑ ፄዋ ሠራዊት አፄ አፊላስ ልኮ ግብፃውያንን መታ ፡፡ በቃዴስ የሚኖሩትን መንደሮች ኢቃጠለ የሚል ወሬ ለከለዳ ንጉስ ለናቡከደነፆር ደረሰው ፡፡ የከለዳው ንጉስም ለሱሳ ንጉስ ለጢሮስ ለአሶር ንጉሶች እንዲህ ብሎ ላከ ፡፡

የሱባያ ንጉስ በሰራዊቱና በአምላኩ ተመክቶ እኛን ለመውረር የትምክህት ደብዳቤ ላከልኝ ደብዳቤውም እንዲህ ይላል ፡፡ የከለዳ ንጉስ ናቡከደነፆር ሆይ ሕዝብሕን ሳያጠፉ የምታጠፋ ከሆንክ በነሱ ስም ሆኜ አጠፉሃለሁ ፡፡ ሕዝቡ የሚበላው ሳያጣ የምታስርብ ከሆንክ ያለርህራሄ እስሬ በረሃብ እገድልሃለሁ ፡፡ ሕዝቢ መኖሪያ ሳያጣ ማረፊያ ስለከለከልከውና ከፉ ተግባርን ስለጣልከበት መጣሁብህ የሚል ደብዳቤ ላከብኝ ፡፡ አሁን ደግሞ ግብፅን መታ ፤ በቃዴስ ያሉትን መንደሮች ኢቃጠለ የሚል ወሬ ሰማሁ ፡፡ ስለዚህ ኑ እንሰብሰብና ተማከረን እንግጠመው አለ፡፡ የሱባና የአሶር ንጉሶችም ይህ የምትለው ቃል ሁሉ ልክ አይደለም በኛና በአንተ መካከል በሰማርያና በኢየሩሳሌም የሚኖሩ አይሁድ ሁሉ ሰላምን አጥተው ሰላምን ፍለጋ ወደግብፅ ወደሱባ

ሄደው ተቀምጠው ሳለ ስለነገሩት እንጂ ፤ ይህ የታላቅ ሕዝብ ንጉስ ከኛ ይልቅ ሕዝባችን ስለወደደው ብንገጥመው ድል አድርጎ ይመልሰናል ያጠፋናል ። ስለዚህ የሚለንን ስምተን ማድረግ እንጂ ሌላ ነገር አታስብ የሚል መልስ ላኩበት ። ናቡከደነፆርም አማካሪዎቹን ሰብስቦ እነርሱም ስላልደገፉት በአንድ መቶ ሸማግሌዎች ስጦታ አሲዞአቸው ወደመረዌ ላካቸው ። የመረዌ ንጉስም ለአፄ አፈላስ ወደአክሱም ላካቸው ። ልመናቸውን ተቀበለ ። አፄ አፈላስም የዓለም አባት ተባለ ።

ወገኖቼ የዚህ ታሪክ ባለቤት መሆናችንን እናውቃለን ? ከራሳቸው አልፈው ስለሌላው አገር ሕዝብ የሚጨነቅ የሚያዝን መሪ !! ልብ በሉ የዛሬዎቹን ማፈሪያዎች ድንክዬ መሪ ተብየዎች እንኳን ለሕዝብ ሊቆሙ ሕዝቡን በመፍጀት የሚኩራሩ በሴራና በክፋት በጭካኔ የተሞሉ በኢምንት ግዛታቸው እጅግ የታበዩትን እስኪ ከቀደሙት ጋር አወዳድሯቸው !!!

አፄ አፈላስ ብዙዎችን ካስገበረ በኋላ የአባቶቹን የነመልከጼዴቅን ፤ የነኢትኤልን ፤ ሕግና ሥርዓት እንደገና እንዲታደስና እንዲፀና አደረገ ። ለሚገዛቸውም አገሮች ሁሉ እንዲህ ሲል አዋጅን አፅፎ ላከ ። ይህንን አዋጁን ልብ ብላችሁ ተመልከቱት ከ4500 ዓ .ዓለም በፊት የታወጀ ነው ።

እንዲህ ይላል !

የነገሥታት እራስ የጠቢባን ልብ አፄ አፈላስ እንዲህ ይላል — በዚህ ዓለም ምድር የምትኖሩ ነገስታትና አዛውንት ቃሌን ስሙኝ ትእዛዜንም ፈፅሙ ፤ የምላችሁን ሁሉ አድርጉ ቃሌን ስምታችሁ ትእዛዜን ፈፅማችሁ ብትገኙ ለእናንተ ክብር ለወገናችሁ ደስታ ለልጅ ልጆቻችሁ ደህንነት ለነሳችሁ ሰላምና ፍቅር ይሆናል ። — ኤል ብዬ የምጠራው አምላኬ ብሰማይ እርሱ በአየር የሕይወት መንፈሱ በምድር የምስራች ቃሉ ለዘለዓለም የሚኖር እርሱ ብቻ ነው ። ስሙም ቅዱስ አምላክ ለዘለዓለም ነው ። እንደሌሎች አማልእክት አይመስልም ተወዳዳሪ ፈፅሞ የለውም ። ባሕርዩ የማይገመት መልኩ ሊያዩት የማይቻል ስውር ሊቀርቡት የማይቻል የቃልና የመንፈስ ሃይል ነው ። የምስራች ቃሉ ግን ከሰው ልጅ ሰው ሆኖ የሚታይበት የሚዳስስበት ቀን ይመጣል ። ለዚያ ትውልድ ያየው ባለማየቱ ወዮለት !! የሕይወት መንፈሱ በዛን ጊዜ ለእያንዳንዱ የሰው ልጅ ሕይወትን ከማስተዋል ጋር ይሰጥ ዘንድ በቃል ይመራል ። ለሰው ልጆች የተዘጋጀውን ሁሉ ያድላል ።

ይህ ሊሆን ግድ ነው ይላል ፤ የሕይወት መንፈስ ፤ እናንተ አሕዛብ በባሕር ዳር የምትኖሩ በዋሻ የምትቀመጡ ስሙኝ አድምጡኝ የምትታመኑበት መሳሪያና አምልኮት ሁሉ ይሰበራሉ ይደቅቃሉ ። አንዱን በአንዱ መልክ አትመስሉት ወዮላችሁ ! ታፍራላችሁ — መህረምን በጨረቃ ፤ ብህ ጤቅን በኮርማ ወይፈን ፤ ሃደርን በላም በዛፍ ፤ ከሊኑምን በበግ ፤ ሚዛንን በተኩላ ፤ ሰቡንን በጉጉት አሞራ ፤ ስታርን በኮከብ ፤ ሃሩስን በጆፌ አሞራ ፤ ገዲን በንስር ፤ ሄፊርቱንምንና ሆትን በእባብ ፤ ሴቤቅን በዘንዶ በአዞ ፤ ቡባስቴናን በነብር ፤ ቡቀን በአንሽላሊት ፤ አምንን በፀሐይ ፤ ቡዳሃን በነፋስ ፤ ሺባንና ሂንዱህን በእሳት ፤ ሳርሀንና አጵሴን በተራራና በኮረብታ — የምትመስሉና የምታመልኩ አሕዛብ ሆይ !! ይህ ሁሉ እናንተ ስለሰራችሁትና ስለመስላችሁት እንደናንተ ፈራሽ ነውና ! ወደማይፈርሰውና ወደማይጠፋው የህይወት መንፈስ የምስራች ቃሉ ነው ። እሱ እራሱ ሁሉን ይገልጥላችኋልና ፤ ይሰጣችኋልም ይህን ብታደርጉ እናንተን ይቀድሳል ። እናንተም እንደርሱ እርሱም አንድ ነው እናንተም ባአንድ ትሆናላችሁ ። አሁን ግን ያላችሁት በሞትና በሕይወት መሃከል ናችሁ ። አባቶቻችን ቢበድሉት ታናናሾች አባቶች የታላላቆችን አባቶች ሕግና ትእዛዝ አፈረሱ ይኸውም አባትነትን ያጠፉ ዘንድ ነው ። እኔ ግን አባትነትን እኖር ዘንድ የሁሉንም ህግና ትእዛዝ መርጬ ልኬላችኋለሁ ።

አዳም የፈጣሪውን ትእዛዝ ባይፈጽም ከሕይወት ተሸረ ። የማይጠፋ ሞትን አገኘ ። ኖህ የአምላኩን ቃል ሰምቶ መርከቡን ቢሰራ ከዓለም ጥፋት አምልጦ ዘርን አተረፈ ። መልከጼዴቅ የተባለው የኢትኤልና የሃመራቢያ አባት የአዳምን ሞት አይቶ በሕይወቱ አምላኩን በፈጣሪው የሕይወትንም ቃል በሚሰዋው መስዋእት መሰለው ። ስለዚህ ስሙ የሰላም ንጉሥ የደህንነት ካህን ተባለ ። ልጁ ኢትኤል የአባቱን ምክር





ተቀብሎ የፈጣሪውን ሕግና ትእዛዝ ቢያደርግ እንደ አባቱም እንደመልከጼዴቅ የእግዚአብሔር ካህን ቢሆን አባትነትን አገኘ ። ይህችን ምድር እርስትህ ብሎ ሰጠው ። ከዘሩም ጭምር ታላቁን የሕግ ንጉሥ ነገሥት አቼን አስነሳለት ።

ወገኖቼ የእግዚአብሔር ህዝቦች ! እናንተ ይገባችኋል ፤ ምክንያቱም በውስጣችሁ ያለው እውነተኛው መንፈስ — እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ነውና ! የቀደሙት አባቶቻችን የደመቁ የተወደዱ የተከበሩ አስደናቂ የእምነት ተጋድሎ የነበራቸው ናቸው ።

የነዚህን ከላይ በመጠኑ ያነሳኋቸውን ከ4500 ዓመት ዓለም በፊት የነበሩ ታላላቅ ኢትዮጵያዊ ነገሥታት ሙሉ ታሪካቸውን እኔም አላገኘሁትም ።

መራሪስ አማን በላይ በገጠማቸው እድል የተቀበሩና የተረሱ ሳባዊ ሰነዶችን በማግኘታቸው ፤ ከሱባ ወደ ግእዝ ከግእዝ ወደ አማርኛ የመለሱትን መጠነኛ ታሪክ እንጂ ፤ እኛ ስንሰማ የኖርነው በቅርብ የነበሩ ኢትዮጵያውያን ነገሥታትን ታሪክ ሲሆን የሩቁን ግን አልሰማንም ። ለዚህም ነው በዚህ መልእክቴ ላይ ልገልፀው የሳበኝ ። የቅርቡን ታሪካችንንም ቢሆን ነጮች ዘርፈውናል ። ቅርሳችንን አሻግረዋል ፤ ደልዘዋል ፤ ደብቀዋል ፤ አቃጥለዋል ። የራሳቸውን የውንብድና ታሪካቸውን ቀባብተውና አሳምረው እንደታላቅ ገድል ለመላው ዓለም አስተምረዋል ። የዚህ መሃንዲስ ከነጮችም እንግሊዝ ቀዳሚውን ሥፍራ ትይዛለች ።

በዚህ ዘመን የዘለቀ የነጮች ዘረፋና ውንብድና ሳያገኘው በሱዳን ውስጥ ከፍርስራሽ ውስጥ መራሪስ አማን ያገኘው ግን ሸዋ የሚል የቀድሞ የአባቶቻችን ታሪክ ብዙ ቁም ነገር አስጨብጦናል ።

ወገኖቼ ! እነዚህ ሁለት ታላላቅ መንግስታት የነበሩበት ዘመን ሰው በሕገ – ልቡና የሚተዳደርበት ወቅት ነበር ። እግዚአብሔር በተወሰነ መጠን ቢገልጥላቸውም እንደ ሕገ ኦሪቱ እንደ ወንጌሉ የምህረት ዘመን በሙላት አልተገለፀም ። በጥቂቱ ቢናገራቸው አብዝተው ፈለጉት ወደዱት ታመኑበት በእርግጥም ፀኑበት አንፀባረቁበት ልኡል እንዲህ ነው የሚያደርገው ። ለታመኑበት ለወደዱት በማናቸውም ዘመን ተገልጦ የሚያፀና ድንቅ አምላክ ነው ። የአቼዎቹን ፀሎት ሁላችሁም ልብ ብላችሁ ካስተዋላችሁት ስለ ሕገ ኦሪት ስለ ወንጌል አያውቁም ነገር ግን ድንቅና አስገራሚ ፀሎታቸውን ስታስተውሉት በእውነትና በመንፈስ ማምለክ ምን እንደሆነ በትክክል ትረዳላችሁ ። የዛሬው ትውልድ ፤ የዛሬው መሪዎች በነዚህ ነገሥታቶች የእምነት ፅናትና መንፈስ ብርቱነት ፈጣሪያቸውን መውደድ ሲለካ ሚዛኑ ላይ ሲያርፍ እንዴት እንደሚቀል እዩት ።

ታላላቆቹ ነገሥታት በሺዎች ከተቆጠሩ አመታት በፊት በግዮን ዳርቻ በሳባ በአክሱም የነገሱ ዓለምን ያስገበሩ እንዲህ ከላይ እንደሰማችሁት ፈጣሪያቸውን ወደውታል ። ሕዝባቸውን በሥራቸው የነበሩትን ነገሥታትን ሁሉ በደነገጉት ሕግ ለአንዱ አምላክ ኤል ብለው ለጠሩት አስመልክዋል ። አስገዝተዋል ።

ልኡል በጥቂቱ በራእይ እየተገለጠ በተመረጡ አባቶች እነመልከጼዴቅ ፤ ኢትኤል ፤ ኢትዮጵ ፤ እየተገለፀ ትንቢት እንዲናገሩ እያደረገ መርቶአቸዋል ። አኑሮአቸዋል ፤ ባርኮአቸዋል ። በጥቂቱ ተገልጾ ታውቆአቸዋል ። እነርሱ ግን በሙላት በብርቱ ፈልገውታል ። ታምነውበታል ፤ ወደውታል ፤ አክብረውታል ። ለሕጉም ለፈቃዱም በደስታ ተገዝተዋል ። ምድርን ያንቀጠቀጡ መሪዎች ወድቀው ሰግደውለታል ። አመስግነውታል ። አስመልከውታል ።

ወገኖቼ ፤ እግዚአብሔርን ማስደሰት የሚቻለው በምንም አይደለም በማመን በመታመን ብቻ ነው ። እንደነሱ እጅግ በጥቂቱ ያውም በራእይ የተነገራቸውን በማመን እንዴት እንደወደዱት እንደታመኑበት እሱም እንዳስደሰታቸው እንዳላስፈራቸው አይታችኋል ። ዛሬስ ፤ ስነሱ እራሱን የከለለው አምላካችን ፤ በተለይ ህገ ኦሪትን በጣቱ ዕፎ በግልፅ ደንግጎ ፤ በአካል መጥቶ ከክብሩ ወርዶ የደነገገውን ሕግ ፃድቅነት እንደበግ ተሰውቶ አፅድቆ የዘላለምን መድህን አቁሞ ቀሊሉን ሸክም ወንጌሉን / የምህረት ዘመኑን / አጎናፅፎናል ። ግን እንዴት

ተቀበልነው ? ነቢያት ሃዋሪያትን እንዴት አደረግናቸው ? ሥራችንን ስለምናውቅ እኛው ምስክር ስለሆንን መድገም አላሻም ። እሱ በሙላት ሲፈልገን በጥቂቱም እንኳን አልፈለግነውም ። አልሰማነውም ፤ አልተቀበልነውም ። እንዲያውም ካድነው በተሰጠን እውቀትና ጥበብ ታምነን ካድነው ። በሱ ቦታ ይቺ ልቅምቃሚ እውቀታችንን ሥልጣኔያችንን ፤ሃብታችንን ሥልጣናችንን አመለክን ፤ እንዲያውም በእርሱ ፈንታ በእርሱ የተፈጠረውን ከክብር ይልቅ ውርደት የመረጠውን ዲያብሎስን አመንን በሥራና በፊቃድም መሰልነው እንደሱም ሆንን ። የአባቶቻችንን የትላንቱን በዚህ ልግታው እጅግ ብዙ አስደማሚ የልኡል አርበኞች እንደፀሐይ አብርተው አልፈዋል ።

ወደዛሬው እውነታ እንመለስ ።

ወገኖቼ ! አባቶቻችን የራሳቸውን ግዳጅ ተወጥተው እንደኮከብ አንፀባርቀው አልፈዋል ። በነሱ ጫማ ልንተካ ሲገባን ከንቱ ሆነን ስለቀረነው ስለእኛ ስናነሳ ብዙ ጉድ የተሸከምን ሆነን እንገኛለን ።

አባቶቻችን እንደዛሬው ትውልድ የኢድሜ ፍርፋሪ ተቀብለው አልኖሩም ። በረቀቀ ሕክምና አልተደገፉም ። በእምነት ፅናታቸው የእድሜን ከፍታ ልኡል አጎናፅፎአቸዋል ። ከላይ እንደምሳሌ ያነሳሁላችሁ ሁለቱም ነገሥታት ከ450 ዓመት ያላነሰ እድሜን ሁሉ ተወደው ተከብረው ኖረዋል ። በክብርም አልፈዋል ። ውሃ ልኮቹ ሚዛኖቹ እንላቸዋለን ። የዛሬ መሪዎች የሃገራችንም የውጪውም በመንደር እልቅናችሁ እጅግ የምትጎፈሉ ፤ ትእቢታችሁ ወሰን ያጣ ፤ ከህደታችሁን / ፈጣሪን መካድ/ እንደእውቀት በአደባባይ እየገለፃችሁ በድርጊታችሁም የአዋቂነት መለኪያ አድርጋችሁ በተዋህዶ እምነት ፀንቶ ያለውን ስትነቅፉ ስትሳደቡ ስታቃልሉ ቅርም የማይላችሁ ። መዳቡን ወርቅ ወርቁን መዳብ ያደረጋችሁ ። ተመዘናችሁ ተለካችሁ ያው ናችሁ ። ጊዜ ተትረፍርፎ ተሰጥቷችሁ እንኳን ልትፀፀቱ ንስሀ ልትገቡ ጭራሽ የትአለ እግዚአብሔር ? እስኪ እንየው? የምን ማስጠንቀቂያ የምን ምክር? እያላችሁ የምታፌዙ ፤ የእግዚአብሔርን ትእግሥት አጠናቃችሁ የበላችሁ ። ምን ዓይነት ጉደኛ ትውልድ ናችሁ ፤ ምንዝርና ማጭበርበር ፤ ማታለል ንቀት ሌብነት ዘረፋ ዘረኝነት በባዶ መኮፈስ ትእቢት ፤ እኔ ብቻ አውቃለሁ ባይነት ታላላቆችን ማዋረድ መናቅ መስደብ ፤ በእምነቱ /በተዋህዶ/ የፀናውን ማዋረድ ማሳደድ ምን ሥፍር ቁጥር አለው ይህ ሁሉ የቀንም የሌሊትም ምግባራችሁ ሆኖአል ።

ኢትዮጵያ አገራችን በዘመኗ ሁሉ ካፈራችው ትውልድ እንደ አሁኑ የወደቀና የረከሰ የጠፋ ትውልድ ከማህፀኗ ወጥቶ አልታየም ። በሁለመናው የተውሸለሸለ አገሩን የናቀ ፤ በተለያዩ አምልኮ ባእድ የተጠመደ ፤ የዲያብሎስ ድርስት በሆኑት የሃሰት እምነቶች የተጠመደ  ሆኖአል ። የሚገርመው ይመለሳል ተብሎ በትእግሥት ሲጠበቅ እንኳን ሊመለስ ያለውን እጅግ ጥቂት የሆነውን እያወከ እያናወፀ በመውሰድ ወደጥፋት እየቀላቀለ ይገኛል ።

ፈጣሪ ፍፁም ተክዶአል ። ዲያብሎስ ነግሶአል ። የእግዚአብሔር ትእግስት እከመጨረሻው ጠርዝ ተገፍቶአል ። የተዋህዶ እምነት እውነተኛውን አማኝ ማግኘት ፍፁም አዳጋች ሆኖአል ። ስለአገራችን ስንሰማ ከሁሉም በላይ የሚገርመን ቅጣቱ እየወረደበት መመለስ መፀፀት ፍፁም በልቡ ያለመኖሩ ሲሆን ፤ የሚገርመው ምሁር ተብዬው ጋዜጠኛው መሪ ተብየው እንደአሸን የፈላውን ዩኒቨርሲቲ ኮሌጅ ያጥለቀለቀው ወጣት ዲያስፖራ እያሉ የሚያንቆለጳጵሱት ትውልድ ሁሉም ማለት ይቻላል መፍትሄ እያለ በፍሉጋ የተጠመደው ከምእራቡ ዓለም የዲሞክራሲ ፍልስፍና ነው ። ተቀዋሚ ተብዬው ፕሮፌሰሩ ዶክተሩ በየሚዲያው ቀርበው ከሽነው በስላ´ምላሳቸው ሲደስኩሩ ከሰማይ መና የሚያወርዱ የሚመስሉ ናቸው ።

መላው ሕዝብ በረሃብ በኑሮ ውድነት በዘር ፍጅት በስደት በጭንቀት ሰላምን በማጣት ለመኖሪያውም ለእለቱም መጠለያ አጥቶ ሲጨነቅ ሲጠበብ መልሳቸው ዲሞክራሲ ስላልተጋት ነው ። ነገ ስንግትህ ትደናለህ የሚሉትን ነው የሚያዳምጠው ። ራሱ ሕዝቡ በጉዳትና በጭንቀት ተውጦ የየእለቱን ፕሮፓጋንዳቸውን እንደምሳና ቁርስ ጀሮውን ተክሎ ሲያዳምጥ ሲውል ማደሩ ነው ።

ልብ በሉ ወገኖቼ ! ከስድስት ጊዜ በላይ ያ ሁሉ ምክር ግሳፄ ፍርድ ሲፈስ ማን ሰማ ?አይናችሁ እያየ ጆሯችሁ እያደመጠ ፍርዱ እንደታዘዘው እየቀቀላችሁ በእሳት ባሕር እያጠለማችሁ / የረሃብ እሳት የዘር ፍጅት እሳት ፤ የዋስትና ማጣት እሳት የስራ የመጠለያ ማጣት እሳት ምን ስፍር ቁጥር አለው / ይህ ሁሉ እየወረደባችሁ ማን ሰምቶ ! የትኛው መንግሥት? የትኛው ሚዲያ ፕሬስ የትኛው ተቃዋሚ? የትኛው ምሁር የትኛው መሪ? ስለመልእክቱ ተናገረ :: መልእክቱ እየለካህ እየሰፈረህ እየነቀለህ እያነደደህ እየጠረገህ የታዘዘውን ጥፋት ሁሉ በየደረጃው እያሳዳገ ሲያጠፋህ ትስቃለህ ታፌዛለህ :: የኖሕ ዘመን ሕዝቦች ልክ እንደአንተው ነበር በኖሕ ጩኸት ሲያፈዙ የነበረው :: እንልበታቸው ሲደርስ ወገባቸው ሲደርስ ያው ያፈዙ ነበር እንጂ ሞኝ ሰሙ ፤ አንገታቸው ጋ ሲደርስ ግን ቢጮሁ በሸርፍራፊ ሰከንዶች መፍትሄ አይመጣ አከተመ አንተም ለታሪክ ትርክት እንደምሳሌ ትቀርብ እነደሆን እንጂ ሌላ ምን ትርጉም አለህ !

ዛሬ በአገራችን ያለው ሁኔታ እጅግ አስፈሪ እንደሆነ እንኳን በልኡል የሚታመነው ቀርቶ የጠፋውም ትውልድ ግራ ገብቶት እንደ ውሃ ላይ ኩበት ሲዋልል እየታየ ነው :: አገራችን ልትፈርስ ነው ። በዘር ልትገነጣጠል ነው እርስ በእርስ ልንጫረስ ነው እየተባለ ሁሉም በድንጋጤ የተዋጠበት ዘመን ነው :: ሁሉም እንደሚያውቀው አገራችን ኢትዮጵያን ወደዚህ ደረጃ ያደረሳት ዛሬ ጥግ ይገፍአለሁ የሚለው ሁሉም የሚጠራው ወያኔ በሚለው ስሙ እኔም የማውቀው ዘረኛ ቡድን ነው :: 27 ዓመት ሙሉ ሲፈጭህ ሲቆላህ የቆየው ክፉ ወፍጮ ከአጠገብህ ሳይርቅ በሩቅ መቆጣጠሪያ እየተቆጣጠረህ ግራ ተጋብተህ እንደ አሻሮ ትቆላለህ ፤ መፍትሄ የለውም :: እሱን ተከቶ የመጣው ከራሱ ማሕፀን የወጣው መንግሥት ደግሞ ችግርህን ከድጡ ወደማጡ አድርጎብሃል ::

አንዱን ዘር በአንዱ ላይ እያናከሰ የዘራው ዘር አሁን ፍሬው ደርሶ እሬቱን እየተጎነጨኸው ነው :: በመላው አገሪቱ የተቀጣጠለው የዘር ግጭት እራስህን በልቶ ይጨርስሃል እንጂ አሸንፎ መውጣት የለም :: እግዚአብሔርንና ምክሩን ስለናቅህ ፤ በአምልኮ ባእድ ፤ በራስህ የኢቢሲዲ እውቀትህ ስለታመንክ ፤ ለማመን ብትሞክርም ነጩና አረቡ ውስጥ የመሸገው ዲያብሎስ በረቀቀ ድርሰቱ በፈጠረው እንደ ካቶሊክ ፤ ፕሮቴስታንት ፤ እስላም በመሳሰሉት እምነት ተሸሽገህ የመፍትሄ ያለህ ትላለህ ! ቀጣፊ ትውልድ ፤ ሴባ ፤ አመንዛሪ ፤ትእቢተኛ ፤ አገሩን የጠላ ትውልድ ! ፈልግ መፍትሄ ! ከሰመይ እነደመና ታወርድ ይሆናል :: መቼም ይሳነኛል የምትለው ነገር የለም :: ከንቱ ትውልድ ! ምን ተነካህ ገና ምንም ሳይደርስብህ ! እዚህም እዚያም በማያቋርጠው ግጭት ጥቂት ሰዎች ስለሞቱ ፤ ስለቆሰሉ ፤ ስለተሰደዱ ትደነቃለህ አገር ፈረሰ ትላለህ ! መቼ ተጀመረ ! ከዚህ መልእክት መውጣት በኋላ ጉድህን ታየዋለህ ::

በከተማችን አንድን ዘር ለማገንስ በቀደሙት መልእክቶች የተሰጡትን ማስጠንቀቂያዎች ንቃችሁ የድሃው ቤት አፍርሳችሁ የተለያየ የማጭበርበሪያ ስም ለጥፋችሁ :: ከንጉሠ ነገሥቱ ጀምሮ በገንዘባቸው ገዝተው የኖሩበትን የመኖሪያ ይዞታ ስነድ አልባ በሚል ስታስጨንቁ ስትበድሉ ስትነጥቁ የማይሸከሙትን የገንዘብ ክፍያ ስትጥሉ ሊዝ ግባ የሚል የሕግ ሽፋን የተሰጠው ንጥቂያን ስትተገብሩ ፤ የወደዳችሁትን ቦታ ድሃውንና ጎጀውን በልማት ስም በዶዘር ስታፈርሱ ፤ በምትኩም የራሳችሁን ዘር ፎቅ እንዲገነባ ስታደርጉ ፤ ሁሉንም የአገሪቱን ባንክ ኢንሹራንስ በቁጥጥራችሁ ሥር አድርጋችሁ ለዘራችሁ ያለማያገ ብሩን በገፍ ስታድሉ ፤ የገበሬውን መሬት ነጥቃችሁ የራሳችሁን እርሻ ስታደራጁ ፤ በሚጋ ፕሮጀክቶች ስም ሁሉንም በራሳችሁ የዘር ቡድን አድርጋችሁ ለጆሮ የሚሰቀጥጥ ዘረፋ ስታደርጉ የራሳችን ከተማ ባላችሁት የአገሪቱን ሃብት ሁሉ በጠራራ ፀሓይ ያለማቋረጥ ዘርፋችሁ ስታከማቹ በውጪ የውጭ ምንዛሪ ስታከማቹ ድሃውን ወደመጨረሻው ድህነት ስትነዱ ፤ መላውን ትውልድ ለስደት ስትዳርጉ በየባሕሩ ሰምጦ እዲቀር ስታደርጉ ፤ የሚበዛውን የተቃወማችሁን ስታፍኑ ስትገድሉ ስትሰውሩ ሃይ የሚላችሁ ጠፍቶ ዛሬም ለጊዜው ጥግ ብትይዙም ገና ብርቱ እዳ አለባችሁና አታመልጡም :: በሰውኛ ታክቲካል ማፈግፈግ ትሉት ይሆናል/ዛሬ ያለውን ሁኔታ/ :: አታውቁትም ድሮም ንቃችሁታል ልኡል እግዚአብሔር ዛሬ ያለውን ነገም የሚሆነውን ቀድሞም ተናግሮአል ያም ይሆናል ዛሬም እየሆነ ነው :: እናንተም በቅን ፍርዱም ትጠረጋላችሁ እንጂ በዚች ምድር ምሽግም ሆነ መከለያ የላችሁም :: ለናንተ ሽፋን የሚሰጡ

ከለላ ያደረጉላችሁ የውጪውም የአገር ውስጥም የሆኑ ሁሉ እንዲሁ በቅን የልኡል ፍርድ ይደመደማሉ እንጂ አያድኗችሁም :: መልካም ሥራ እንጂ መልካም ምላስና ብልጠት የሸንገላ አንደበት በምንም መስፈርት ዘላቂ መፍትሄ አያመጡም :: የአህያ ባል ከጅብ አያስጥልም ::

የድሃ ደም ፤ የድሃ እምባ ፤ በማንአለብኝነት የፈሰሰ የቅኖች ደም ፤ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ደም ሁሉም የሚያስከፍሉ ታላቅ እዳዎች ናቸው :: ፍቅር የአውሬዎችና የደም አፍሳሾች መሸፈኛ አይሆንም :: ወንጌላዊው ዮሃንስ በአንደኛ መልእክቱ ሞት ለሚገባው ሞትን አለምንም ያለው ወዶ አይደለም :: ስለእግዚአብሔር የምህረትና የቅጣት አካሄድ በሚገባ ስለሚያውቅ እንጂ !

የዘመኑ ወገኖቼ !!

በከተማችን አንድ ትልቅ ቂራ አለ :: የወፈሩ የጠገቡ የሰቡ በሬዎች ከዚህ ቄራ ገብተው ይታረዳሉ :: ይበለታሉ :: ይከፋፈላሉ :: እንግዲህ ወገኖቼ በድሃ ደም ፤ በዘረኝነት ፤ በዝርፊያ ፤ በሥልጣን በጠመንጃ የተመካህ ፤ የትላንቱም የዛሬውም አሊቃና ምንዝር የሆንከው ሁሉ እንኳን ደስ አለህ ቄራ ደርሰሃል :: እንደአረድክ እንደዘረፍክ እንደፈነጨህ መዝለቅ የለምና ስላቢቃ እንደበሬዎቹ እግዚአብሔርም ላንተ ቄራ አዘጋጅቶልሃል :: በዚያ ትደመደማለህ ::

ኢትዮጵያን የጠላ ፤ ድንግልን ተዋህዶን እምነት የጠላ ፤ ባንዲራዋን የጠላ ሁሉ የጠረጋል እንጂ በፍፁም አይድንም :: ማምለጫም መዳኛም መንገድ ፍፁም የለውም :: በሰሜን በምእራብ በምስራቅ በደቡብ የመሸጋችሁ አገራችንን እንደ አንጋሬ ቆዳ ወጥራችሁ ያስጨነቃችኋት ሁሉ በከፋ እሳት ትጠረጋላችሁ እንጂ ከእንግዲህ እድሜ የላችሁም :: የሚጠቅማችሁን ጊዜ በደል በበደል ላይ ፤ አማጽ በአመጽ ላይ እየጨመራችሁ መጣችሁ እንጂ ቅንጣት የመጸጸት ምልክት አልታየባችሁም :: በመሆኑም ስታፈጅ ጊዜው አለቀ ተከደነ :: የመጣውን መቀበል ብቻ ነው ::

ስለአገሩ በየድንበሩ የወደቀው ወገን ፤ ስለኢትዮጵያ የተሰዋ ፤ የቆሰለ ፤ እንደ የኔ ብጤ የተጣለ ዳግም ፍርድን ያገኛል እንጂ ውለታው አይጣልም :: አንተ ደሙን ያፈሰስከ የትላንቱም የዛሬውም ብርቱ እዳ አለብህ በብዙ እጥፍ ትከፍላለህ :: በደም ከጨቀየው ማንነትህ ጋር በተለይም በሰሜን የመሸግህ የእዳ መክፈያ ሰአትህ ደርሶአልና ተዘጋጅ ይልሃል የሰራዊት ጌታ እግዚአብሔር :: አገር ቆርሶ ለባእድ መሥጠት ቦታ ለማስፋት ዘርን ማጥፋት መጨፍጨፍ ሁሉም ዛሬ እጫፍ ስለደረሱ ያንተ መጥፎ ትውልድ ከታመኑብህ ምንዝሮችህ ጋር ትቀበራለህ ፤ ታሪክም ትሆናለህ ::

በጥቅሉ በአገሬ በኢትዮጵያ ያለህ በውጪም ያለህ ፤ ከእውነተኛይቱ ተዋህዶ እምነት የወጣህ ፤ ይህችን ብሩክ ምድር የድንግል ምድር ፤ ልኡል በሰስት የሚያያት ምድር ፤ የጠላሃት ፤ ለጥፋቷ የደከምክ ፤ በባእድ እምልኮ የታመንክ ፤ አመንዛሪ ሌባ ዘረኛ ትእቢተኛ ጨካኝ ትውልድ ፤ እስላም ፤ መናፍቅ ፤ ካቶሊክ ፤ ተብታቢ ፤ ድግምተኛ ፤ ጠንቋይ ባለውቃቢ ፤ ዋቄ ፈታ መተተኛ ሁሉ ከኢትዮጵያ ምድር ትጠረጋለህ :: አንተ ከተጠረግህ በኋላ ኢትዮጵያ የዓለም ሁሉ ጌታ መጠለያ የቅን ሕዝቦች መፅናኛ ትሆናለች :: የልኡል ቃል እንዲህ ይላል !!

— በኢትዮጵያ ወንዞች ማዶ ላለች ክንፍ ያላቸው መርከቦች ላሉባት መልእክተኞችን በባሕር ላይ የደንገል መርከቦችንም በውሃ ላይ ለምትልክ ምድር ወዮላት ! እናንተ ፈጣኖች መልእክተኞች ሆይ ወደረጅምና ወደ ለስላሳ ሕዝብ ከመጀመሪያው አስደንጋጭ ወደሆነ ወገን ወደሚሰፍርና ወደሚረግጥ ወንዞችም ምድራቸውን ወደሚከፍሉት ሕዝብ ሂዱ :: በዓለም የምትኖሩ ሁሉና በምድር የምትቀመጡ ሆይ ምልክት በተራሮች ላይ በተነሳ ጊዜ እዩ ! መለከትም በተነፋ ጊዜ ስሙ !!!

እግዚአብሔር –በፀሐይ ጮራ እንደ ደረቅ ትኩሳት በአጨዳም ወራት እንደ ጠል ደመና ሆኜ በማደሪያዬ በጸጥታ ተቀምጬ እመለከታለሁ ብሎኛልና :: እርሱ ከመከር በፊት አበባ በረገፈ ጊዜ የወይኑን ፍሬ ጮርቃ ሲይዝ የወይኑን ዘንግ በማጭድ ይቆርጣል ጫፎቹንም ይመለምላል ያስወግድማል :: በተራራ ላይ ላሉ ነጣቂዎች ወፎች ለምድርም አውሬዎች በአንድነት ይቀራሉ ነጣቂዎችም ወፎች ይባጁባቸዋል :: የምድርም አውሬዎች ሁሉ ይከርሙባቸዋል :: በዚያን ዘመን ለሰራዊት ጌታ ለእግዚአብሔር ከረጅምና ለስላሳ ሕዝብ ከመጀመሪያው አስደንጋጭ ከሆነ ወገን ከሚሰፍርና ከሚረግጥ ወንዞችም ምድራቸውን ከሚከፍሉት ሕዝብ ዘንድ እጅ መንሻ የሰራዊት ጌታ የእግዚአብሔር ስም ወደሚገኝበት ሥፍራ ወደ ጺዮን ተራራ ይቀርባል ::
ትንቢተ ኢሳኢያስ ምእራፍ 18 በሙሉ

## ቤተ ክርስቲያናችን / የኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን/

ወገኖቼ ! የተዋህዶ አምነታችን ፤ ቤተ ክርስቲያናችን ዛሬ ምን ላይ ነች የሚለውን በመጠኑ እንመልከት :: ባጭሩ ቤተ ክርስቲያን የተዋህዶ ቤታችን በዘርፈ ብዙ ጥቃት ተመታ በታላቅ አደጋ ውስጥ ነች ::

የሕይወት ቤት ፤ የድንግል ቤት ፤ ራሷ የሆነው የጌታችን መድሃኒታችን እየሱስ ክርስቶስ ቤት ፤ የተዋህዶ ሕዝበ ክርስቲያን ቤት ነበረች :: ዛሬ ግን በውስጧ የመሸጉት እነተሃድሶ ፤ እነፀጋ ፤ እነቅባት እነመናፍቅ እግርና እጇን ተብትበው መንጋውንም ለአውሬ ስጥተዋል :: ድንቋ ቤተ ክርስቲያናችን ዛሬ ሽባ ሆናለች :: ወገኖቼ ! ቤተክርስቲያን የንግድ ማእከል ፤ ፎቅ ሰሪ አከራይ ነጋዴ ሆናለች :: አገልጋዮቿ በአብዛኛው እንደ አፍኒንና ፊንሀስ ያሉ በመሆናቸው እርኩሰትን አንግሰዋል :፤ የወፈረውን በግ አርደው በሊታ ሆነዋል የከሳውን ደግሞ የሚወረውሩም ናቸው :: ወገኖቼ በተጉ አባቶች ሰማእትነት ተጋድሎ የፀናችው ቤተ ክርስቲያናችን የፖለቲካ ሹመኛ መጫወቻ ሆናለች :: የሚበዙቱ አባቶች በፍርሃት የተሸበቡ ለገዢው የተንበረከኩ ናቸው :: ዘረኝነትን የመንግስት ሰላይነትን የለበሱ የከበረውን ቀሚስ ጥምጣም መስቀል ለመከለያ ጨብጠው እለሃፍረት የሰፈሩባት ሆናለች :: በቅዳሴአቸው በማህሌታቸው በወረባቸው በኪዳን ሁሉ ጌታን ስቅለው የሚወጉ ሆነው ተገኝተዋል :: እግዚአብሔርን በከፍተኛ ደረጃ ለቁጣ ቀስቅሰዋል በቅናትም እንዲነሳ አድርገዋል ::

ቤተ ክርስቲያን በታሪኳ ሁለት ፓትርያርክ አንግሳም አታውቅ :፤ ነገር ግን ለፖለቲካው ለመንግሥት ድጋፍና ሕልውና ሲባል የቤተ ክርስቲያን ቀኖና ይጣሳል :: ቤተ ክርስቲያናችን ለአገራችንም ለዓለምም ሚዛን ውሃ ልክ ናት :፤ ሁሉም በሷ ልክ ይመዘናሉ :: ዛሬ የአባቶቻችንን ድንበር ያፈረሱ ምንፍቅናን ያነገሱ የኮተለኩ ፤ የድንግልን ክብር የቀነሱ ፤ ጌታ የከፈለውን ውድ ዋጋ ያራከሱ እነዚህ ነጋዴዎች ፤ ስለሆዳቸው ስለደሞዛቸው ብቻ የሚገዳቸው ፤ ቤተክርስቲያናችን አይታም ሰምታው በማታውቀው ጥፋት የጣሏት የዲያብሎስ የውስጥ አርበኞች ፍርዳቸው ወጥቶአል ::

ለባለጊዜዎቹ በቤተ ክርስቲያናችን ነፍሳቸውን አስጨንቀው ተገፍተው ፤ አንገታቸውን ሰብረው ፤ ስፍራቸውን ለቀው ለሚያዝኑት ለሚያለቅሱት ወገኖች ልኡል ድንግል ደርሰዋል :: ፍርዳቸውንም እንደ ፀሃይ ያወጡታል ::በሕዳር ወር ውስጥ ለያዛችሁት ምህላ መልሱ ይኸው መልእክት መሆኑን እንድታስተውሉና መልስ ለሚጠብቀው ከልኡል የተቆረጠውን እውነት ልትነግሩት ይገባችኋል ::

በአሁኑ ሰዓት ቤተ ክርስቲያናችን ታላቅ ሰማእትነትን የተቀበሉ አገልጋዮቻን አፍልሳለች :: በጅጅጋ ያለቁት የተዋህዶ አርበኞች ከልኡል የሕይወት አክሊልን ተቀዳጅተዋል :: ዛሬ ተዋህዶን የጠሉ መናፍቃን ፤ ዋቄ ፈታዎች ፤ እስላሞች ፤ ካቶሊኮች ፤ ተብታቢ መተተኞች ባጠቃላይ በዚች በዘመን ሁሉ በፀና ተጋድሎዋ የገሃነም ደጅ ያልቻሏት ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያናችንን ለማጥፋት ብትደክሙም አሸንፋችኋለች :: በእሷ ላይ

የዘመታችሁ ፤ የጠላችኋት ያሳደዳችኋት ያፈረሳችኋት ሁሉ በዚህ መልእክት የሚረጋግጥላችሁ ፍፁም የእግዚአብሔር የድንግል ጠላቶች ስለሆናችሁ በሙሉ ያለርህራሄ ከምድረ ገፅ ትጠረጋላችሁ ለእሳትም ትጣላላችሁ :: ወደዳችሁም ጠላችሁትም የተዋህዶ አርበኛ የተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን ምድርን ይወርሳሉ ፤ ይነግሳሉ ዓለምን ይገዛሉ :: ሁሉህም በምርኮ ለጀግኖቹ የተዋህዶ አርበኞች ተሰጥተሃል :: እንዴት ይሆናል ፤ እድሉ ካለህ ታየዋለህ :: ከዚህም ውጪ የሚሆን አለ ብለህ አታልመው :: የዐመጽ ብድራትህን ትከፍላለህ ::በድሃ ደም በቤተ ክርስቲያናችን በተዋህዶ አርበኞቻችን ደም የጠመከውን ጠላ ትጋተዋለህ :: ትደመደማለህ ጥቀበራለህ ::

ቤተ ክርስቲያናችን የተዋህዶ አርበኞች ቤትን ንቃችሁ በውስጧ የተሰገሰጋችሁ ተኩላዎች አንደኤሊ አንገታችሁ ተጠምዝዞ ትወገዳላችሁ :: ሌሎችም ዲያቆን ቄስ ካህን ጳጳስ ራሳችሁን ያሰማራችሁ በአፍኒንና በፊንሀስ ጫማ የተገኛችሁ በሙሉ ታልቃላችሁ :: የኢትዮጵያ ተዋህዶ አርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያናችን እንደጌታዋ እንደመድሃኒታችን እየሱስ ክርስቶስ መቃብሩን በስላሴና በድንግል በሊቃነመላእክትም ሃይል አፍርሳ ትነሳለች :: በምድር ሁሉ ላይ ትነግሳለች :: የእምነታችን መሪም ትሆናለች :: የሚነግሱት ምድርንም የሚመሩአት የእግዚአብሔር አገልጋዮች እምጣ የወለደቻቸው ልኡል ባርኮ ያነገሰላት ልጆቿ ናቸው :: ምድርን በልኡል ብርቱ ክንድ ፀጥ አረጭ አድርገው በእውነትና ፍትህን በማንገስ የሚገዙአትም ናቸው :: ቤተ ክርስቲያንን እንደአይናቸው ብሌን የሚጠብቋት የሚታዘዙላትም ናቸው ::

ወገኖቼ ! የኢትዮጵያ ተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን የመላው ዓለም የእምነቱ መሪ ትሆናለች :: ሌላ እምነት በምድር ዳግም አይሰራም :: ተዋህዶአችን መንፈሳዊ አባትነቷ ምድርን ሁሉ ይከድናል :: በበቁ አባቶች ትመራለች :: ትባረካለች :: በሶስት ዓይን ትጠበቃለች ::

1/ ብርሃናዊው የኢትዮጵያ መንግስት : —

መጪው የትንሳኤው ዘመን ከተወደደችው ኢትዮጵያ ተነስቶ አፍሪካን ፤ መካከለኛው ምስራቅን ጨምሮ በመደበኛ ግዛትነት አካቶ የሚያበራ ልኡልም ድንግልም የሚነግሡበት የተራራዎች ሁሉ አናት ነው :: በሕግጋተ ሥላሴ የሚፀናው ብርሃናዊው የኢትዮጵያ መንግሥት ዓለምን ሁሉ በበላይነት የሚገዛ የሚያስተዳድር ነው :: በተዋህዶ እምነታቸው የፀኑ በልኡልም በድንግልም የተመሰከረላቸው እረኞች ናቸው በመላው ምድር የልኡልን ሕግ የሚዘረጉት :: ለተዋህዶ እምነትም ዘብ ከሚቆሙት ሶስቱ አካላት አንዱም ነው ::

2/ ቤተ ክህነት : —

ቤተ ክህነት በመጪው የትንሳኤው ዘመን እንደ አዲስ በአባቶቻችን መንገድ በፀናችው የተዋህዶ እምነታችን የምትታነፅ ናት :: በበቁ አባቶች ፤ ዛሬም በውስጧ ሆነው ነገር ግን ፍፁም በዲያብሎስ ተረግጠው ያሉትን አቅፉ ፤ ከውስጧም ተገፍተው በውጪው /ከቅጥሯ ውጪ/ ሆነው ወድቀው በእንክርት በእስራት በመራብ በመሰደድ በጥቅሉ በታላቅ ጉዳት ውስጥ ሆነው ያሉትን ጨምራ ልኡል በሚያውቃቸው በቀባቸው ባፀደቃቸው በወደዳቸው የክህነቱንም ሥልጣን በቅድስና ያለነቀፋና ሕፀፅ የጨበጡትን በመሪነት አስቀምጣ ዓለምን ሁሉ የምትመራ የኢትዮጵያ አርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን ቤተ ክህነት ናት :: ወገኖቼ ! ዛሬ የምታዩአት ቤተ እምነታችን በዲያብሎስ በነገሱ የጨለማው እምነቶች ፍፁም ተመትታለች :: ቀብሮ ተኩላ እባብ ጊንጥ ወርሶአታል :: ክብሯ ተገሰሶአል :: ንግድ ፤ ገንዘብ መውደድ ፤ ትእቢት ፤ ኑፋቄ ፤ ራስን ማስመለክ ፤ ምእመኑን ለአውሬ መስጠት ፤ የገገርዎች መሳሪያ መሆን ይህን ሁሉ በሕይወታቸው ያነገሱ ተኩላዎችን ሹማና አንግሳለች :: በከሃዲዎች ተሞልታለች ስሟ እንጂ ከአገልጋዮቿ ሕይወት ያለው እምነት ጠፍቶአል ::ይህ ሁሉ ግን ቀደምም አሁንም በዚሁ ስምንተኛ መልእክት የሚረጋገጠው ተዋህዶ እንደገና በክብር በታላቅ ግርማ እምላኳን ድንግልን እንግሳ ተኩላና ቀብሮውን ጠርጋ ትነሳለች :: ተዋህዶ እምነታችንን በቀጥታ እነደ አይኗ ብሌን ትጠብቃለች ትመራለች ::



Scanned by CamScanner

3/ ቤተ ምርፋቅ / መማክርተ ካህናት ሲሆን የሁሉም የበላይ እራስ እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ይሆናል ። ከፍም ዝቅም የሚል ነገር የለም ።

ቤተ ምርፋቅ ፡ — ቤተ ምርፋቅ ይህ አካል ራሱን ችሎ በቤተ ክህነቱም በመንግሥታዊ አስተደደር ተቋማት ጎን ለጎን የሚቆም አካል ነው ። ሥራው የተዋህዶ ቤተ ክርስቲያንን ዶግማዋን ቀኖናዋን ጠብቃ መጓዟን እለት በእለት የሚከናወነውን ሥርአተ አምልኮውን በሕጉ በስርአቱ አለሕፀፅ መከናወኑን የሚከታተል አካል ነው ። ይህ አካል ከሁሉም በላይ በበቁ አባቶች ፤ ስላሴም ድንግልም በመስከሩላቸው የሚዋቀር ነው ። ሁሉም አባቶች የክህነት ሥልጣናቸውን የጠበቁ የሚሆኑበት ነው ። በቤተ ክርስቲያናችን አስተምህሮ ከፍታውን የጨበጡ መሆንም የሚገባቸው ናቸው ። በአባቶቻችን አጠራር አራት ዓይናማዎቹ የሚባሉትን ማለት ነው ። በመንፈሳዊው እውቀቱ ብቻ ሳይሆን ለስጋውም እውቀት ከሌላው የማይተናነስ አጠቃላይ እውቀት የጨበጡም ናቸው ። በዚህ አካል የሚመደቡ አባቶች እጅግ የከበሩ በመንግሥትም በቤተ ክህነትም የሚወደዱ የሚከበሩ የሚፈሩም ናቸው ። በሕዝብም እንዲሁ የሚወደዱም ናቸው ። በሕግጋተ ሥላሴ በታወጀው ሥርዓት አገዛዝ ውስጥ ሥልጣናቸውና ሃላፊነታቸው የተገለፀና የሠፈረ ስለሆነ ከዚህ በላይ መግለፅ አስፈላጊ አይደለም ። በጥቅሉ ሶስተኛው ዓይን ናቸው ። የተዋህዶ ቤተ ክርስቲያን በሶስት ዓይን ትጠበቃለች ተብሎ በጥቅሉ የተገለፀው ለዚህ ነው ።

እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ፡ — ወገኖቼ የእግዚአብሔር ሕዝቦች ኢትዮጵያ በሥላሴ በድንግል የተወደደችው የነገሰችው – ኢትዮጵያ! ሕይወቷ የሆነችው ተዋህዶ ቤተክርስቲያናችን – የብርሃናዊው መንግሥት አገዛዝም የሁሉም እራሳቸው ጌታችን መድሃኒታችን እየሱስ ክርስቶስ ነው ። በመሆኑም እግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ የሁሉም —ዓለምን የሚመሩ የሚገዙ የልኡል የድንግል ባሮች መንግስታት ንጉሣን ሁሉ መሪያቸው ዳኛቸው አስተማሪያቸው ነው ። ይህ ሁሉ በሥላሴ ሃይል ይፈፀም ዘንድ ተወስኖአል ። እንግዲህ ጠፊው ትውልድ ሩቅ አልመህ ቅርብ ያደርከው ከሃዲ ከንቱ ትውልድ ብታምነውም ባታምነውም ሰምተኸውም ከሆነ ሰማኸው እንጂ አታየውም ። እንዳፌዝክ እንደተፈላሰፍክ እንደዘለፍክ ላንተም በዚሁ መልክ በብዙ እጥፍ ይሰፈርልሃል ። በውርደት በከባድ ስቆቃ ከምድረ ገፅ በአስጨናቂ መላእክ ሞት ትወሰዳለህ እጣህ ይህ ነው ። የብርሃኑን ዓለም አንተም ዘርህም በፍፁም አታዩትም ።

ወገኖቼ የእግዚአብሔር ሕዝቦች !!

በመልካሙ ዘመን አምልኮተ እግዚአብሔር በእውነትና በመንፈስ እንጂ በዘልማድና በስሜት አይሆንም ። አባቶቻችን የተዋህዶ እምነትን መሰረት ሲያሲዙ ሁለመናቸውን ሰውተው እንጂ እንደ ልማድ ሥራ በመሥራት አልነበረም ። እንዲሁም እንዴ ግለው በትንሽ ፈተና የሚቀዘቅዙ አልነበሩም ። እምነታቸው እውነትን ማስመሰል ሳይሆን መሆንን የለበሰ ነበር ። በእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ የተመሉ በልባቸውም በነፍሳቸውም በሃሳባቸውም ፍጹም አምላካቸውን የወደዱ ነበሩና ሌትም ቀንም ፈጣሪያቸውንና ትእዛዙን በልቡናቸው የሚያመላልሱ ነበሩ ። ቅንነትን ትህትናን ቸርነትን እውነተኝነትን ደግነትን ወንድምን መውደድን መታመንን ቅድስናን የተላበሱ ነበሩ ። ሃሰትን ምንዝርናን አምልኮ ባእድን ጥንቆላን ተብታቢነትን እጅግ የሚጸየፉ ነበሩ ። ዛሬ ትውልዱ እምነት የሌለው ቀጣፊና አታላይ ዘረኛ ትውልድ በመሆኑ እንደ ስልጣኔው እንደ ህክምናው መራቀቅ እድሜን አላገኘም ። አባቶቻችን ከመቶው ዘለው እየኖሩ ኑሮአቸውን እንደ እንግድነት ቆጠሩት እንጂ እንደዛሬው ትውልድ የዘለዓለም ንዋሪ መስለው አላሰቡትም ። እንደ አሁኑ ትውልድ መጠነ ብዙ የበሽታ ዓይነት አያውቁም ነበር ። መቶን እድሜ መድረስ ከዚያም አልፎ አለመኖር የመቀሰፍን ያህል ይቆጥሩት ነበር ። የዛሬው ትውልድም/ ሁሉም የዓለም ሕዝብ /መቶ ዓመት ቀርቶ ሃምሳ ዓመትን ለመኖር የሰማይ ያህል እርቆታል ። ወገኖቼ ! ዛሬም ይህ የጠፋ ትውልድ የኖህን ዘመን የጥፋት ትውልዶች በብዙ በልጦና አሻሽሎ

የተካ በመሆኑ የተተደሰውን መልካም ቃል ለውሾች አትጣሉ እንዳለው የልኡል መልእክትን ለከንቱዎቹ ስጥታችሁ በፈዛቸው ባትቆስሉ መልካም ነው ::

ወገኖቼ ! የእግዚአብሔር ሕዝቦች ! ይህን መልእክት በትእግስት በፅሞና እንደምታነቡ እርግጠኛ ነኝ ! መልካም መንፈስ ያለበት ሁሉ መልካምን ያውም ከልኡል የሆነውን ለማንበብ ጉጉቱ ከፍ ያለ እንጂ የታከተ ስሜት የለውም ::

እንግዲህ ወደአባቶቻችን ልመለስ ! — አዳም አባታችን የፈጣሪን ትእዛዝ ባይፈፅም ከሕይወት ተሻረ :: የማይጠፋ ሞትን አገኘ :: ኖሕ የአምላከን ቃል ሰምቶ መርከቡን ቢሰራ ከዓለም ጥፋት አምልጦ ዘርን አተረፈ :: መልከፄዴቅ የተባለው የኢትኤልና የሃሚራቢያ አባት የአዳምን ሞት አይቶ በሕይወቱ አምላኩን በፈጣሪው የሕይወትንም ቃል በሚሰዋው መስዋእት መሰለው :: ስለዚህ ስሙ የሰላም ንጉሥ የደህንነት ካህን ተባለ :: ልጁ ኢትኤል የአባቱን ምክር ተቀብሎ የፈጣሪውን ሕግና ትእዛዝ ቢያደርግ እንደአባቱም እንደ መልከፄዴቅ የእግዚአብሔር ካህን ቢሆን አባትነትን አገኘ :: ይህችን ምድር እርስትህ ብሎ ሰጠው :: ከዘሩም ጭን ታላቁን የሕግ ንጉሠ - ነገሥት አፄን አስነሳለት ::

እንግዲህ ልበሉ ወገኖቼ ! አባቶቻችን ማን እንደነበሩ ቀደም ባለው ገፆች የሁለቱን ታላላቅ አፄዎች ታሪክ ሰምተናል :: በእውነትና በመንፈስ ልኡል በሙላት በፅናት በመታመን የፈለጉ ፤ ሕዝቦቻቸውን በፈቃዱ ሕግ /ሕገ ልቡና / የገዙ የዓለምን ሁለት ሶስተኛ በሰላም ያስገዛላቸውም የምድራችን የሰላም አባት ተባሉ :: እግዚአብሔር በትንሹ ራሱን ቢገልፅላቸው እጅግ አብዝተው የወደዱት የፈለጉት በሕጉም የተደሰቱ የእምነት ጀግኖች ነበሩ :: ወገኖቼ በእውነትና በመንፈስ ማምለክ ሚስጥሩ ጥልቅ ነው :: ከልብ ልኡልን ለሚፈልጉ ብቻ ነው የሚገለጥላቸው :: አባቶቻችን እንደፈለጉት ሁሉ ወደዳቸው እድሜን ክብርን አለበሳቸው :: የታመነው ጌታ /ሥላሴ/ ::

በእውነትና በመንፈስ ያመለኩት አባቶቻችን ዛሬ ከወደቀችውና የዲያብሎስ ውላጆች መራገጫ ከሆነችው ኢትዮጵያ ተነስተው ነበር ዓለምን የገዙት የመሩት ያስገበሩት :: እስኪ የትኛው የነጭ ዓለም ነው ይህን የመሰለ በእውነትና በመንፈስ አምላኩን የፈለገና የከበረ መንግሥት ? የለም :: የውሸት ድርስት ሕይወት እንደማይሆን ከአባቶቻቸው የዲያብሎስ አገልጋዮች የተቀበሉትን የጥፋት ምግባርና የክፋት አባትነት እያየን እዚህ ሰዓት ደርሰናል :: እነሱም ዛሬ ፍርዱ ሲገለጽ ከፊታቸው የቆመውን እድል ፈንታቸውን ሊቀበሉት ቆመዋል ::

ወገኖቼ ! ዛሬ የምናያቸው ነጮች የማያውቁትን ከአባቶቻቸው ያልተቀበሉትን መሰረት እንኳ ያላበጁላቸውን ደርሰው የሃይማኖት መሪ ፤ ሃያል መንግስት ፤ የዓለም ገዥ ሆነው የጨለማው መንፈስ ቢያነግሳቸውና አብረውትም ቢነግሱ ልኡልና ፍቃዱን የደመሰሱ መሰላቸው :: ልብ በሉ ወገኖቼ ከአባቶቻችን ጀምሮ ከሕገ ልቡና እስከ ወንገሉ ድረስ በታላቅ ተጋድሎ የፀናችውን እምነታችንን ለማጥፋት ያልሄዱበት ጎዳና አለወይ ? እምን አይካድም ጎድተውናል :: ጥቂቶች የተዋህዶ ልጆች በልኡል ጥበቃ ለዘር ይትረፉ እንጂ የሚበዛውን አጥፍተዋል ::

ዛሬ እዚህ መድረሳችንን አይደለም ማየት ብዙ የልኡል ልጆችን ገብረናል :: ማን እራራላቸው? ማንስ አዘነላቸው? በእውነትና በመንፈስ ማምለክ ዋጋ ቢያስከፍልም መንገዱ እሱ ብቻ ነው :: በዚህ ንግግሬ መነሻነት በእውነትና በመንፈስ ማምለከን በይበልጥ እንድትረዱት መንደርደሪያ ሃሳብ ይሆናችኋል ብዬ አስባለሁ ::

ራስን ማስመለከና የውድቀት መንገዱ ፤

ባሳለፍነው የጥፋት ዘመን ያሳለፍነው የአምልኮ ሁኔታችን እጅግ የጠፋ ነበር :: በብዙ ንግግሬ እንደተረዳችሁት ቀደምት አባቶቻችን አምልኮታቸው በእውነትና በመንፈስ ነበር :: ራሳቸውን ዝቅ አድርገው አምላካቸውን ያከብሩና ያስመልኩ ነበር ::

ዛሬስ ? ዛሬ ብዙ ጳጳሳት ካህናት ዲያቆናት አገልጋዮች ራሳቸውን የሚያስመልኩ ፡ የከበሬታ ወንበር የሚፈልጉ ራሳቸውን ብቻ የሚያስግሩ የወፈሩ በጎችን አርደው የሚበሉ የከሱትን የሚጠሉ የሚገፉ የሚያሳድዱ ሆነው ተገኝተዋል ፡፡ ያውም ክርስቲያን ነን ብለው ካባውን ያጠለቁ ናቸው ፡፡ ፈጣሪ አምላካቸውን ከልባቸው ከደው ሆዳቸውን አንግሰው ዲያብሎስን በልባቸው ተክለው የስጋ ትርፋቸውን አምላክ አድርገው ይመላለሳሉ ፡፡ በአፋቸው ግን የከበረ ስሙን ለከፉ ሥራቸው ሁሉ መሸፈኛ ያደርጉታል ፡፡

ወገኖቼ እንደተዋህዶ ክርስቲያን የሥጋ ስብእናችንን ብቻ ገንብተን ፤ ቤተ እምነታችን ያላስጨበጠችንን ከቡር የእግዚአብሔር ቃል ያልተናገረንን በሕይወታችን አንግሰን እንዴት ክርስቲያን እንሆናለን ፡፡ ራሳችንን ለተለያዩ ከፋቶችና ሃጢያቶች ካስገዛን እንዴት የልኡል ልጆች እንሆናለን ?

ራስን መውደድ ፤ ለሥጋ ትርፍ ብቻ መድከም ፤ መናቅ ትእቢት ማን አለብኝነት ጭካኔ ውሸታምነት ዘራፊነት እግዚአብሔርን አለመፍራት አንግሰን የምንመላለስ ከሆነ ራሳችንና የለበስነውን ሥጋ አመለከን እንጂ ለልኡል አይደለም ራሳችንን ያስገዛነው ፡፡

ስለእምነት ስናነሳ እጅግ ወሳኝ የሆነውን ርእስ ማየታችን ስለሚሆን በመጠኑ ዳሰሼ አልፌዋለሁ ፡፡ ምክንያቱም በዚህ ጠባብ ሥፍራ ለትምህርት የታሰበ አይደለም መልእክት ለማድረስ ብቻ እንጂ !!

ስለእምነት በልኡል ቃል በእብራውያን በምእራፍ ፲፩ የተገለፀውን በሙሉ አንብቡት ፡፡

## የተዋህዶ አርበኞች የእግዚአብሔር ሕዝቦች !!

እነሆ እግዚአብሔር የሚገሥፀው ሰው ምስጉን ነው ፤ ስለዚህ ሁሉን የሚችለውን የአምላከህን ተግሳጽ አትናቅ ፤ እርሱ ይሰብራል ይጠግንማል ፤ ያቆስላል እጆቹም ይፈውሳሉ ፤ በስድስት ከፉ ነገር ውስጥ ያድንሃል ፤ ከምላስ ጅራፍ በሰባትም ውስጥ ክፋት አትነካህም ፡፡ በራብ ጊዜ ከሞት ፤ በሰልፍም ከሰይፍ እጅ ያድንሃል ፤ ከምላስ ጅራፍ ትፈወሳለህ ፤ ጥፋትም ሲመጣ አትፈራም ፤ በጥፋትና በራብ ላይ ትስቃለህ ፤ ከምድረበዳ ከአራዊትም አትፈራም ፤ ቃል ኪዳንህ ከምድረ በዳ ድንጋይ ጋር ይሆናል ፤ የምድረ በዳም አራዊት ከአንተ ጋር ይስማማሉና ፤ ድንኳንህም በሰላም እንዲሆን ታውቃለህ ፤ በረትህን ትጎበኛለህ አንዳችም አይጎድልብህም ፤ ዘርህም ታላቅ እንዲሆን ፤ ትውልድህም እንደ ምድር ሳር እንዲሆን ታውቃለህ ፤ በወራቱ የእህል ነዶ ወደ አውድማ እንዲገባ ፤ በረጅም እድሜ ወደ መቃብር ትገባለህ ፡፡እነሆ ይህችን መርምረን የሰማነውም ይህ ነው ፡፡ ይላል የልኡል ቃል፡፡

መጽሐፈ ኢዮብ ምእራፍ 5 ፡ 17 – 27

ወገኖቼ የእግዚአብሔር መርጦች አይዞአችሁ ! እንባችሁ ይታበሳል ፤ ቁስላችሁ ይፈወሳል ፤ ያለአባት ያለእናት አይደላችሁም ፡፡ የሰፈራችሁትን መከራ ፤ ያለፋችሁበትን የጨለማ ዓለም ፤ ዲያብሎስ ያደረሰባችሁን እስር እንግልት ማሳደድ ርሃብ ስቃይ ውርደት ሁሉም በልኡል ፊት በድንግል ፊት በቁጭት ታስበዋል ፡፡ ብድራቱን ይከፍላሉ ፤ የሆነው ሁሉ ለእናንተ ለበጎ ነው ፡፡ አባታችሁም እናታችሁም ሁለቱም አሁን ደርሰዋል ፡፡ ከአጠገባችሁም ናቸው ፡፡ እንደ ጥኝ የምተውበርቁበት ዘመን እነሆ ከፊታችሁ ነው ፡፡ ሁለመናችሁ ይፈወሳል ፡፡ ስለእናንተ ቅዱሳን መላእከት ሁሉ ይተጋሉ ፡፡

የጠላቶቻችሁን ጥፋት በመልካሙ ሥፍራ ሆናችሁ ትመለከታላችሁ ፡፡ ብድራታቸውን በስፈሩት እስር እጥፍ ሲስፈርላቸው ታያላችሁ ፡፡ ምድራቱንም ትወርሳላችሁ ፡፡ ከምርኮውም ፍጹም ትጠግባላችሁ ፡፡ ቀኑም ሌቱም ፤ ምድራቱም ማህፀኗም ስለእናንተ ያላቸውን ሁሉ ይሰጣሉ ፡፡ የተወደዳችሁ በእሳት የተፈተናችሁ እንቁ የልኡል

ልጆች ናችሁ ፡፡ የተዋህዶ ኦርቶዶክስ አርበኞች እንዲሁም ባላችሁበት ባሕታችሁ በቅንነታችሁ ፤ በየዋህነታችሁ ፤ እግዚአብሔርን በመፈለጋችሁ የተጎዳችሁ ሁሉ ዛሬ ታሰባችኋል ፡፡ አትፍሩ አትደንግጡ ፡፡

ወገኖቼ ይህንን ለእናንተ እናገር ዘንድ በዋናነት የታዘዝኩበት ነው ፡፡ ከእንግዲህ አትፍሩ አትደንግጡ ፤ ያለፈው መከራ ትውልታው አያስበርግጋችሁ ፡፡ ሁላችንም ከየወደቅንበት ፤ ከታሰርንበት እንፈታለን እንነሳለን ፡፡ ልኡል ! ድንግል ! ቅዱሳን ሊቃነ መላእክት የጠላትን ምሽግ የትምክህታቸውን ከምር የጥፋት እጃቸውን አርዝመት ለቆራርጠት ለያጠፉት ለያመስሱት በጠላቶቻችን እናት ላይ ቆመዋል ፡፡ ለአንዴም ለሁሌም ወደገሃነማቸው ይወርዳሉ ፡፡ ምን ልበላችሁ ወገኖቼ ! ወንድም እህቶቼ ! አባት እናቶቼ ! እንዲሁም ልጆቼ ! ድንቅ ናችሁ ፡፡ ለእናንተ ልኡል ያዘጋጀላችሁን ድንግል ያሰናዳችውን ብትመለከቱት ይህ ሁሉ ለእኔ ፤ ማን ስለሆንኩ ፤ ምንስ ያህል ፈጣሪም ድንግልም ቢወዱኝ ነው ብላችሁ ከመደመማችሁ የተነሳ የደስታ እምባችሁ የማትገቱት እንዲሆን ልገልፅላችሁ እወዳለሁ ፡፡

የዛሬው የጠፉ ትውልዶች በተለይም ወጣቶች ፤ ተምረዋል የሚባሉ ምሁሮች ፤ አገር እንመራለን ብለው በሥልጣኑ ዙሪያ የተኮለኮሉ ሰዎች ፤ ጠመንጃ የጨበጡ የተለያዩ ሃይሎች ሁሉንም ስናያቸው በምን ጎዳና ላይ ናቸው ፤ ምንስ ጥፋት ውስጥ ወድቀዋል ሰንል ብናነሳው እጅግ ብዙ ነው ፡፡

ዛሬ ምንዝርና ፤ ሌብነት ፤ ዘረኝነት ፤ ውሸት ፤ አምልኮ ባዕድ ፤ ሱሰኝነት ፤ ጫት ቃሚነት፤ ሰካራምነት ፤ ጨካኝነት ፤ ክህደት ፤ ትእቢተኝነት ፤ ነፍሰ ገዳይነት ፤ ሰነፍነት ፤ ተብታቢነት ፤ አታላይነት ፤ የአብዛኛው ትውልድ መገለጫ ሆኖአል ፡፡

እውነት እምነት ጠፍቶ በምትኩ የውሸት እምነት ነግሶአል ፡፡ በአገራችን የነገሱት ዘረኝነት በራሱም በመንግሥት ተብዬው በመሆኑ አንዱ አንዱን እንዲጠላና በጠላትነት እንዲተያይ ተደርጎአል ፡፡ እስልምና ምንፍቅናና ኩትልክና ዋቄ ፈታ ጣኦት አምላኪ ፤ ተብታቢ መተተኛ ጠንቋይ አስጠንቋይ ፤ ውቃቢ የመሳሰሉ ትውልዱን ይዘውት የጠፉ ሆነዋል ፡፡

ዛሬ በምናየው መንግስታዊ አርቴፊሻል ለውጥ የሚመጣ አንዳች ነገር የለም ፡፡ እግዚአብሔር ያለው ቀድሞም የተናገረው ፍርዱንም ያሳወቀው ኢትዮጵያ ወደትንሳኤው እንድትሻገር ነው ፡፡ አብሯት የሚሻገሩትም ዛሬ በእምነቱ ስም የሚነግዱትን ቀጣፊዎችን ተኩላዎችን አይደለም ፡፡ ራሱ ኮትኩቶ ደክሞ በእሳት አንጥሮ ተሸክሞ በማእበሉ ሁሉ ያሳለፋቸውን አገልጋይ ባሮቹን እንጂ !

ወገኖቼ !! ልትረዱት ይገባል ፤ ልታደምጡም ፤ ልትዘጋጁም ይገባችኋል ፡፡ የምድሪቱ ወራሾች የክብሩ ቀዳሽ አወዳሾች እናንተ የልኡል ማሕተም ያረፈባችሁ ናችሁ ፡፡

ቤተ ክርስቲያናችን የተዋህዶ ቤታችን እግዚአብሔር በወደዳቸው በአከበራቸው ባፀደቃቸው ልጆቹ እንደገና የውርደትና የጥፋት ካባዋን አውልቃ እንደ አዲስ ትነሳለች እንጂ !! ሌባ ተኩላ የበግ ለምድ ለብሶ ሁሌም የሚፈነጭባት አትሆንም ፡፡ አመጽን ፤ ማፍረስን በቤተ እግዚአብሔር /በተዋህዶ/ ላይ ሲፈጽም ሲያስፈጽም የነበረ የአገርም የውጪም ጠላት ሁሉ ለአንዴም ለሁሌም እንዳይነሳ ሆኖ በእሳት ባሕር ይከደናል ፡፡

የተዋህዶ አርበኞች ከዚህ በታች ያሰፈርኩት ሁሌም የምትሰሙት ምሳሌ ነውና እንደልኡል ታማኝ አገልጋይ ሊቀ መላእክት ገብርኤል ፀንተን እንቁም !!

በአንድ ወቅት ልኡል ቅዱሳን መላእክትን ፅናት ይመለከት ዘንድ በዙሪያው ካሉ ሊቃነ መላእክቶች ራሱን ሰወረ ፡፡ በወቅቱ ከከበሩት መላእክትም በክብሩም በሥልጣኑም ከልኡል ቀጥሎ ይታይ የነበረው ሳጥናኤል ነበር ፡፡ ልኡል ራሱን ሲሰውር ሁሉም ተደናገጡ ፈጣሪያችን ማነው ወዴትስ ሄደ ብለው ታወኩ ፡፡ ሳጥናኤል ቀድሞም በልቡ ሥልጣንን እነጥቃለሁ ብሎ ሃሳብ በልቡናው ያሳደረ በመሆኑ ፤ ከመላእክቱም በከፍታ ያለ

